# መጽሐፍ ፡

## የዓለም ፡ ምሬት ፡ ማጣፊጫ ፡

# ማር ፡ ነው ።




ራስ ፡ ቢ. መኰንን ፡ እንዳልካቸው ።



አዲስ ፡ አበባ ፡ ፲፱፻፵፪ ዓ. ም.

በትንሣኤ ፡ ዘጉባኤ ፡ ማተሚያ ፡ ቤት ፡ ታተመ ።

መጽሐፍ ፡ የዓለምን ፡ ምሬት ፡

ማጣፈጫ ፡ ማር ፡ ነው ።




ደስታን ፡ ዕረፍትን ፡ ዓለምን ፡ ትወዳለኽን ። እኔ ፡ ሁሉንም ፡ ነገር ፡ ቀመስ ኩት ። ግን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ከማገልገልና ፡ መጽሐፍን ፡ ከማንበብ ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ ደስታና ፡ ዕረፍት ፡ ዓለም ፡ የለም ።

ራስ ፡ ቢ. መኰንን ፡ እንዳልካቸው ።




ሦስተኛ ፡ በ፲፱፻፵፱ ፡ ዓ ፡ ም ፡ በትንሣኤ ፡ ዘጉባኤ ፡ ማተሚያ ፡ ቤት ፡ ታተመ ።

ተንትመ ፡ ዝንቱ ፡ መጽሐፍ ፡ አመ ፡ ፳ወ፱ ፡ ዓመተ ፡ መንግሥቱ ፡
ለቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዘኢትዮጵያ ።

ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡
ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዘኢትዮጵያ ።

# መግለጫ ።

የሰው ፡ ልጆች ፡ ከሚንቀሳቀሱ ፡ ፍጡራን ፡ ሁሉ ፡ በላይና ፡ ገዥ፡ ሆነው ፡ የሚታዩት ፡ ቀዋሚ ፡ የሚሆኑ ፡ ዕውቀቶችና ፡ አሳቦች ፡ ስላሏቸው ፡ ነው ።

እነዚህም ፡ ቀዋሚ ፡ የሚሆኑት ፡ ዕውቀቶችና ፡ አሳቦች፡ አካል፡ አውጥተው ፡ እንዲታዩ ፡ ለማድረግ ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ምንም ፡ የተፈጥሮ ፡ ዕውቀትና ፡ ችሎታ ፡ ቢኖራቸው ፡ ከፍጻሜ ፡ ለማድረስ ፡ ትምህርትና ፡ ጊዜ ፣ የዕሙና ፡ ቦታ ፡ ያስፈልጋቸዋል ።

ከዚህም ፡ በቀር ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ኀዘንና ፡ መከራ ፡ ብቸኝነት ፡ የሰውን ፡ ልጆች ፡ መንፈስ ፡ ከፍ ፡ ስለሚያደርጉና ፡ ስለሚያጣሩ ፡ ቀዋሚ ፡ የሆኑ ፡ ዕውቀቶችና ፡ ሐሳቦች ፡ ከመከራና ፡ ከኀዘን ፡ ውስጥ ፡ እየተጣሩ ፡ ይወጣሉ ። ለምሳሌ ፡ ብዙዎች ፡ ለዓለም ፡ ጠቃሚ ፡ የሆኑ ፡ መጽሐፎች ፡ ተጽፈው ፡ የተገኙት ፡ ከስደተኞችና ከእስረኞች ፡ ከችግረኞች ፡ ነው ።

እኔም ፡ እነዚህን ፡ ትንንሽ ፡ መጽሐፎች ፡ ለመጻፍ ፡ የረዳኝ፡ ባ፲፱፻፳፫ ፡ ዓ. ም. ጥቂት ፡ ቀን ፡ አቃቂ ፡ እርስቴ ፡ ላይ ፡ በብቸኝነት ፡ ስለ ፡ ተቀመጥሁ ፡ ነው ።

ይህችም ፡ ቦታ ፡ በሁለት ፡ ተራሮች ፡ መካከል ፡ በለገዳዲ ፡ ወንዝ ፡ ዳር ፡ ከተራሮቹ ፡ እግር ፡ የምትገኝ ፡ ለምለም ፡ የሆነች ፡ ሽለቆ ፡ ናት ።

ከወንዙም ፡ ዳር ፡ አንዲት ፡ የመኖሪያ ፡ ቤት ፡ አለችኝ ፤ ይህቺም ፡ ቤት ፡ ልከኛ ፡ የሆነች ፡ ይበቃኛል ፡ የሚል ፡ ሰው ፡ መኖሪያ፡ ያኽል ፡ ትሆናለች ። በክፍሏም ፡ ከላይ ፡ አንዲት ፡ የሰው ፡ መቀበያ ፡ አነስተኛ ፡ እልፍኝና ፡ ከወንዙ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ የሆነ ፡ አንድ፡ ሰፊ ፡ ሰበሰብ ፡ ይገኛል ። ደግሞ ፡ ከሰበሰቡ ፡ የተያያዘች ፡ አንዲት፡ መኝታ ፡ ቤት ፡ አለችኝ ። ከታች ፡ ምድር ፡ ቤቱ ፡ የፈረስ ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሁለት ፡ በቅሎዎችና ፡ አንድ ፡ ፈረስ ፡ ታስረውበታል ። ጥቂት ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ ሁለት ፡ ክፍል ፡ ወጥ ፡ ቤትና ፡ ማድ ፡ ቤት ፡ ያላት ፡ አንዲት ፡ ቤት ፡ ትገኛለች ።

በዚችም ፡ መኖሪያ ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ብሎ ፡ አንድ ፡ በት ልቅ ፡ በይ ፡ ለወፍጮና ፡ ላታክልት ፡ የሚሆን ፡ በቂ ፡ የሆነ ፡ ውሃ፡ ይፈሳል ። ከወንዙ ፡ ማዶ ፡ ከቤቴ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ያለው ፡ ተራራ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ መጥቶ ፡ አያስቸግረኝም፡ ነበር ።

ከወንዙም ፡ ወዲህ ፡ ከቤቴ ፡ አንሥቶ ፡ እስከ ፡ ተራራው ፡ ጫፍ፡ ድረስ ፡ መንገዱ ፡ ጕርብጥብጥ ፡ የሆነና ፡ በአጋም ፡ በቀጋ ፡ በግራር ፡ በሌሎችም ፡ ዛፎች ፡ የተከበበ ፡ ጥቅጥቅ ፡ ያለ ፡ ዱርና ፡ ጕራንጕር ፡



ያቃቂ ፡ ቤት ።

ስለ ፡ ሆነ ፡ ከከተማ ፡ ለሚመጡ ፡ ሰዎች ፡ በእግራቸው ፡ ለመውረ ድና ፡ ለመውጣት ፡ አስቸጋሪ ፡ ነው ።

ስለዚህ፡ የእንግዳ፡ መቀበያ፡ ቤቴን፡ ከፋፍ፡ ላይ ፡ ሠርቼ ፤ ቤተ ፡ ሰቦቼ፡ ከዚያው ፡ ስለሚገኙ ፡ የሚጠይቁኝ ፡ እንግዶች ፡ የሚበዙት ፡ እነሱ ፡ ዘንድ፡ ደርሰው ፡ ይመለሳሉ ። በዚህ ፡ ምክንያት ፡ በዕሙና ፡ ከሕሊናዩ፡

ጋራ ፡ ለመጫወትና ፡ አንዳንድ ፡ ማስታወሻ ፡ ለመውሰድ ፡ የሚበቃ ፡ ጊዜ ፡ አገኘሁ ።

ትንሽ ፡ ውካታ ፡ የምሰማው ፡ አንዲት ፡ በቀን ፡ ካምስት ፡ ዳውላ ፡ ይበልጥ ፡ የማትፈጭ ፡ በውሃ ኀይል ፡ የምትዞር ፡ ወፍጮ ፡ ስለ ፡ ነበረችኝ ፡ ለማስፈጨት ፡ የሚመጡ ፡ ባላገሮች ፡ ጭቅጭቅ ፡ ብቻ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ከቤቴ ፡ አንድ ፡ አምስት ፡ መቶ ፡ ሜትር ፡ ያህል ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ በዱሮው ፡ የሐረርጌ ፡ መንገድ ፡ በኩል ፡ ካንድ ፡ ትልቅ ፡ የብረት ፡ ድልድይ ፡ አጠገብ ፡ በደን ፡ የተከበበች ፡ ሜዳ ፡ በወንዙ ፡ ዳር ፡ የኔው ፡ ርስት ፡ የሆነች ፡ የዕረፍት ፡ ቦታ ፡ ስላለችኝ ፡ ያሣ ፡ ማጥመጃ ፡ ይዤ ፡ እወንዙ ፡ ዳር ፡ ከለምለም ፡ ሣር ፡ ላይ ፡ ጋደም ፡ ብዬ ፡ መጽሐፎቼን ፡ እመለከት ፡ ነበር ።

አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ መጽሐፎቼን ፡ ትቼ ፡ የሚገርም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የጥበብ ፡ ሥራ ፡ ከወፎችና ፡ ከትሎች ፡ ንብረት ፡ ውስጥ ፡ ገብቼ ፡ ስመለከት ፡ በብዙ ፡ የሚያስደንቁ ፡ ነገሮች ፡ ይገጥሙኛል ።

ምክንያቱም ፡ በመቶ ፡ የሚቈጠሩ ፡ ብዙዎች ፡ ወፎችና ፡ ትሎች ፡ በየዛፉና ፡ በየቍጥቋጦው ፡ ላይ ፡ ቤታቸውን ፡ ሲሠሩ ፡ ሲወጡ ፡ ሲገቡ ፡ ሲታዩ ፡ ስለሚያስገርም ፡ ነው ። ቀጋውና ፡ አጋሙ ፤ ጠንበለሉ ፡ ሌሎችም ፡ ብዙዎች ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ አበቦች ፡ ስላበቡ ፡ የደኑ ፡ ውስጥ ፡ መዐዛ ፡ እንደ ፡ ጥሩ ፡ የሽቶ ፡ መሸጫ ፡ ቤት ፡ ያህል ፡ ይሸታል ።

ስለዚህ ፡ በብዙ ፡ ሺሕ ፡ የሚቈጠሩ ፡ የንብ ፡ ሠራተኞች ፡ በተራ ፤ በተራ ፡ አበባውን ፡ እየቀሰሙ ፡ ሲሄዱና ፡ ሲመጡ ፡ አያቋርጡም ፡ ነበር ።

ከዚህም ፡ በቀር ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የሆኑ ፡ ትሎች ፡ እንደዚሁ ፡ ምግባቸውንና ፡ መኖሪያቸውን ፡ ለማዘጋጀት ፡ ይጥራሉ ። አንዳንዶቹም ፡ መኖሪያቸው ፡ ከዛፍ ፡ ላይ ፡ ስለሆነ ፡ ሳይሰለቹ ፡ ሲወድቁና ፡ ሲነሡ ፡ ጥረው ፡ ግረው ፡ ከመኖሪያ ፡ ቤታቸው ፡ ይደርሳሉ ።

ሌሎቹም ፡ በመሬትና ፡ በሣር ፡ ላይ ፡ ቤታቸውን ፡ ስለ ፡ ሠሩ ፡ ምንም ፡ ለሕይወታቸው ፡ አሥጊ ፡ ኑሮ ፡ ቢሆን ፡ እስከ ፡ ዘመናቸው ፡ መጨረሻ ፡ ድረስ ፡ ደስ ፡ ብሏቸው ፡ ይመላለሳሉ ።

በጣም ፡ የሚገርመው ፤ ወፎች ፡ ትሎችን ለማጥመድ ፡ ይጠባበቃሉ ። እንደዚሁም ፡ ገዲ ፤ ጭልፊትና ፡ ሲላ ፡ እነዚህን ፡ የመሰሉ ፡ አሞሮች ፡ ወፎቹን ፡ ለመያዝ ፡ ያደፍጣሉ ።



ትል ፡ የምትበላ ፡ ወፍ ።

የፍየል ፡ ዐይን ፡ ወደ ፡ ቅጠል ፤ የነብር ፡ ዐይን ፡ ወደ ፡ ፍየል፤ ያዳኝ፡ ዐይን ፡ ወደ ፡ ነብር ፡ እንደተባለው ፡ በዚያ ፡ ደን ፡ ውስጥ ፡ የማያቸው ፡

ወሮችና ፡ ትሎች ፡ አሞሮቹም ፡ አንዱ ፡ ላንዱ ፡ ምግብ ፡ በመሆ ናቸው ፡ ሁሉም ፡ በየኗላቸው ፡ ተከታታይ ፡ ጠላት ፡ አላቸው ።



ወፍ ፡ የምትበላ ፡ አሞራ ፡ ( ገዲ ። )

ይልቁንም ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ከፍ ፡ ያለ ፡ አሳብ ፡ አስታወሰኝ ፤ የሰው፡ ዐይን ፡ ከገንዘብ ፡ ላይ ፡ የሞት ፡ ዐይን ፡ ከሰው ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ሆነ፡ ተረዳ ሁት።ነገር ፡ ግን፡ ሰውም ፡ እንስሳም ፡ ቢሆን ፡ አንዱ ፡ ከመካከላቸው ፡

ብሞት ፡ ሲነጠቅ ፡ እነሱ ፡ ቀሪዎቹ ፡ የማይሞቱ ፡ ስለሚመስላቸው ፡
ዕድላቸው ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ባለማወቅ ፡ ተጽናንተው ፡ ይኖራሉ ።
አንባቢ ፡ ሆይ ፡ ቢሆንም ፡ እነዚህ ፡ ፍጡሮች ፡ በዚያች ፡ በትዳራ
ቸው ፡ውስጥ ፡ ያለ ፡ ደስታና ፡ በባሕርያቸው ፡ ያጌጡት ፡ ሽልማት ፡ እጅግ ፡
የሚገርምና ፡ የሚያምር ነው ። እኛ ፡ ከምናውቃቸው ፡ ወፎች ፡ እንደ ፡
ወማይ ፡ ድንቢጥ ፡ ጨረባ ፡ መነኰሴ ፡ ወፍ ፤ የመስቀል ፡ ወፍ ፡ ጕራ
ማይሌ ፡ አራኅራኂት ፡ የት ፡ ውዬ ፡ የት ፡ አድር ፡ ብዬ ፡ ጭሪ ፡ ከሚ
ባሉት ፡ በቀር ፡ ሌሎች ፡ በሰማያዊ ፡ በጥቍርና ፡ በቀይ ፡ ቀለም ፤ ብጫና ፡
አረንጓዴ ፡ በሆነ ፡ ቀለም ፡ ያጌጡ ፡ ወፎች ፡ በየዛፉ ፡ ላይ ፡ ይታያሉ ።
አንዳንዶቹም ፡ በራሳቸው ፡ ላይ ፡ በሚገርምና ፡ ወርቅ ፡ በሚመስል ፡
ከባሕርያቸው ፡ በተገኘ ፡ አክሊል ፡ ተቀጽለዋል ።

ሌሎቹም ፡ ከላይ ፡ ጥቍር ፡ ሆነው ፡ እግራቸው ፡ ቀይ ፡ ሆኖ ፡
ግምጃ ፡ ሱሪ ፡ የታጠቁ ፡ ይመስላሉ ። እንደዚሁም ፡ ከነሱ ፡ ጋራ ፡
በደኑ ፡ ውስጥ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ቀለም ፡ ያላቸው ፡ አበቦች ፡ ፈንድተው ፡
ሲታዩ ፡ የሁለቱም ፡ ፍጥረቶች ፡ የባሕርያቸው ፡ ጌጥ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡
በሀብት ፡ ከፍ ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ እንኳ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ልብስ ፡ አለበሱም ።

ስለዚህ ፡ መድኃኒታችን ፡ አበቦችን ፡ ተመልከቱ ፡ እንዴት ፡ ያድጋሉ ፡
አይደክሙም ፡ አይፈትሉም ፤ እላችሁማለሁ ፡ ሰሎሞን ፡ እንኳ ፡
በክብሩ ፡ ሁሉ ፡ ከእነዚህ ፡ እንዳንዲቱ ፡ አለበሰም ፡ ብሎ ፡ የተናገረ
ውን ፡ ያሳስባል ።

እነዚሀ ፡ ወፎችም ፡ እንደ ፡ መልካቸው ፡ ልዩነት ፡ ድምፃቸውም ፡
ልዩ ፡ ሆኖ ፡ ርስ ፡ በርሳቸው ፡ ሲጠራሩና ፡ ከንዱ ፡ ዛፍ ፡ ወዳንዱ ፡ ዛፍ ፡
ሲበሩ ፡ በማየት ፡ የነፍስ ፡ ደስታ ፡ ይሰማል ። ይልቁንም ፡ ጕሬዝማ ፡
የሆኑ ፡ ትንንሽ ፡ ወፎች ፡ እንደ ፡ መልካም ፡ እንቢልታ ፡ ነፊ ፡ በዜማ ፡
ሲያፏጩ ፡ ፉጨታቸው ፡ በተሰማ ፡ ጊዜ ፡ ከነሱ ፡ ውስጥ ፡ እንደዚሀ ፡
ያለ ፡ ቃል ፡ መውጣቱ ፡ ያስደንቃል ። እነዚህም ፡ በባላገር ፡ ወፌ ፡
ያሬድ ፡ ይባላሉ ፤ የተባዕቱና ፡ የእንስቲቱ ፡ ድምፅ ፡ እንደ ፡ በገና ፡ ስልት ፡
ልዩነት ፡ አለው ። በጣም ፡ የሚገርመው ፡ አራኅራኂት ፡ የምትባለው ፡
አደጋ ፡ ተጠባባቂ ፡ ወፍ ፡ ሸሌ ፡ መጠማጥ ፡ እባብ ፡ ሌሎችም ፡ ተና
ጣቂ ፡ አሞሮችና ፡ አውሬዎች ፡ ሲመጡ ፡ ልዩ ፡ የሆነ ፡ ያደጋ ፡ ድምፅ ፡
አጯጯኽ ፡ ስትጮኽ ፡ ወፎች ፡ ሁሉ ፡ ይጠነቀቃሉ ። በውነት ፡ በወ
ፎች ፡ ውስጥ ፡ ያለውን ፡ ማኅበራዊ ፡ ኑሮ ፡ ማየት ፡ በጣም ፡

ይገርማል ፤ ይልቁንም ፡ የገላግልቶቻቸው ፡ ዕውቀት ፡ በጣም ፡ ያስደ ንቃል ። ምክንያቱም ፡ የወፍ ፡ ጫጩቶች ፡ በጐገሮዋቸው ፡ ውስጥ ፡ ሆነው ፡ ክንፋቸው፡እስኪጠነክር ፡ ድረስና ፡ በረው ፡ ካደጋ ፡ ለማምለጥ፡ እስኪችሉ ፡ ከጐገሮዋቸው፡ውስጥ ፡ አይወጡም ። እናት ፡ አባቶቻቸውም፡ ምግብ፡ ሲያመጡላቸው ፡ አፋቸውን ፡ ከፍተው ፡ ተቀብለው ፡ ከዚያው ፡ ከጐገሮዋቸው፡ ይከተታሉ ፡ እንጂ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ልጆች፡ከእሳት ፡ እንዳ ይወድቁ ፤ ከገደል ፡ እንዳይገቡ ፡ ሞግዚት ፡ አያስፈልጋቸውም ። የሰው፡ ልጆች ፡ ግን ፡ ዐቅማቸውን ፡ ባለማወቃቸው ፡ ደጋፊና ፡ ጠባቂ ፡ ሞግ ዚት ፡ ያስፈልጋቸዋል ። የሰው ፡ ልጆች ፡ በሕፃንነት ፡ ይቅርና ፡ ዐቅመ፡ አዳም፡ ቢያደርሱ ፡ እንኳ ፡ ያለመደጋገፍ ፡ ብቻቸውን ፡ አይቆሙም ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ መንጠቆዬን ፡ ይዤ ፡ ዓሣ ፡ ለመያዝ ፡ ወደ ፡ ባሕሩ፡ ዳር ፡ እሄዳለሁ ። ያቃቂ ፡ ዓሣ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ዓሣ ፡ ወጋሮች ፡ ስላስመረ ሩት ፡ ለመጠመድ ፡ በጣም ፡ ያስቸግራልና ፡ እመንጠቆው ፡ ጫፍ ፡ ሥጋ፡ ሰክቼ፡ ከባሕሩ ፡ ውስጥ ፡ ጥዬ ፡ እጠባበቃለሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ የሚበል ጠው ፡ ደስታዬ ፡ ዓሦችና ፡ ሌሎችም ፡ ጥቃቅኖች፡ ተሐዋስያን ፡ (ተንቀ ሳቃሾች ) ሁሉ ፡ ሳያቋርጡ ፡ በውሃው ፡ ውስጥ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ ሲሯ ሯጡ ፡ ማየት ፡ ነበር ።

ከዚያ ፡ ውስጥ ፡ ያሉ ፡ ተሐዋስያን ፡ ሁሉ ፡ አንዱ ፡ ላንዱ ፡ ምግብ፡ በመሆናቸው ፡ ፋንታቸው ፡ እስኪደርስ ፡ ደስ ፡ ብሏቸው ፡ ይቦርቃሉ ፡ ትልቁ ፡ ዓሣ ፡ ትንሹን ፡ ይውጠዋል ፤ ደግሞ ፡ ትንሹ ፡ ዓሣ ፡ ከውሃው ውስጥ ፡ የሚገኙትን ፡ ትንንሽ ፡ ተሐዋስያን ፡ ይውጣል ። እኔም ፡ ደግሞ፡ ሥጋን ፡ በመንጠቆዬ ፡ ጫፍ ፡ ሰክቼ ፡ ትልቁን ፡ ዓሣ ፡ ለማጥመድ ፡ እጠ ባበቃለሁ ። እኔንም ፡ ሞት፡በመንጠቆው ፡ ጫፍ ፡ ገንዘብን ፡ ሰክቶ ፡ ይጠ ባበቀኛል ። ‹ አ ፡ ለሰብእ ፡ ዘኢየአምር ፡ ዕለተ ፡ ሞቱ ፤ ወዕራቃ ፡ ትበ ጽሕ ፡ ነፍሱ ፡ ቅድመ ፡ እግዚአብሔር › ፡ እንዳለ ። በውነት ፡ ሰውም ፡ ቢሆን ፡ እስኪሞት ፡ ድረስ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሲቦርቅ ፡ ሲታይ ፡ ከወፎ ችና ፡ ከዓሣ ፡ ከሌሎችም ፡ ተሐዋስያን ፡ ሁሉ ፡ የሚበልጥበት ፡ ነገር ፡ የለውም ። በጣም ፡ የሚገርመው ፡ አንዲት ፡ ዓሣ ፡ የምትበላ ፡ ወፍ፡ አፏ፡ በጣም ፡ ረዥም ፤ የሆነ ፡ በባሕሩ ፡ መካከል ፡ ሦስት ፡ ሜትር ፡ ያኽል ፡ ራቅ ፡ ብላ ፡ በአየር ፡ ላይ ፡ ክንፏን ፡ ዘርግታ ፡ ጥቂት ፡ ከተመለከተች ፡ በኋላ ፡ ከባሕሩ፡ውስጥ ፡ ተወርውራ ፡ ጠልቃ ፡ ዓሣውን ፡ ይዛ ፡ ትወጣለች።

እኔ ፡ በመንጠቆዬ ፡ አንድ ፡ ዓሣ ፡ እስክይዝ ፡ ድረስ ፡ እሷ ፡ ሦስት ፡ አራት ፡ ዓሣ ፡ ለመያዝ ፡ ትችላለች ።



ዓሣ ፡ የምትበላ ፡ አሞራ ፡ (የወንዝ ． አሙቴ) ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ ከሰው ፡ የተለየ ፡ ከውሃ ፡ የጠራ ፡ ነው ፡ እንደ ፡ ተበ ለው ፡ በሕዝብ ፡ ውካታ ፡ ውስጥ ፡ ተቀላቅሎ ፡ አእምሮን ፡ ከማሳደፍ ፡ በመልካም ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ ከወፎችና ፡ ከዓሦች ፡ ከአውሬዎች ፡ ንብረት ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ግሩም ፡ ሥራ ፡ ማየትና ፡ ማድነቅ ፡

ሕሊናን፣ ከፍ ፣ የሚያደርግና ፣ መንፈስን ፣ የሚያንቀሳቅስ ፣ የጽሕፈት ንም ፣ መንፈስ ፣ የሚያሳድር ፣ ነው ፣ «ASPIRATION»

በዚያች ፣ በድኻ፣ጐጆዬ፣ውስጥ ፣ በዕሙና ፣ በተቀመጥሁ ፣ ጊዜ የሚያሳዝኑኝ ፣ ሁለት ፣ ነገሮች ፣ ብቻ ፣ ናቸው ፤ አንደኛው ፣ ሥራ ፣ ይገኛ ፣ ካዲስ ፣ አበባ ፣ ሰው ፣ መጥቷል ፣ ብለው፣በሚነግሩኝ፣ ጊዜ፤ሁለ ተኛው ፣ ከባላገሮቹ ፣ ስለ፣ ተላመድኩና ፣ ከኑሯቸው ፣ ውስጥ ፣ ስለ ፣ ገባሁ ፣ ባላገሮቹ፣ ያገልጋዮቻቸውን ፣ ልጆች ፣ ያላቅማቸው ፣ ሥራ ፣ ሲያሲዟቸው ፣ በማየት ፣ ነው። ይልቁንም ፣ ከኔ ፣ መሬት ፣ ማዶ ፣ ራቅ ፣ ብለው ፣ ከተራራው ፣ ወገብ ፣ ላይ ፣ ያሉ ፣ መንደሮች ፣ ውሃ ፣ የሚቀ ዱት ፣ ከኔ ፣ ቤት ፣ አጠገብ ፣ ለገዳዲ ፣ ከሚባለው ፣ ወንዝ ፣ ስለ ፣ ሆነ ፣ ያገልጋዮቻቸው ፣ ትንንሽ ፣ ልጆች ፣ ካቅማቸው ፣ በላይ ፣ የሆነ ፣ ትልቅ ፣ ገንቦ ፣ ጊዜ ፣ ያለጊዜ ፣ ተሸክመው ፣ ውሃ ፣ ለመቅዳት ፣ ሲመጡና ፣ በጭንቅ ፣ ውሃውን ፣ ይዘው ፣ ሕፃናቱ ፣ እያለቀሱ ፣ ዐቀበ ቱን ፣ ሲወጡ ፣ ከወንዝ ፣ ዳር ፣ ሆኜ ፣ ስመለከት ፣ በጣም ፣ አዝን ፣ ነበር ፣ በዚህ ፣ ምክንያት ፤ ያይኔ ፣ አበባ ፣ የሚባለውን ፣ ልብ ፣ ወለድ ፣ ታሪክ ፣ ባ፲፱፻፳፫ ፣ ዓ ፣ ም ፣ ጻፍኩ ፣ ከዚያ ፣ ውስጥ ፣ ነው ፣ ዓለም ፣ ወረተኛ ፣ የተባለው ፣ መጽሐፍ ፣ ባጭሩ ፣ ለቲያትር ፣ እንደሚመች ፣ የተገለበጠው ። ባቃቂ ፣ ርስቴ ፣ ላይ ፣ ፩ ፣ ዓመት ፣ ከሦስት ፣ ወር ፣ ከተቀመጥኩ ፣ በኋላ ፣ ተመልሼ ፣ ከዚያው ፣ አዲስ ፣ አበባ ፣ ገባሁ ።

ባ፲፱፻፳፬ ፣ ዓ. ም. ያዲስ ፣ አበባ ፣ ከንቲባ ፣ ሆንኩ ።

ባ፲፱፻፳፭ ፣ „ " የሲቡና ፣ የጉዳያ ፣ ጠቅላይ ፣ ገዢ ፣ ሆንኩ።

ባ፲፱፻፳፮ ፣ „ „ የይሉባቦር ፣ የቡኖ ፣ " „ „

ባ፲፱፻፳፯ ፣ „ „ ኅዳር ፣ ፰ ፣ ቀን ፣ የጦር ፣ ሠራዊቴን ፣

ይዤ ፣ ወደ ፣ ውጋዴ ፣ ዘመትኩ ።

ባ፲፱፻፳፯ ፣ ዓ. ም. ሚያዝያ ፣ ፳፮ ፣ ቀን ፣ ከውጋዴ ፣ ተመልሼ ፣ ከግርማዊነታቸው ፣ ጋራ ፣ ተሰደድኩ ። የስደት ፣ ቦታችንም ፣ ኢየሩ ሳሌም ፣ እንዲሆን ፣ ተቈረጠ ። አንድ ፣ ዓመት ፣ ከተቀመጥን ፣ በኋላ ፣ ግርማዊነታቸው ፣ በረዳን ፣ ገንዘብ ፣ ኢያሪኮ ፣ ላይ ፣ ርስት ፣ ገዛን ፣ በዚ ያችም፣ርስታችን ፣ ውስጥ፣ከበዥረ ፣ ሎሚና፣ከመንደሪን ፣ ከሙዝ፣ዛፎች፣

መካከል ፡ የተሠራች ፡ ፬ ፡ ክፍል ፡ ያላት ፡ ለኛ ፡ ትዳር ፡ የምትበቃ ፡ ልከኛ ፡ ቤት ፡ ነበረችባት ። እኔና ፡ ባለቤቴ ፡ ልዕልት ፡ የሻሸ ፡ ወርቅ ፡ ይልማ ፡



የ ኢ ያ ሪ ኮ ፡ ቤ ት ።

በዚያች ፡ በጕዢዋችን ፡ ውስጥ ፡ ደስ ፡ ብሎን ፡ ሥራችንን ፡ ተከፋፍለን ፡ እንኖር ፡ ነበር ። እኔ ፡ የውሃ ፡ ማጠጣትና ፡ አታክልቱን ፡ መኰትኰት ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የበሰለውን ፡ በኰረ ፡ ሎሚና ፡ ሙዝ ፡ ሌላውንም ፡ አታክ



ከረቢ ፡ መምሪያ ፡ ቤት ፡ ስብሰባ ፡ ላይ ።

ልት ፡ አንድ ፡ መንኰራኵር ፡ ብቻ ፡ ባላት ፡ ባንዲት ፡ ትንሽ ጋሪ ፡ እየገፋሁ ፡ በከተማው ፡ ውስጥ ፡ እያዞርሁ ፡ እሸጥ ፡ ነበር ። ከዚህም በቀር ፡ ሥዕል ፡ እየሣልኩ ፡ ለልብሳችን ፡ መግዣ ፡ ያኽል ፡ ገንዘብ ፡ እናገኝ ፡ ነበር ። ባለቤቴም ፡ በማለዳ ፡ ተነሥታ ፡ ሥራዋ ፡ ቤት ፡ መጥረግና ፡ መስተዋት ፡ መወልወል ፡ ወጥ ፡ መቀቀል ፡ እንጀራ ፡ መጋገር ፡ ሹራብ ፡ መሥራት ፡ ነበር ።



የረቢ ፡ ጎልጎታ ፡ መድኀኔ ፡ ዓለም ።

ከዚህ ፡ በቀር ፡ በትዳራችን ፡ ውስጥ ፡ ጥቂት ፡ የሚያሰቅቀኝ ፡ የኛ፡ የውሃ ፡ ተራ ፡ የሚደርስን ፡ ከሌሊቱ ፡ በስድስት ፡ ሰዓት ፡ ተኩል፡ ስለ፡ ሆነ ፡ የውሃው ፡ አካፋይ ፡ ሹም ፡ የሆነ ፡ ሠራተኛ ፡ ሌሊት ፡ በር ፡

መቶ፡ያስነሣኝና ፡ ይሄዳል ።እኔም ፡ ውሃው ፡ እንዳያመልጠኝ ፡ በከንቱ፡ እንዳይባክን ፡ የጋዝ ፡ ፋኖሴን ፡ አብርቼ ፡ የላስቲክ ፡ ቦት ፡ ጫማዬን ፡ አድርጌ ፡ ዶማና ፡ አካፋዬን ፡ ይዤ ፡ በውድቅት፡ ጨለማ ፡ አታክልቱን፡ ሁሉ ፡ ብቻዬን ፡ ውሃ ፡ ሳጠጣ ፡ ያለፈውን ፡ በላያችን ፡ ደር በነው ፡ የነበረውን ፡ የጸጋ ፡ ሀብትና ፡ ክብር ፡ ሁሉ ፡ የከንቱ ፡ ከንቱ ፡ መሆኑን ፡ ያሳስበኝ ፡ ነበር ። ቢሆንም ፡ አታክልቱን ፡ ካጠጣሁ ፡ በኋላ፡ የተረፈውን ፡ ውሃ ፡ ለመጠጥና ፡ ለመታጠቢያ ፡ እንዲሁም ፡ ለሥራ ፡ የሚበቃንን ፡ በስሚንቶ ፡ በተሠራው ፡ ጉድጓድ ፡ ውስጥ ፡ መልቼ ፡ ተመልሼ ፡ እተኛለሁ ።

ኢያሪኮ፡ በተቀመጥንበት ፡ ዘመን፡ሁሉ ፡ ያገራችን ፡ በጠላት፡መወ ረርና ፡ ወንድሞቻችን ፡ በፋሺስት ፡ እብሪት ፡ ሥቃይ፡በማየታቸው፡ከማ ዘን ፡ በቀር ፡ እኔም፡ባለቤቴም፡ጊዜ፡የምናሳልፍበት ፡ ሥራ ፡ አላጣንም።

ስለዚህ ፡ ፩ኛ ፡ ስለ ፡ ምንድነው ፡ ኢትዮጵያ ፡ ድል ፡ የሆነችው ። ፪ኛ ፡ አትፍሩ ፡ ሥጋን ፡ ከሚገድሉ ፡ ተብለው ፡ የተሰየሙ ፡ ሁለት ፡ መጽሐፎች ፡ ጽፌ ፡ ነበር ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ባ፲፱፻፴፫ ፡ ዓ. ም. ሚያ ዝያ ፡ ፳፯ ፡ ቀን ፡ ከንጉሠ ፡ ነገሥታችን ፡ ጋራ ፡ በከርቱም ፡ በኩል ፡ ወዳገራችን ፡ ተመልሰን ፡ ከመናገሻ ፡ ከተማችን ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ገባን።

ባ፲፱፻፴፬ ፡ ዓ. ም. ካዲስ ፡ አበባ ፡ ፲ ፡ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ያኽል ፡ ራቅ ፡ ባለች ፡ አጎቴ ፡ ራስ ፡ ቢትወደድ ፡ ተሰማ ፡ በሰጡኝ ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ የመድኀኔ ፡ ዓለምን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሠራን ።

ባ፲፱፻፴፭ ፡ ዓ. ም. የመኖሪያ ፡ ቤታችንን ፡ ሠራን ፤ ደግሞ ፡ ባለ ቤቴ ፡ ልዕልት ፡ የሻሽ ፡ ወርቅ ፡ ጊዜዋን ፡ የምታሳልፍበት ፡ አንድ፡ሰና ቶርዮምና ፡ አንዲት ፡ እናት ፡ አባት ፡ የሞቱባቸው ፡ የድኾች ፡ ልጆች፡ ማሳደጊያ ፡ ቤት ፡ ሠራን ፤ ይህችም ፡ ቦታ ፡ ጥንት ፡ በጋሎች ፡ ጊዜ ፡ ረቢ ፡ ረጺ ፡ (ፃሕስ) ፡ ትባል ፡ ነበር ። አሁንም ፡ በፋሺስት ፡ ወረራ ፡ ጊዜ ፡ ከሌን ፡ ኤዘሊ ፡ ተብላ ፡ ተሰየመች ፡ ይኸውም ፡ ልዩ ፡ ተራራ ፡ ማለት ፡ ነው ።

በውነትም ፡ ይህች ፡ ተራራ ፡ ካገር ፡ ጋራ ፡ ያልተያያዘች ፡ ለብ ቻዋ ፡ የተነጠለች ፡ ኰረብታ ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ ከበሽታና ፡ ከነገር ፡ የራቀች ፡ ናት ፤ ይልቁንም ፡ በጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ከመቶ ፡ ሺህ ፡ የሚ



የረቢ ፣ መድኀኔ ፣ ዓለም ፣ ቤተ ፣ ክርስቲያን ፣ ፊት ፣ ለፊት ።

በልጡ ፡ ዛፎች ፡ ባሕር ፡ ዛፍና ፡ ጥድ ፡ ግራር ፡ ስለ ፡ በቀሉባት ፡ በሩቁ ፡ ስትታይ ፡ እንደ ፡ ስዊስ ፡ ተራሮች ፡ አረንጓዴ ፡ ለብሳ ፡ ደስ ፡ ከማሰኘቷም ፡ በላይ ፡ ከተራራዋ ፡ ጫፍ ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ የጌታችን ፡ የመድኀኔ ፡ ዓለም ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በሩቁ ፡ እየታየ ፡



የረቢ ፡ ተራራ ፡ ጫፍ ።

በመንገድ ፡ የሚሄዱትን ፡ ድኾችና ፡ ችጋረኞችን ፡ ያጽናናል ፤ እኔም ፡ ዘወትር ፡ ማለዳ ፡ ስለምነጣ ፡ በ፲፪ ፡ ሰዓት ፡ ተኵል ፡ ከጎልጎታ ፡ መድኀኔ ፡ ዓለም ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ገብቼ ፡ ጥቂት ፡ የሕሊና ፡ ጸሎት ፡ አደርጋለሁ ።

አንበቢ ፡ ሆይ ፡ ማለዳ ፡ ተነሥተኽ ፡ ችግርኽን ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ለማካፈል ፡ ከዚኽ ፡ ከረቢ ፡ ጎልጎታ ፡ መድኀኔ ፡ ዓለም ፡ ቤተ ፡

ክርስቲያን ፡ ብትገባ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ መጽናናት ፡ ታገኛለኽ ፤ ምክንያቱም ፡ መዠመሪያ ፡ ስትገባ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በመንበሩ ፡ ላይ ፡



አዲስ ፡ አበባን ፡ የሚያሳይ ፡ መስኮት ።

የመድኀኒታችን ፡ ሥዕል ፡ ተሰቅሎ ፡ ይታያል ። በግራ ፡ በኩል ፡ ደግሞ ፡ እንደዚሁ ፡ ያለ ፡ አንድ ፡ የሮፓ ፡ ሠዓሊ ፡ የሣለው ፡ የሚ ያሳዝን ፡ የመድኀኒታችን ፡ ሥዕል ፡ ይታያል ። ከበላዩም ፡ አባቴ ፡

ሆይ ፡ ይቅር ፡ በላቸው ፡ የሚሠሩትን ፡ አያውቁትምና ፡ የሚል ፡ ጽሑፍ ፡ ተጽፏል ፤ በስተቀኝ ፡ በኩል ፡ መድኀኒታችን ፡ በምስማር ፡

በረቢ ፡ መኖሪያ ፡ ቤት ።

የተቸነከረውን ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡ ይታያል ። ከበላዩ ፡ ወደኔ ፡ ኑ ፡ እናንተ ፡ ደካሞች ፡ ሸክማችሁ ፡ የከበዳችሁ ፡ ሁሉ ፡ እኔ ፡ አሳርፋችኋለሁ ፡ የሚል ፡ ጽሑፍ ፡ ይታያል ፤ ከመቅደሱ ፡ ውጭ ፡ ከድንጋዮቹ ፡ ዐም



አትላስ ፡ የሚባለው ፡ ሐውልት ።

ዶች ፡ በላይ ፡ የሩፋኤል ፡ ሥዕል ፡ ኮፒ ፡ (ግልባጭ) ፡ እመቤታችን ፡ ልጅዋን ፡ ታቅፋ ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ልጆች ፡ የምታዝን ፡ የምትለምን ፡ ሁና ፡ ትታያለች ። የቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ጠባቂ ፡ አንድ ፡ መነኰሴ ፡ በረቀቀ ፡ ድምፅ ፡ ኪዳኑን ፡ በዜማና ፡ በንባብ ፡ እያደረሱ ፡ ጸሎተ ፡ ዕጣን ፡

ሲያጥኑ ፡ የማዕጠንቱ ፡ መዐዛና ፡ የጸሎቱ ፡ ርቀት ፡ (ረቂቅነት) ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ የሚታዩት ፡ ሥዕሎች ፡ አንድነት ፡ ሆነው ፡ መንፈስን ፡ ከፍ ፡ የሚያደርግ ፡ ስሜት ፡ ይሰጣሉ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ወጥቼ ፡ ወደ ፡ ደኑ ፡ በሚወስደው ፡ መንገድ ፡ ምርኩዜን ፡ ይዤ ፡ እጓዛለሁ ። ከመንገዱ ፡ ወደ ፡ ቀኝ ፡ አንዲት ፡ ወደ ፡ ተራራዋ ፡ ጫፍ ፡ የምታስወጣ ፡ ቀጭን ፡ መንገድ ፡ ስላለች ፡ ዘወትር ፡ በምናፈስበት ፡ ጊዜ ፡ ከተራራዋ ፡ ጫፍ ፡ ድረስ ፡ በዚችው ፡ መንገድ ፡ መውጣት ፡ እወድ ፡ ነበር ። ምክንያቱም ፡ ከዚያ ፡ ከተራራው ፡ ጫፍ ፡ ሆኖ ፡ የደከምንበትን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንና ፡ የድኾች ፡ ልጆች ፡ ማሳደጊያ ፡ ቤት ፤ ደግሞ ፡ ሰናቶርዮም ፡ ተብሎ ፡ የተሰየመውን ፡ ቤትና ፡ አትክልቱን ፡ ሁሉ ፡ ስለሚያሳይ ፡ ነው ። ይልቁንም ፡ ከተራራው ፡ ጫፍ ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ የዕንጨት ፡ መስቀል ፡ ስለ ፡ ተተከለ ፡ እሱን ፡ በመመልከት ፡ የኀሊና ፡ ደስታ ፡ ይሰማ ፡ ነበር ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከመስቀሉ ፡ ሥር ፡ ካለው ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ ዐረፍ ፡ ብዬ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ሥራ ፡ ካደነቅሁና ፡ ካመሰገንሁ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ እመለሳለሁ ። ከቤቴ ፡ በራፍ ፡ ስደርስ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የሆኑ ፡ አበቦች ፡ ዐቀቦት ፡ በሆኑ ፡ ሥፍራዎች ፡ ላይ ፡ ፈንድተው ፡ ሲታዩ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኝ ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ ባበቦቹ ፡ መከከል ፡ አትላስ ፡ «ATLAS» የሚባለው ፡ የጥንት ፡ ታሪካዊ ፡ የሆነ ፡ የግሪክ ፡ ሐውልት ፡ ዓለምን ፡ ተሸክሞ ፡ ሥሩ ፡ ተግተርትሮ ፡ ሲጨነቅ ፡ በማየቴ ፡ ደስታዬ ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ኀዘን ፡ ይለወጣል ፤ ምክንያቱም ፡ ይህ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ የኀላፊነት ፡ ሸክም ፡ የብርቱ ፡ ቅጣት ፡ ምሳሌ ፡ መሆኑን ፡ ስላሳሰበኝ ፡ ነው ፡ ይልቁንም ፡ ልብን ፡ የሚነካው ፡ አትላስ ፡ በተሸከመው ፡ በዓለም ፡ ዙሪያ ፡ የተቀረጹት ፡ ቃሎች ፡ ናቸው ።

በግዕዝ ፡ ቋንቋ ፡ አ ፡ ዓለም ፡ ክብደ ፡ ጾር ፡ ኀጢአት ፡ እለ ፡ ይትዋረሱኪ ፤ ሰረቅት ፡ ወፈያት ፡ ይላል ፤ ይህ ፡ ባማርኛ ፡ ሲተረጐም ፡ ኀጢአት ፡ ሸክምሽ ፡ የከበደ ፤ ሌቦችና ፡ ቀማኞች ፡ የሚካፈሉሽ ፡ ዓለም ፡ ሆይ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ስለዚህ ፡ በደስታና ፡ በመጽናናት ፡ ከቤቴ ፡ ወጥቼ ፡ በትካዜ ፡ ከቤቴ ፡ ገብቼ ፡ ቍርሴን ፡ ካደረግሁ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሥራዬ ፡ እመለሳለሁ ።

ባለቤቴም፡ ልዕልት ፡ የሻሽ ፡ ወርቅ ፡ ይልማ ፡ እቤተ ፡ ክርስቲያን፡ ገብታ ፡ የተለመደ ፡ ጸሎቷን ፡ ካደረገች ፡ በኋላ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ወጥታ ፡ እናት ፡ አባት ፡ ወደሌላቸው ፡ ልጆች ፡ ማሳደጊያ ፡ ቤት ፡ ሄዳ ፡ ዳቦ ፡ ብስኩት ፡ ከረሜላ ፡ ለልጆቹ ፡ ትሰጣቸው ፡ ነበር ።

ሕፃናቱም፡እማማ ፡ እቴቴ፡እያሉ ፡ ሲስሟት፡ሲያጫውቷት ፡ የሚሰማትን፡ ኀዘን ፡ ያረሳኗት ፡ ነበር። በውነትም፡ በናትና፡ በልጅ ፡መካከል ፡ ያለ፡የተፈጥሮ፡ፍቅር ፡በሁለቱም፡ መካከል ፡ አይጐድልም ፡ ነበር።ከዚያ፡ ወጥታ ፡ጥቂት ፡እልፍ ፡ብሎ ፡ የመንደሩ ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ከሚማሩበት ፡ ተማሪ ፡ ቤት ፡ ገብታ ፡ የልጆቹን ፡ አኳኋንና ፡ ጽዳት ፡ ተመልክታ ፡ የሚያስፈልገውን ፡ነገር ፡ ሁሉ ፡ አድርጋላቸው ፡ በዚያው ፡ መንገድ ፡ላይ ከሚገኘው ፡የዶሮ ፡ማርቢያ ፡ ቤት ፡ ሄዳ ፡ ዶሮዎቹንና፡ ዶንዶዎቹን ፤ ርግቦቹን፡ ተመልክታ ፡ ምግባቸውን ፡ ሰጥታ ፡ በላሞች ፡ ቤት ፡ በኩል ፡ አልፋ ከብቶቹን ፡ ከጐበኘች ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ቤቷ ፡ ትመለሳለች ።

ከዚህ ፡በኋላ፡ቍርሳችንን ፡ በልተን ፡ ሁለታችንም፡ አዲስ፡አበባ ፡ ወደየሥራችን ፡ እንሄዳለን ። ምንም ፡ ያዲስ፡ አበባ ቤታችን ፡ ለሥራችንና ፡ ለወዳጅ ፡ ለዘመድ ፡ መገናኘት ፡ ቢቀርብን ፡ እንኳ ፡ የሚበልጠውን ፡ ጊዜ ፡ ከረቢ ፡ ቤታችን ፡ ሄደን ፡ ስናመሽና ፡ ስናድር ፡ በጣም፡ ደስ ፡ ይለናል ፤ ምክንያቱም ፤ ጸጥታ ፡ ያለውና ፡ አሳብን ፡ የሚሰበስብ ፡ ቦታ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ነው ።

የዘወትር፡የማታ፡ ፕሮግራማችን።ራታችንን፡ከበላን፡በኋላ፡ከምድጃችን፡ ዳር፡ ተቀምጠን ፡ የዓለምን ፡ ወሬ ፡ በራዲዮ ፡ እንሰማለን፤አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ክላሲክ ፡ ሙዚቃ ፡ (መንፈሳዊ ፤ የሆነ ፡ ሙዚቃ) ፡ እንሰማለን ፤ ለምሳሌ ፤ እንደ ፡ ሞዛርት ፡ «MOZART» ፡ እስትራዎስ ፡ «STRAUSS › ቤቶቬን፡«BEETHOVEN» ሹቢር፡ ‹SCHUBERT» ሌሎችም ፡ እነዚህን ፡ የመሰሉ ፡ የነፍስ ፡ ምግብ ፡ የሚሆነውን ፡ መንፈሳዊ ፡ ዜማ ፡ እየቃኙ፡ ምልክት፡ ያወጡ፡ ዐዋቂዎች ፡ ናቸው ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ከኛው ፡ ዘንድ ፡ካሉት ፡ ፊልሞች፡ ሲኒማ፡ እናያለን ። ለምሳሌ ፤የሙት ፡ ቤት ፡ መታሰቢያ ፡ የሚባለውን ፡ የሙሴ ፡ ቴሊራን ፡ ግንብ ፡ የሚያሳይ፡ «MEMOIRE DES MAISONS MORTES» ፡ ጆርጅ ፡ ቤዚ ፡ «GEORGES BIZET» የሚባል፡የሙዚቃ፡ሊቅ፡ተፈጥሮው፡እንደ፡ምን፡ እንደ፡ ገዛውና ፡ ካሰበው ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡ እንደ ፡ ደረሰ ፡ የሚያሳይ ፡

ነው ። ደግሞ ፡ የክርስቶስ ፡ እርምጃ ፡ የሚል ፡ በቅድስት ፡ አገር ፡ መድኀኒታችን ፡ የረገጣቸውን ፡ መሬቶች ሁሉ ፡ የሚያሳይና ፡ ሌሎችም ፡ ክላሲክ ፡ የሆኑ ፡ ፊልሞች ፡ ናቸው ።

እኔም ፡ ባለቤቴም ፡ የምንወደው ፡ ፊልም ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ልጆች ፡ የሚደርስባቸው ፡ ዕድል ፡ በመጥፎ ፡ ተዠምሮ ፡ የሚጨረስና ፡ ወይም፡ በመጥፎ ፡ ተዠምሮ ፤ በመልካም፡ የሚጨረስ ፡ ልብን ፡ የሚነካ፡ መንፈስን፡ ከፍ፡ የሚያደርግ፡ ሲኒማ፡ ስለ፡ ሆነ፡ይህ፡ከከተማው፡ ውስጥ፡ በጣም፡ ባለመታየቱ፡ ወደሲኒማ፡ ቤት፡መሄድ፡ አንፈቅድም፡ ነበር ። ስለዚህ፡የሚበልጠውን ፡ ጊዜያችንን ፡ ከምድጃችን፡ አጠገብ፡ ተቀምጠን ፡ እኔም ፡ መጽሐፍ ፡ ለመጻፍ፡ ማስታወሻ ፡ መውሰድና ፡ ባለቤቴም፡ መጽሐፍ ፡ ማንበብ ፡ ነበር። አንባቢ ፡ ሆይ ፡ በዚያች ፡ ልዩ ፡ በሆነች ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ከተሠራችው ፡ ቤታችን፡ ሰበሰብ ፡ ሆነን፡ ያዲስ ፡ አበባን፡ ከተማ ፡ ውበት ፡ ማየት ፡ እንደምን ደስ ፡ ያሰኛል ፤ ከዚህም ፡ በቀር ፡ ማለዳ ፡ ከተራራው ፡ ጫፍ ፡ ላይ ፡ ወጥቶ ፡ የእንጦጦንና ፡ የፉሪን ፤ የየረርንና ፡ የዝቋላን ፡ ተራሮች ፡ ከሰማዩ ፡ ጋራ ፡ የተጋጠሙ ፡ መስለው ፡ በጉም ፡ ተጐናጽፈው ፡ ፀሐይ ፡ ሲገባና፡ ሲወጣ ፡ በተራሮች ፡ ላይ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ቀለም ፡ ወድቆባቸው ፡ ሲታዩ ፡ መንፈስን ፡ ከፍ ፡ በማድረጋቸው ፡ የጽሕፈትንና ፡ የቅኔ ፡ መቍጠርን ፡ አሳብ ፡ ያነቃቃሉ ፤ ‹INSPIRATON› ።

ስለዚህ ፡ ቦታ ፡ ዘመዴ ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ጊዜ ፡ በማግኘትና ፡ መጽሐፎችን ፡ በማንበብ ፡ ይልቁንም ፡ ልዩ ፡ በሆነችው ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ በጸጥታ ፡ በመኖርና ፡ በላይዋ ፡ ላይ ፡ በተሠራችው ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መንፈሳዊ ፡ አስተዋሽነት ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ የተመለከቱትን ፡ ትንንሽ ፡ መጽሐፎች ፡ ለመጻፍ ፡ ርዳታ ፡ አገኘሁ ። እነዚሁም ፡

፩ኛ ፡ ዓለም ፡ ወረተኛ ፡
፪ኛ ፡ የቃየል ፡ ድንጋይ ፡
፫ኛ ፡ የደም ፡ ድምፅ ፡
፬ኛ ፡ ሣልሳዊ ፡ ዳዊት ፡
፭ኛ ፡ የድኾች ፡ ከተማ ፡
፮ኛ ፡ አሳብና ፡ ሰው ።
፯ኛ ፡ አልሞትኹም ፡ ብዬ ፡ አልዋሽም ፡
፰ኛ ፡ የማይጨው ፡ ጦርነትና ፡ ባጭሩ ፡ የዓለም ፡ ፖለቲካ ፡ ናቸው ።



እግዚአብሔር ፡ አዳምን ፡ አለው ፡ ምድር ፡ ስላንተ ፡ የተረገመች ፡ ትሁን ።
አዳምም ፡ ሚስቱን ፡ ሔዋንን ፡ ዐወቀ ፡ አረገዘች ፡ ቃየልንም ፡ ወለደች ።

## የ ቃ የ ል ፡ ድ ን ጋ ይ ።

እግዚአብሔር ፡ ቃየልን ፡ አለው ፡ አቤል ፡ ወንድምህ ፡ ወዴት ፡ ነው ። ርሱም ፡ አለ ፡ አላውቅም ፤ እኔ ፡ የወንድሜ ፡ ጠባቂው ፡ ነኝን ።

አለውም ፡ ምን ፡ አደረግኽ ፡ የወንድምኽ ፡ የደሙ ፡ ድምፅ ፡ ወደኔ ፡ ከምድር ፡ ይጮኻል ።

አሁንም ፡ አንተ ፡ ርጉም ፡ ነኽ ፡ በምድርም ፡ ላይ ፡ አፏን ፡ በከፈተች ፡ የወንድምኽን ፡ ደም ፡ ከጅኽ ፡ ትቀበል ፡ ዘንድ ፡ (ዘፍ ፡ ፬ ፡ ፱–፲፩) ።

## ማስታወቂያ ።

ይህ ፡ የቃየል ፡ ድንጋይ፡የተባለ ፡ መጽሐፍ ፡ የዓለምን ፡ የኅሊና፡ ክርክር ፡ በሰዎች ፡ አስመስሎ ፡ ባጭሩ ፡ የሚያስረዳ ፡ ታሪክ ፡ ነው ።

በውስጡም ፡ የሚገኙት ፡ ምግባሮች ፡ ከዚህ ቀጥሎ የተመለከ ቱት ናቸው ።

፩ኛ ፤ የሰው ፡ ልጆች ፡ ትዳር ፡ የተወጠነው ፡ በደም ፡ ማፍሰስ፡ መሆኑን ።

፪ኛ ፤ የቃየል ፡ ድንጋይ ፡ የዘመናዊው ፡ መሣሪያ ፡ ሁሉ ፡ አባት ፡ መሆኑን ።

፫ኛ ፤ እግዚአብሔር ፡ በቸርነቱ ፡ የገለጸልን ፡ ዕውቀቶች ፡ ሁሉ፡ የቃየልን ፡ ድንጋይ ፡ እንደ ፡ ተከተሉ ።

፬ኛ ፤ በዓለም ፡ ላይ ፡ ሰላም ፡ እንደማይገኝ ።

፭ኛ ፤ በዚህ ፡ በክፉ ፡ ጊዜ ፡ ሰው ፡ ኅሊናውን ፡ የሚደግፍ በት ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ያሳያል ።

## ተከራካሪዎች ።

፩ኛ ፤ አቶ ፡ ማስተዋል ።
፪ኛ ፡ አቶ ፡ ጥበቡ ፡
፫ኛ ፤ አቶ ፡ ዐወቀ ፡
፬ኛ ፤ አቶ ፡ ብልጦ ፡
፭ኛ ፤ አቶ ፡ ብልኅ ፡
፮ኛ ፤ አቶ ፡ ፈላስፋ ።

# የ ቃ የ ል ፡ ድ ን ጋ ይ ።

አቶ ፡ ማስተዋል ፡-ወንድሜ ፡ አቶ ፡ ጥበቡ ፡ ይህ ከፊታችን ፡ የምናየው ፡ ድንጋይ ፡ ምንድነው ።

አቶ ፡ ጥበቡ ፤—ታሪካዊ ፡ የሆነ ፡ የቃየል ፡ ድንጋይ ፡ ነው ።

አቶ ፡ ማስተዋል ፡—ታሪካዊ ፡ የሆነበት ፡ ምክንያት ፡ ምንድነው

አቶ ፡ ጥበቡ ፡-ቃየል ፡ ወንድሙን ፡ አቤልን ፡ በሚስቱ ፡ ደም ፡ ግባትና ፡ ውበት ፡ ምክንያት ፡ እሷን ፡ ለራሱ ፡ ለመውሰድ ፡ በድንጋይ ፡ ስለገደለው ፡ ያ ንጋይን ፡ አዲስ ፡ መሣሪያ ፡ አወጣ ። ስለዚህ ፡ የጠላት ፡ ማጥቂያ ፡ መሣሪያዎች ፡ ሁሉ ፡ አባት ፡ የቃየል ፡ ድንጋይ፡ ስለሆነ ፡ ለመታሰቢያ ፡ እንዲሆን ፡ እነሆ ፡ ከፊታችን ፡ አድርገነዋል ።

አቶ ፡ ዐወቀ ፤-ወይግሩም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የማይሰማ ፡ ነገር ፡ የለም ፤ እባክህ ፡ ወንድሜ ፡ ጥበቡ ፡ የቃየል ፡ ድንጋይ ፡ ምን ፡ መታሰቢያ ፡ እንዲኖረው ፡ ያስፈልጋል ። ቃየል ፡ የድንጋይን ፡ መሣሪያነት ፡ ብቻ ፡ አልፈጠረም ፤ ወንድሙን ፡ አቤልን ፡ በመግደሉ ፡ ሞትን ፤ ቅንዓትን ፤ ተንኰልን ፤ ራስን ፡ ብቻ፡ መውደድን ፤ ዝሙትን ፤ ደግሞ ፡ እግዚአብሔር ፡ አቤል ፡ ወንድምህ ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ቢጠይቀው ፡ እኔ ፡ የወንድሜ ፡ ጠባቂ ፡ ነኝን ፡ ብሎ ፡ በመመለሱ ፡ እብሪትና ፡ ሽፍጥ ፡ በጠቅላላው ፡ ኀጢአቶች ፡ ሁሉ ፡ ከቃየል ፡ እንደ ፡ ተፈጠሩ ፡ መጽሐፍ ፡ ይናገራል ። አሁን ፡ ወንድሜ ፡ እንደምትለው ፡ ለቃየል ፡ ድንጋይ ፡ መታሰቢያ ፡ ለማቆም ፡ የሚገባ ፡ ከሆነ ፡ በኀጢአተኞች ፡ ሁሉ ፡ መታሰቢያ ፡ ሊቆምላቸው ፡ ይገባል ፡ ማለት ፡ አይሆንብኝምን ።

አቶ ፡ ብልጠ ፡-ተው ፡ ወንድሜ ፡ ዐወቀ ፡ ይህነን ፡ ያህል በሩቅ ፡ ማየት፡ አይገባህም፤ ስለዚህ፡ ነገር ፡ እኔ፡ ሁላችሁንም፡ ለማስማማት፡ እችላለሁ ። የቃየል ፡ ድንጋይ ፡ አቤልን ፡ ወንድሙን ፡ በመግደሉ ፡ የሚያሳዝን ፡ ቢሆን ፡ እንኳ ፡ ከቃየል ፡ ድንጋይ ፡ የተወለዱ ፡ የጥበብ ፡ መሣሪያዎች ፡ የጠላት ፡ ማጥቂያ ፡ በመሆናቸው ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ የሰው ፡ ልጆች ሁሉ፡ በመሣሪያ፡ መበላለጥ፡ ምክንያት ፡ ያገኙትን ፡ የዝግንነት ፡ ክብር ፡ ገልጦ፡ አሳይቷል ። ለምሳሌ፤ ከታሪክ፡ በፊት፡ ብዙ፡ አርበኞች፡ ጠላታቸውን፡ ያጠቁ፡ በቃየል፡ ድንጋይ፡ ልጆች ፡ በፋስ ፡ በጦር ፡

በቀስት፡ በጐራዴ፡ መሆኑን፡ አትስተውም ። ዳዊት፡ አባታችን ፡ ከፍ፡ ያለ ውን ፡ ታሪካዊ፡ ድል ፡ ያገኘ፡ ጎልያድን፡ በወንጭፍ ፡ በሩቅ፡ በመምታቱ፡ አይደለምን ፤ ደረት ፡ ለደረት፡ ተያይዘው ፡ ቢታገሉ ፡ ግን ፡ ዳዊት፡ ጎልያ ድን፡ ባላሸነፈው ፡ ነበር። ከዚህም፡ በኋላ ፡ የቃየል ፡ ድንጋይ፤ እየተጣራ፡ በመሔዱ፡ ባ፲፰፻፹፰ ፡ ዓ፡ ም ፡ (፩) የተሻሻለ፡ መሣሪያ ፡ ብሩድን ፡ በመው ለዱ ፡ በክሬሲ ፡ ላይ ፡ እንግሊዞች ፡ ያገኙትን ፡ የድል ፡ ክብር ፡ መጠየቅ፡ ነው ። ክቡር፡ ወንድሜ ፡ ስንኳን፡ ሰው ፡ ፀዋቂ፡ ሆኖ ፡ በእግዚአብሔር፡ መልክ ፡ የተፈጠረው ፡ በሬ ፡ እንኳ ፡ ጠላቱን፡ ለማጥቂያ፡ ጠንካራ፡ መሣ ሪያውን ፡ መርጦ ፡ ቀንዱን ፡ ለጠላቱ ፡ ይመክታል ፤ ስለዚህ ፡ ለቃየል ፡ ድንጋይ ፡ የጥበብ ፡ መሣሪያዎች ፡ ሁሉ ፡ አባት ፡ መታሰቢያ ፡ እንዳይቆ ምለት ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ መቃወም ፡ የሚገባ ፡ አይመስለኝም ።

አቶ ፡ ጥበቡ ፡-ወንድሞቼ ፡ይቅርታ ፡ እየጠየቅሁ ፡ አንዲት ፡ ነገር፡ ላሳስባችሁ ፡እወዳለሁ፡ሰው፡ሊተወው፡ የማይችለውን፡ ኅጢአት ፡ ጽድቅ እንዲሆንለት ፡ በትርጕም ፡ ለማሻሻል ፡ መጣሩ ፡ የተለመደ፡ ነው ። ኅጢ አቶች ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ተከፋፍለው ፡ የግል ፡ ገንዘብ ፡ ሆነዋል፤ ስለዚህ ፡ የወንድማችን፡ ኅጢአት ፡ ብቻ ፡ ነው፡ እንጂ ፡ የሚታየን ፡ ራሳ ችንን ፡ በራሳችን ፡ ማየት ፡ አንችልም ። ወንድማችን ፡ አቶ ፡ ብልጦ ፡ ራሱን፡ ለመጥቀሚያ፡ ወንድምን ፡ ለጥቅም ፡ ማጥፋት፡ ትልቅ ፡ የውቀት ሥራ ፡ መሆኑን ፡ አስረዳን ። ቅድም ፡ እንዳመለከትኩት ፡ አቶ ፡ ብልጦ ፡ ራስን ፡ ብቻ፡ መውደድ ፡ የሱ ፡ የግል ፡ ገንዘቡ ፡ ስለሆነ ፡ አለመጠቃ ትን ፡ መሸፈኛ ፡ አድርጎ ፡ የወንድሞችን ፡ ማጥቂያ ፡መሣሪያ ፡ የተቀደሰ ስጦታ ፡ መሆኑን ፡ በሰፊው ፡ አስረዳን ። ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ሰሎሞን ፡ የብ ልኅ ፡ ዓይኑ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ነው ፡ ብሏልና ፤ ብልኅ ፡ ወንድሜ ፡ እስቲ፡ በኛም ፡ በንተም ፡ ላይ ፡ እውነትን ፡ ተመልክተኽ ፡ ፍረድ ።

አቶ፡ ብልኅ ፡-ወንድሜ ፡ጥበቡ ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ የውነት ፡ ፍርድ የለም ፤ እኔም ፡ ብሆን ፡ ሥራዬን ፡ ሁሉ ፡ በብልኅነት ፡ እየገፋሁ ፡ ካሰብ ኩት ፡ ስፍራ ፡ አደርሰዋለሁ ፡ እንጂ ፡ ከነፋስና ፡ ከጐርፍ ፡ ጋራ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ አልጋፋም ። ትልቅ ፡ የነፋስ፡ ሞገድ ፡ በላዩ፡ ላይ ፡ በመጣ ፡ጊዜ፡ እንደ ፡ ሰንበሌጥ ፡ ተኝቼ፡ አሳልፈዋለሁ፡ እንጂ ፡ አልታገልም፤ ቢሆንም አሁን፡ ለጠየቅኸኝ፡ ጕዳይ፡ ካባታችን፡ ከአዳም፡ ታሪክ ፡ ዠምሬ፡ ባጭሩ ሰው ፡ ምን ፡ እንደሆን ፡ ላስረዳኸ ፡ እችላለሁ ። ሰው ፡ በእግዚአብሔር ፡

፩ ከዚህ ፡ ዠምሮ ፡ ወደፊት ፡ ያለው ፡ ቍጥር ፡ ሁሉ ፡ እንዳውሮፓ ፡ አቈጣጠር ፡ ነው ።

መልክ ፡ ሲፈጠር ፡ በውቀት ፡ እግዚአብሔርን ፡ ሊመስል ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ፈቃድ ፡ ትቶ ፡ በራሱ ፡ ፈቃድ ፡ ዕውቀትን ፡ ስለ ፈለገ ፤ አትብላ ፡ የተባለውን ፡ ክፉና ፡ በጎ ፡ የምታስታውቀውን ፡ ፍሬ ፡ በገዛ ፡ እጁ ፡ በሚስቱ ፡ ፈቃድ ፡ ስለ ፡ በላ ፡ ክፉና ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ዐዋቂ ፡ ፍጥረት ፡ ሆነ ፡ ስለዚህ ፡ ሰው ፡ ለሠራው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ክፉም ፡ ቢሆን ፡ በጎም ፡ ቢሆን ፡ በገዛ ፡ ፈቃዱ ፡ ኀላፊነትን ፤ ወሰደ ። ነገር ፡ ግን ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ምንም ፡ ዕውቀቱን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ወደ ፡ መሥራት ፡ ቢያዘነብል ፡ እንኳ ፡ መልካምንም ፡ ሥራ ፡ ለመሥራትና ፡ ለሰው ፡ ጥቅም ፡ የሚሆኑትን ፡ ጥበቦች ፡ ለማውጣት ፡ ችሎታ ፡ ያለው ፡ ፍጥረት ፡ መሆኑንም ፡ አለመዘ ንጋት ፡ ነው ።

ለምሳሌ ፡ ማተሚያ ፡ ባ፲፬፻፶፫ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ ዮሐንስ ፡ ጉታ ምቤርግ ፡ በሚባል ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ ተገለጠ ። ይህ ፡ ጥበብ ፡ የውቀቶች ፡ ሁሉ ፡ አባት ፡ ተባለ ፤ እግዚአብሔር ፡ ዓለምን ፡ በፈጠረ ፡ ጊዜ ፡ ብርሃን ፡ ይሁን ፡ ሲል ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ተገለጠ ፤ ማተሚያም ፡ ሲወጣ ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ጥበብ ፡ ሁሉ ፡ ለዓለም ፡ ታየ ። ከዚህም ፡ በኋላ የሰው ፡ ልጆች ፡ የበለጠ ፡ መገናኘትና ፡ መቀራረብ ፡ መተጋገዝ ፡ መፋቀር ፡ እን ዲያገኙ ፡ ባ፲፮፻፲፫ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ ላበት ፡ መኪናዎችን ፡ በፍጥነት ፡ እንዲያስኬድ ፡ ዴኒ ፡ ፓፓ ፡ በሚባል ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ ተገለጠ ። ከጌታችን ፡ ከክርስቶስ ፡ ልደት ፡ በፊት ፡ ፮፻ ፡ ዘመን ፡ ታሊስ ፡ በሚባል ፡ ኤሌክት ሪክ ፡ መኖሩ ፡ ቢታወቅ ፡ እንኳ ፡ ባ፲፰፻፫ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ማርኮኒ ፡ በሚባል ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ ዓለምን ፡ አንድ ፡ የሚያደርግ ፡ ጥበብ ፡ ተገለጠ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አዴር ፡ ካሌማ ፡ በሚባል ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ መኪና ፡ በአየር ፡ እን ዲበር ፡ ተገለጠ ። እነዚህ ፡ ሁሉ ፡ ከፍ ፡ ያሉት ፡ ጥበቦች ፡ የተገለጡት ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ባገር ፡ ርቀት ፡ ምክንያት ፡ በሐሳብ ፡ እንዳይለያዩ ፡ባንድ ፡ ቤት ፡ እንደሚኖሩ ፡ ቤተ ፡ ዘመዶች ፡ እንዲቃረቡና ፡ እንዲተሳሰቡ ፡ እንዲረዳዱ ፡ ነው ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ርስ ፡ በርሳቸው ፡ ካልተረዳዱ ፡ ሰው ፡ ብቻውን ፡ ለመቆም ፡ የተፈጠረ ፡ ነገር ፡ አይደለም ።

ስለዚህ ፡ ቃየል ፡ የወንድምን ፡ መግደያ ፡ ድንጋይን ፡ በመፍጠሩ ፡ ስናዝን ፡ እንሆ ፡ ደግሞ ፡ ለሰው ፡ ጥቅም ፡ የሚሆኑ ፡ ጥበቦች ፡ ከአዳም ፡

ልጆች፡ መፈጠራቸውን፡ ስንመለከት ፡በጣም፡ደስ፡ይለናል፡ በዓለም፡ላይ፡ክፉ፡መስሎ፡ የሚታየን፡ነገር፡ መልካም፡ነገር፡ሆኖ ፡ የሚያገለግልበት፡ጊዜ፤ እንደሚኖረው፡እናምናለን። ለምሳሌ፡መርዝ፡ ከሁሉ፡ነገር፡ይበልጥ፡አጥፊ፡ ሆኖ፡ሳለ፡ሰውን፡ለማዳን፡ የሚገባበት፡ጊዜ፡አለው፡ሰሎሞን፡ለሁሉ፡ጊዜ፡ አለው፡እንዳለው፡ ሁሉ፡ መነቃቀፍን፡ትተን፡ሁሉንም፡በየሥራው፡ብናመሰግን፡ይሻል፡ ይመስለኛል፤ እህ፡ ወንድሜ፡ፈላስፋ፡ አንተ፡ ምን፡ ታስባለኽ።

አቶ፡ፈላስፋ፤–ወንድሜ፡ ሆይ፡ቅድም፡ እንደ፡ ተናገርከው፡ ከነፋስና፡ከጕርፍ፡ጋራ፡መጋፋትን፡ስላልፈለግኽ፡ከጊዜው፡ነፋስ፡ ጋራ፡አብረህ፡ ስለምትነዳ፡ ሁለቱን፡ የማይሰማሙ፡ነገሮች፡በብልኀት፡ለማሰማማት፡የሰነዘርከው፡ነገር፡ፍሬው፡ ወደ፡ሐሰት፡ አደላብኽ፡ቢሆንም፡የተወደድኽ፡ወንድሜ፡ሆይ፡ አስበኽ፡ስለ፡ ጠየቅኽኝ፡ነገር፡ላስረዳኽ፡እፈቅዳለሁ።ቅድም፡የሰው፡ልጆች፡ባሕርይ፡ ከበጎው፡ነገር፡ ይልቅ፡ወደ፡ክፉው፡ያዘነብላል፡ብለኽ፡እንደ፡ተናገርከው፡ለሰው፡ጥቅም፡የተፈጠሩት፡ጥበቦች፡ሁሉ፡ ከሰው፡ ባሕርይ፡ጋራ፡ወደ፡ጥፋት፡አዘነበሉ፡እንጂ፡ጥቅም፡አልሆኑም፤ክፉ፡ ዛፍ፡መልካም፡ፍሬ፡እያፈራም፡እንደ፡ተባለው፡የቃየል፡መራራ፡ ፍሬዎች፡ለሰው፡ልጆች፡ለመጠቃቀሚያ፡የተፈጠሩትን፡ሁሉ፡የቃየልን፡ድንጋይና፡ባሩድ፡ ተከትለው፡የወንድሞችን፡መኰኛ፡መሣሪያ፡እንዲሆኑ፡የሰው፡ ክፉት ፡ አከናወናቸው ።

አቶ ፡ ማስተዋል ፤–ወንድሜ፡ፈላስፋ፡ሆይ፡እንደ፡ምን ፡ ለሰው፡ልጆች፡ጥቅም፡የተገለጡ፡የሰላም፡ጥበቦች፡ሁሉ፡ የቃየልን፡ድንጋይና፡ባሩድ፡ተከትለው፡የወንድሞች፡መኰኛ፡ሆኑ፡ ትላለኽ፡የሚበቃ ፡ ማስረጃ ፡ አለኽን ።

አቶ፡ፈላስፋ፤–አዎን፡በጣም፡የሚበቃ፡ማስረጃ፡አለኝ፡ነገር፡ ግን፡ጊዜያችሁን፡እንዳላጠፋ፡ባጭሩ፡በኛው፡ዘመን፡የደረሰውን፡ ላስረዳችሁ፡እፈቅዳለሁ ።በ፲፱፻፲፬፡ዓ፡ም፡ዳግማዊ፡ጊዮም፡የፕሩስ፡ ንጉሥ፡የጀርመን፡ንጉሠ፡ነገሥት፡በሆነ፡ጊዜ፡ራሱን፡ከፍ፡ከፍ፡ በማድረጉና፡በእብሪቱ፡ምክንያት፡ከ፲፱፻፲፬፡እስከ፡፲፱፻፲፰፡ዓ፡ም፡ የተደረገውን፡የዓለም፡ጦርነት ኀላፊነት፡ወሰደ፡ከዚህ፡በኋላ፡ጊዮም፡

ዓለምን ፡ በእሳት ፡ ውስጥ፡ጣለው ። የቃየል ፡ ልጅ ፡ ጊዮም፡ከመምህሩ ፡ ደቀ ፡ መዝሙሩ ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ለጦር ፡ አለቆቹ ፡ ሰውም ፡ ከብ ትም ፡ ቤትም ፡ ዛፍም ፡ ብታገኙ ፡ አፍርሱት ፡ ቍረጡት ፡ አቃጥሉት ፡ ብሎ ፡ የጭካኔ ፡ ትእዛዝ ፡ ሰጠ ፤ በዚህ ፡ ጦርነት ፡ ምክንያት ፡ አዲስ ፡ በወጡት ፡ መሣሪያዎች ፡ ወንድም ፡ ሴትም ፡ ሕፃንም ፡ ሽማግሌም ፡ ሳይቀሩ ፡ በእሳት ፡ ተቃጠሉ ። እግዚአብሔር ፡ በቸርነቱ ፡ ልንጠቃቀ ምበቸው ፡ የገለጸልንን ፡ ጥበቦች ፡ ሁሉ ፡ ለቃየል ፤ ድንጋይና ፡ ለባ ሩድ ፡ አገልጋይ ፡ ረዳት ፡ አደረጓቸው ። ከዚህም ፡ በኋላ ፡ ሒትለርና ፡ ሙሶሊኒ ፡ በዲስኩር ፡ (ስብከት፡) ማሳመር፡ና ፡ በተስፋ ፡ የጀርመንንና ፡ የጣልያንን ፡ ልብ ፡ ማርከው ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ ባደረጉት ፡ ጦርነት ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ጥቅም ፡ የተገለጡት ፡ ጥበቦች ፡ ይቅሩና ፡ ፋርማሴ ፡ (መድኃኒት ፡ ቤት) ፡ ሳይቀር ፡ የጦር ፡ ፋብሪካ ፡ ሆነ፡ ይህ ፡ ያቀረብኩት ፡ ሐሳብ ፡ እውነት ፡ ነውን ፡ ሐሰት ።

አቶ ፡ ብልጦ ፤-እኔ፡ደግሞ፡አንዲት፡ቃል፡እንድጠይቅኽ፡ፍቀድልኝ ።

አቶ ፡ ፈላስፋ ፤ -እሺ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኛልና ፡ ጠይቀኝ ።

አቶ ፡ ብልጦ ፡-ወንድሜ ፡ ፈላስፋ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ዘወትር ፡ ከነ ፋ.ስና ፡ ከጐርፍ ፡ ጋር ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ስለምትጋፋ ፡ አሳብኽ ፡ ወደ ፡ ፊት ፤ አይራመድም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ከወንድሙ ፡ ጋር ፡ እየታገለ ፡ ብል ጫን ፡ ካላገኘ ፡ የማይንቀሳቀስ ፡ ንብረት ፡ መሆኑ ፡ አይደለምን ፡ ? ስን ኳን ፡ ሰው ፡ ዕንጨት ፡ ርስ ፡ በርሱ፡ ካልተፋጨ ፡ እሳት ፡ አይወጣውም ፡ ሰውማ ፡ ከወንድሙ ፡ ጋር ፡ ካልታገለ ፡ ከፍ ፡ ካለ ፡ ዕውቀትና ፡ ከሰው ነት ፡ ሙብት ፡ በምን ፡ አኳኋን ፡ ይደርሳል ። ቢላዋ ፡ እንኳ ፡ ስለት ፡ የሚወጣው ፤ ርስ ፡ በርሱ ፡ ሲፋጭ ፡ ነው ። የሰው ፡ ልጆች ፡ በይቀናኑ ፤ ባይፈካከሩ፡ አንዱን ፡ አንዱ፡ ለመብለጥ፡ ባይሽቀዳደሙ ፤ ኑሯቸውንና ፡ ዕውቀታቸውን ፡ ለማሻሻል ፡ አይችሉም ፡ ነበር ። የዕውቀትም ፡ እሳት ፡ ተዳፍኖ ፡ ይኖር ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ብርሃኑ ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ አያበራም ፡ ነበር ፤ ይህ ፡ ርግጥ ፡ አይደለምን ።

አቶ ፡ፈላስፋ፤-ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ከነፋስና ፡ከጐርፍ ፡ጋር፡ ፊት ፡ለፊት ስለምትታገል ፡አሳብኽ ፡ወደ ፡ፊት ፡ አይራመድም ፡ ስላልከኝ ፡ መገመ ሪያ ፡ ባጭሩ ፡ የምመልስልኽ ፡ ይህ ፡ነው ። እውነት ፡ ከነፋስና ፡ ከጐ

ርፍ ፡ ጋር ፡ ስለምትታገል፡ ቶሎ ፡ ብሎ ፡አይቀናትም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ዝግ፡ ብላ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ድልን ፡ ታገኛለች ። ሐሰት ፡ ግን ፡ ቶሎ ፡ ስለሚቀናት፡ ሁሉንም፡ ነገር ፡ቶሎ፡ታጣዋለች ።ከዚህ፡ቀጥዬ፡ስለ፡ጠየቅኸኝ፡ጉዳዮች፡ ላስረዳኽ ፡ እወዳለሁና ፡ ስማኝ ። ቃየል ፡ የወንድሙን ፡ የአቤልን ፡ ሚስት ፡ በውበቷና ፡ በደም ፡ ግባቷ ፡ ቀንቶ ፡ ወንድሙን ፡ ገድሎ ፡ በመውሰዱ ፡ቃየል ፡ የተቅበዘበዝኩም፡ የኰበለልኩም ፡እሆናለሁ ፡በም ድር ፡ ያገኘኝም ፡ ሁሉ ፡ ይገድለኛል ፡ብሎ ፡ ራሱ ፡ በራሱ ፡ ፍርድን ፡ ተቀበለ ፤ አንተ ፡ ግን ፡ ገና ፡ በራስኽ ፡ አልፈረድኽም ። እንደዚህም ፡ ሁሉ ፡ የቃየል ፡ ልጅ ፡ሙሶሊኒ ፡ የኢትዮጵያን፡ ደም ፡ ግባትና ፡ ውበት፡ አይቶ ፡ ስላማረው ፡ ባሏን ፡ ወግቶ ፡ልጆቿን ፡ በእሳት ፡አቃጥሎ ፡ በግፍ፡ በመውሰዱ ፡ ምክንያት ፡ ከገሩ ፡ ላይ ፡ ኰብሎ ፡ እባዕድ ፡ አገር ፡ ሄዶ ፡ ከባዕድ ፡ አገር ፡ ተቅበዝብዞ ፡ አገሩ ፡ ላይ ፡ መጥቶ ፡ ያገኙት ፡ ወንድ ሞቹ ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ገደሉት ፡ ምን ፡ ተጠቀመ ። የሰውን ፡ አገር ፡ አጥ ፍቶ ፡ የራስንም ፡ አገርና ፡ ሕዝብ ፡ ከችግርና ፡ ከውርደት ፡ ላይ ፡ መጣል ፡ ነውን ፡ ርስ ፡ በርስ ፡ በመታገል ፡ ዕውቀት ፡ ይገኛል ፡ የምት ለው ፤ ይልቁንስ ፡ ስንት ፡ ዐዋቂዎችና ፡ ፈላስፎች ፡ ያሉበት ፡ አገር ፡ የጣልያን ፡ ሕዝብ ፡ ያንድ ፡ ዕብድ ፡ ሰው ፡ ትከሻ ፡ ይዘው ፡ እየተ መሩ ፡ ከጕድባ ፡ መግባትና ፡ ጥፋታቸውን ፡ አለመመልከት ፡ በጣም ፡ ያሳዝናል ።

አቶ ፡ማስተዋል፡— ወንድሜ ፡ፈላስፋ ፡ሆይ ፡ቅድም ፡ከተናገርኸው፡ ውስጥ ፡ በጣም ፡ የተሰማኝ ፡ ፋርማሴ ፡ ሳይቀር ፡ የጦር ፡ መሣሪያ ፡ ፋብ ሪካ ፡ ሆነ ፡ ብለኽ ፡ ያሳሰብከው ፡ ነው ፡ እባክኽ ፡ ይህነን ፡ በዝር ዝር ፡ አስረዳኝ ።

አቶ ፡ ፈላስፋ ፤— በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ቅድም ፡ እንደ ፡ ነገር ኩኽ ፡ ዳግማዊ ፡ ጊዮም ፡ ዓለምን ፡ ለመግዛት ፡ እንደ ፡ ተነሣ ፡ ሁሉ፡ ሒትለር ፡ ደግሞ ፡ ዓለምን ፡ ለመግዛት ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ምኞት ፡ ቢያድ ርበት ፡ የጀርመን ፡ ሺሚስት ፡ ሁሉ ፡ የመርዝ ፡ መሣሪያ ፡ እንዲፈ ልጉ ፡ ስላደረገ ፡ ቅድም ፡ ወንድሜ ፡ ብልጦ ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ጥበ ቦች ፡ ርስ ፡ በርሳቸው ፡ ሲፋጩ ፡ ቦምብ ፡ አቶሚክን ፡ ወለዱ ። ይህ፡ ፋርማሴ ፡ የወለደው ፡ የዓለም ፡ ጥፋት ፡ የቃየል ፡ ድንጋይ ፡ የልጅ ፡ ልጅ ፡ ዓለምን ፡ ወደ ፡ ታላቅ ፡ ጉዳት ፡ ያደርሰዋል ፡ እየተ ባለ ፡ ያሠጋል ። ይኸውም ፡ በጃፓን ፡ ላይ ፡ በተደረገው ፡ ጦርነት በናጋሲኪና ፡ በሔሮሺማ ፡ በሚባሉት ፡ ከተሞች ፡ ላይ ፡ ተፈትኗል ፡

እስካሁንም ፡ ድረስ ፡ የእሳቱ ፡ ማዕበል ፡ ጸጥ ፡ አላለም ። በዙሪያው ፡ ያሉ ፡ ሕዝቦች ፡ በእሳት ፡ ማዕበል ፡ የሰጠሙትን ፡ ወንድሞቻቸውን ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ በሩቅ ፡ ያዩዋቸዋል ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ተዳፍኖ ፡ የነበረው ፡ ትልቅ ፡ ዕውቀት ፡ ፋርማሴ ፡ የወለደው ፡ የጥፋት ፡ ልጅ ።

አቶ ፡ ብልኅ ፡ – ወንድሜ ፡ ፈላስፋ ፡ ሆይ ፡ ሰሎሞን ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ የለም ፡ ብሏል ፡ ስለ ፡ ምን ፡ አንተ ፡ እንዳዲስ ፡ ነገር ፡ ተገርመኽ ፡ ትናገራለኽ ። ከቃየል ፡ አንሥቶ ፡ እስከ ፡ ኖኅ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ የአቤልና ፡ የቃየል ፡ ልጆች ፡ ርስ ፡ በርሳቸው ፡ በመዋጋት ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ኀጢአት ፡ በመሥራታቸው ፡ ይልቁንም ፡ ኀጢአትንና ፡ መሣሪያን ፡ እያራቀቁ ፡ እያጣሩ ፡ ስለ ፡ ሄዱ ፡ ከጥቂት ፡ ሰዎች ፡ በስተቀር ፡ በንፍር ፡ ውሃ ፡ አጠፋቸው ። ቸሩ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ትዕግሥት ፡ ስላሳጡት ፡ ሰውን ፡ በመፍጠሬ ፡ አዘንኩ ፡ አለ ። የአዳም ፡ ልጅ ፡ በወንድሙ ፡ ላይ ፡ የሚበላ ፡ እንጀራ ፡ እንኳ ፡ ሳይቀር ፡ የወንድሙ ፡ መግደያ ፡ መሣሪያ ፡ አድርጎታል ። ስለዚህ ፡ ሰው ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ መሆኑ ፡ ከጥንት ፡ ዠምሮ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ አይደለም ።

አቶ ፡ ብልኅ ፤–ክርክርን ፡ እንተውና ፡ እስቲ ፡ አቶ ፡ ማስተዋልን ፡ አንዲት ፡ ነገር ፡ ልጠይቀው ፣ እባክኽ ፡ ወንድሜ ፡ ማስተዋል ፡ ሆይ የሰው ፡ ልጆች ፡ ሰላምን ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያገኙ ፡ ይመስልኻል ።

አቶ ፡ ማስተዋል ፤–በዓለም ፡ ላይ ፡ ሰላም ፡ አይገኝም ፡ ከፊተኛው ፡ የኋለኛው ፡ የከፋ ፡ ይሆናል ፡ እንደ ፡ ተባለው ፤ የቃየል ፡ ፍሬዎች ፡ ካለፉት ፡ ዘመኖች ፡ ይልቅ ፡ የመረሩ ፡ የጐመዘዙ ፡ ሆነዋል ፤ የዓለም ፡ ሰላም ፡ በብዙ ፡ ገንዘብ ፡ የሚገዛና ፡ በፋብሪካ ፡ የሚሠራ ፡ አይደለም ። በውነት ፡ ሰላምን ፡ ለማግኘት ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ ተለያይተው ፡ ከሁለት ፡ ከተሞች ፡ ላይ ፡ የሚኖሩትን ፡ የአቤልንና ፡ የቃየልን ፡ ልጆች ፡ ማስታረቅ ፡ ያስፈልጋል ። ይህ ፡ ካልሆነ ፡ ዘወትር ፡ ዓለምን ፡ የሚያቃጥል የጸብ ፡ ክብሪት ፡ የሚጫረው ፡ የደምም ፡ ምንጭ ፡ የሚፈልቀው ፡ ከነሱ ፡ ውስጥ ፡ ነው ፤ ስለዚህ ፡ ወንድሜ ፡ ፈላስፋ ፡ ምን ፡ ታስባለኽ ።

አቶ ፡ ፈላስፋ ፤–ክቡር ፡ ወንድሜ ፡ የኔም ፡ አሳብ ፡ እንዳንተው ፡ ነው ፤ እነዚህ ፡ በሁለት ፡ ከተማ ፡ ተከፍለው ፡ የሚኖሩ ፡ የአቤልና ፡ የቃየል ፡ ልጆች ፡

በኑሮም ፡ በሥራም ፡ በመንፈስም ፡ ብዙ ፡ ያልተመዛዘነ ፡ ልዩነት ፡ ስላለባቸው ፡ ሁለቱን ፡ ለማስታረቅ ፡ በጣም ፡ ችግር ፡ ነው ።

አቶ ፡ ማስተዋል ፤-ከሁለቱም ፡ ከተማ ፡ ውስጥ ፡ የሚያስታርቁ ፡ ሽማግሎች ፡ የሉምን ፤ አንተስ ፡ ወንድሜ ፡ ፈላስፋ ፡ የሚያስታርቅ ፡ ሽማግሌ ፡ አትፈልግምን ።

አቶ ፡ ፈላስፋ ፤-የተወደድኽ ፡ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ አስታራቂ ፤ ጨዋ ፡ ሽማግሌ ፡ መቼ ፡ ጠፋ ፤ ከዚህ ፡ ቀደም ፡ የአቤል ፡ ከተማ ፡ አስተዳዳሪ ፡ መድኃኒታችን ፡ የሁለቱን ፡ ከተማ ፡ ነዋሪዎች ፡ ሊያስታርቅ ፡ መጥቶ ፡ የደም ፡ ወዝ ፡ እስኪወዛ ፡ ድረስ ፡ ደከመ ፤ ስለነሱም ፡ ሲል ፡ የደማውን ፡ እጁን ፡ እያሳየ ፡ ሰላም ፡ ለናንተ ፡ ይሁን ፡ ቢላቸው ፡ የቃየል ፡ ልጆች ፡ ዓለ ምን ፡ በመዛረፍና ፡ በመቃማት ፡ በጥቅም ፡ ውካታ ፡ ጕሯቸው ፡ ተደፍኖ ፡ ምንም ፡ ለመስማት ፡ አልቻሉም ። ከዚህም ፡ አስቀድሞ ፡ ከ፬፻፲፫ ፡ ዓ ፡ ም ፡ በፊት ፡ የኔ ፡ ቀድም ፡ አያት ፡ ዲዮጋንስ ፡ የሚባል ፡ ፈላስፋ ፡ ከቃየል ፡ ከተማ ፡ በቀን ፡ መብራት ፡ ይዞ ፡ ሁለቱን ፡ የከተማ ፡ ነዋሪ ዎች ፡ የሚያስታርቅ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ ቢፈልግ ፡ አጣ ፤ ስለዚህ ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ ሰላም ፡ ለማድረግ ፡ የማይቻል ፡ ነገር ፡ ነው ።

አቶ ፡ ዐወቀ ፤-እንግዴህ ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ ሰላም ፡ የማይገኝ ፡ ከሆነ ፡ ጎሊናዊ ፡ ሰው ፡ ምግባሩና ፡ ሃይማኖቱ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ማዕበል ፡ እንዳ ይናወጡ ፡ በምን ፡ ላይ ፡ መደገፍ ፡ ይገባዋል ፤ እባክኽ ፡ ወንድሜ ፡ ምከረኝ ።

አቶ ፡ ፈላስፋ ፤-ወንድሜ ፡ ምክሬን ፡ ሰምተኽ ፡ የምታደርገው ፡ ከሆነ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ። በዚች ። በክፉ ፡ ጊዜ ፡ በምትኖርበት ፡ ዘመን ፡ ሁሉ ፡ ሃይማኖትንና ፡ እውነትን ፡ ተመርኰዝ ፤ ለሰው ፡ ያለው ፡ ትዳሩ ፡ ሁሉ ፡ ጠፍቶ ፡ ሃይማኖቱና ፡ እውነቱ ፡ ቢቀሩለት ፡ ቶሎ ፡ ብሎ ፡ ከወደቀበት ፡ ይነሣል ። ነገር ፡ ግን ፡ ይህነን ፡ ስልኽ ፡ የሚሰማኽ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ዐውቀዋለሁ ፤ ሃይማኖትና ፡ እውነት ፡ የሰውን ፡ ክፉ ፡ ፈቃድ ፡ ለመፈጸም ፡ ደስም ፡ ለማሰኘት ፡ ለስላሳና ፡ ልዝብ ፡ ቀልጣፋና ፡ ሥልጡን ፡ ባለመሆናቸው ፡ ከዓለም ፡ የለዩኽ ፡ ይመስልኽ ፡ ይሆናል ። ሐሰት ፡ ግን ፡ ለስላሳ ፤ ሥልጡን ፤ ፈጣን ፤ ንቅ ፡ ለሁሉም ፡ ተስፋ ፡ የምትሰጥ ፡ ከጊዜው ፡ ነፋስ ፡ ጋራ ፡ የምትሮጥ ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ ቶሎ ፡ ሲቀናት ፡ በማየትኽ ፡ አንተ ፡ በሃይማኖትኽና ፡ በውነትኽ ፡ ዘገምተኛነት ፡ ታዝን ፡

ይሆናል ፤ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ አታውቅምን ፡ ሃይማኖትና ፡ እውነት ፡ ከጊ ዜው ፡ ነፋስ ፡ ጋራ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ስለሚጋፉ ፡ አይፈጥኑም ። ስለዚህ ፡ ትዳርኽና፡ ኑሮኽ፤ ክብርኽ፡በመጉደሉ፡ ከዚህ፡ ዓለም፡ ውስጥ፡ወጥተኽ፡ የተጣልክ፡ መስሎኽ፡አትጨነቅ፡አስተዋይም፡ ሁን።ስለ፡ ሃይማኖትኽና ፡ ስለ ፡ እውነትኽ ፡ ዘገምተኛነት ፡ በድንገት ፡ ዘለኽ ፡ ከኽኽደትና ፡ ራስን ፡ ብቻ ፡ ከመውደድ ፡ ከቅሌት ፡ ጉድጓድ ፡ እንዳትወድቅ። እውነትና ፡ ሃይ ማኖት፡ ዝግ፡ ብለው፡ ከፍ፡ ያለውን፡ ድል፡ ያገኛሉ፡ እንጂ፡ በዚህ፡ዓለም፡ ቶሎ ፡ ብሎ፡ አይቀናቸውም።ሐሰት ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ቶሎ ፡ ቢቀናት፡ደስ ታዋ ፡ ከጠመንዣ ፡ ተኵስ ፡ የፈጠነና ፡ ቶሎ ፡ ብሎ፡የሚጠፋ፡መሆኑን ፡ ዕወቅ ፡ የሐሰት ፡ ፍሬዎች ፡ ቅሌትና ፡ ጸጸት ፡ ናቸው ።

ዓለም ፡ ከባድ ፡ ሸክም ፡ ሆይ፡ እስከ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ከሰው፡ልጆች፡ ትከሻ ፡ ላይ ፡ ትወርጃለሽ ፡ ሌቦችና ፡ ቀማኞች፡ የቃየል ፡ ልጆች ፡የሚከ ፈሉሽ፡ ዕጣ ፡ ፋንታቸው፡ ነሽ ፡ ኀሊናውያን፡ ለሆኑም፡ ለአቤል፡ልጆች ፡ ከባድ ፡ ሸክም ፡ ነሽ።ንጉሥ፡ ዳዊት ፡ ባንቺ ፡ ሸክም፡ ክብደት፡ ተጨንቆ፡ እንደዚህ ፡ ብሎ ፡ ጮኽ ፡ ተናገረ ። እንደ ፡ ከባድ ፡ ሸክም ፡ ከበደኝ፡ከስ ንፍናዬም ፡ የተነሣ ፡ ቍስሌ ፡ መገለ ። በሰበስሁም ፡ ጐበጥሁ ፡ እጅ ግም ፡ ተጨነቅሁ ። ሁልጊዜም ፡ አዝኜ ፡ እመላለሳለሁ ።

ዓለም ፡ ሆይ።በሰው ፡ ልጆች ፡ እብሪትና ራስን ፡ መውደድ፡ኀጢ አትና፡ ክፋት፡ ምክንያት፡ ከእግዚአብሔር፡ እጅ፡ ወድቀሽ ፡ ልትፈነጂና ፡ ልትቃጠዪ፡ የቀረበ ፡ ይመስላል፡ ብሎ፡ አቶ፡ ፈላስፋ፡ከተቀመጠ፡በኋላ፡ ሁሉም ፡በትካዜ፡ እንደ፡ ሰመመን፡ ያለ፡ እንቅልፍ፡ ይወድቅባቸዋል፡ከሰ ማይም፡ እንደዚህ፡ የምትል፡ አንዲት፡ ድምፅ ፡ በዜማ፡ ይሰማሉ፤ አንተ ፡ እግዚኦ ፡ አቅደምከ ፡ ሣርሮታ ፡ ለምድር ፤ ወግብረ ፡ እደዊከ፡ እማንቱ ፡ ሰማያት ፤ እማንቱሰ፡ ይትሀጐላ፡ ወአንተሰ፡ ትሄሉ።ወኵሉ ፡ ከመ፡ልብስ፡ ይበሊ ፤ ወከመ ፡ ሞጣሕት ፡ ትዌልጦሙ፡ ወይትዌለጡ ፡ አንተሰ ፡አንተ፡ ከመ ፤ ወዓመቲከኒ ፡ ዘኢየሐልቅ ።

አቶ ፡ ፈላስፋ ፡—ብንን ፡ ብሎ ፡ ወንድሞቼ ፡ ምንም ፡ ድምፅ ፡ አልሰማችሁምን ።

አቶ ብልጦ ፡-እኔ ፡ ምንም ፡ አልሰማሁ ።

አቶ፡ማስተዋል፤-እኔ፡ በሚያሳዝን፡ ዜማ፡ አንዲት፡ድምፅ፡ሰምቻለሁ።

አቶ፡ ፈላስፋ ፡—እኔ፡ በግዕዝ፡ ቋንቋ፡ የሰማሁት፡የሚያሳዝን፡ዜማ ፡ ነው ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ባማርኛ ፡ ስተረጐመው ፡ አንተ ፡ ከጥንት ፡ ምድርን ፡ መሠረትኽ ፡ ሰማዮችም ፡ የጅኽ ፡ ሥራ ፡ ናቸው ። ርሳቸው ፡ ይጠፋሉ ፤ አንተ ፡ ግን፡ ትቆማለኽ፡ ሁሉም ፡ እንደ ፡ ልብስ ፡ ያረጃሉ ። እንደ፡መጐናጸፊያም ፡ ትለውጣቸዋለህ ፡ ይለወጣሉ ። አንተ ፡ ግን ፡ እንዲሁ ፡ አንተ ፡ ነኽ ፡ ዓመታትኽም ፡ ከቶ ፡ አያልቁም ፡ የሚል ፡ ነው ።

አቶ ፡ ማስተዋል—እኔም፡የሰማሁት፡እንደዚሁ ፡ ያለ ፡ ቃል ፡ ነው ፡ ዓለም ፡ እንዳሮጌ ፡ ጨርቅ ፡ ብዙ ፡ ተባይ ፡ ስላፈራች ፡በእሳት ፡ ልትቃጠል፡ ይመስላልና፡ እኛ፡ እንግዴህ፡ በዚህ ፡ ዓለም፡ መኖር ፡ አይገባንም፡ ተነሡ፡ እንሂድ፡ ካለ ፡ በኋላ፡ መጽሐፋቸውን፡ አንሥተው ፡ በኀዘንና ፡ በትካዜ ፡ ቀስ ፡ ብለው ፡ ይሄዳሉ ።

———==———

# መ ግ ቢ ያ ።

ዓለም ፡ ወረተኛ ፡ ከተባለው ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ ውስጥ ፡ የሚታዩትን ፣ ሥዕሎች ፡ አቶ ፡ ሺመልስ ፡ የሚባል ፡ ሠዓሊ ፡ ስለ ፡ ሣለልኝ ፡ ከልብ ፡ የማይረሳ ፡ ውለታውን ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ ላስታውሰው ፡ ይገባኛል ።

ደግሞ ፡ በ፲፱፻፳፰ ፡ ዓ. ም. ሚያዝያ ፡ ፳፬ ፡ ቀን ፡ ታሪካዊ ፡ የሆነውን ፡ ስደትና ፡ የፖለቲካ ፡ ጦርነት ፡ ለመቀጠል ፡ ግርማዊ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ ነገሥታት ፡ ማኅበር ፡ ሲሄዱ ፡ እኔም ፡ ግርማዊነታቸውን ፡ ለመከተልና ፡ በሥራ ፡ ለመርዳት ፡ ከውጋዴ ፡ ጦር ፡ ሜዳ ፡ ተመልሼ ፡ ጅቡቲ ፡ በደረስሁ ፡ ጊዜ ፡ ዋና ፡ ጸሐፊዬ ፡ ቀኛዝማች ፡ መንግሥቱ ፡ ተከትለኝ ፡ ሄዶ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ ከጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ በመምጣታችን ፡ ይልቁንም ፡ ሥንቃችን ፡ በቦምብና ፡ በመርዝ ፡ ስለ ፡ ተቃጠለ ፡ በችግር ፡ ላይ ፡ ነበርንና ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ለመሰደድ ፡ ስለማይችል ፡ ወዳገሩ ፡ እንዲመለስ ፡ አሰናብቼው ፡ ነበር ፡ ስንሰነባበትም ፡ የጣልኩበት ፡ አደራዎች ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ የተጻፉት ፡ ናቸው ።

፩ኛ ፤ ያገርኽን ፡ ነፃነት ፡ አትርሳ ።

፪ኛ ፤ አቃቂ ፡ ሳለሁ ፡ የጻፍኩት ፡ ዓለም ፡ ወረተኛ ፡ የተባለው ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ በጽሕፈት ፡ ቤቴ ፡ ውስጥ ፣ ከነሥዕሉ ፡ ይገኛልና ፤ ምናልባት ፡ ቢያጋጥምኽ ፡ አውጥተኽ ፡ ካንተ ፡ ዘንድ ፡ አስቀምጥልኝ ፡ የሚል ፡ ነው ።

ቀኛዝማች ፡ መንግሥቱ ፡ ሮባም ፡ ከጅቡቲ ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ እንደ ፡ ገባ ፡ ወዲያው ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ ቢሄድ ፡ ቤቴ ፡ ተወሮ ፡ ዕቃዬ ፡ ተበዝብዞ ፡ ጽሕፈት ፡ ቤቴ ፡ ተሰብሮ ፡ ማስረጃዬ ፡ ሁሉ ፡ በየቀጋው ፡ ሥር ፡ ወድቆ ፡ ያ ፡ የዘመድ ፡ ጨዋታና ፡ ያሽከሮች ፡ ውካታ ፡ የለመደ ፡ ቤት ፡ የኀዘን ፡ ጨለማ ፡ ወርሶት ፡ የሞት ፡ ጥላና ፡ የሚያሳዝን ፡ ፀጥታ ፡ ነግሦበት ፡ በመድረሱ ፡ እያዘነ ፡ ከበራፍ ፡ ብቻውን ፡ ቆሞ ፡ ሲመለከት ፡ አደራ ፡ ያልኩትን ፡ መጽሐፍ ፡ ካንዲት ፡ አጋም ፡ ሥር ፡ ከብዙ ፡

ጐድፍ ፡ ጋራ ፡ ወድቆ ፡ አግኝቶ ፡ ወስዶ ፡ ካገር ፡ ቤት ፡ ቀብሮ ፡ ሚያዝያ ፡ ፳፯ ፡ ቀን ፡ ፲፱፻፴፫ ፡ ዓ. ም. የግርማዊነታቸውን ፡ በድል፡ አድራጊነት ፡ መምጣት ፡ ለሚወዱት ፡ ሕዝባቸው ፡ የምሥራች ፡ ለመንገር ፡ ከደብረ ፡ ማርቆስ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ባይሮፕላን ፡ በገባሁ፡ ጊዜ ፡ አደራ ፡ ያልኩትን ፡ መጽሐፍ ፡ አምጥቶ ፡ ሰጠኝ ።

እንባቢ ፡ ሆይ ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ የተጻፉት ፡ ምግ ባሮች ፡ «ሞራል» ፡ ለጊዜው ፡ ከፍ ፡ ያሉ ፡ ጽሑፎች ፡ ሆነው ፡ ባይታዩ ፡ እንኳ ፡ በጣም ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ተአምራት፡ ስለ ፡ ተገለጸበት ፡ ላሳትመው ፡ ፈቀድሁ ። መድኀኒታችን ፡ የሰናፍጭ፡ ቅንጣት ፡ ያኽል ፡ ሃይማኖት ፡ ቢኖራችሁ ፡ ይህነን ፡ ተራራ ፡ ተነ ሥተህ ፡ ሒድ ፡ ማለት ፡ ትችላላችሁ ፡ ብሎ ፡ በሃይማኖት ፡ ትልቅ ፡ ኀይል ፡ እንደሚሠራ ፡ አስታወቀን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እኛ ፡ የሰናፍጭ ፡ ቅንጣት ፡ የሚያኽል ፡ ሃይማኖት ፡ እንኳ ፡ ሳይኖረን ፡ የሚገባንንም፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ያላደረግን ፡ ባሮች ፡ የለመነውን ፡ ያለሃይማኖትና ፡ ያለሥራ ፡ ስላደረገልን ፡ ውለታውን ፡ ምን ፡ መክፈል ፡ ይገባናል ።

ባጭር ፡ ቃል ፡ ኀሊናዊ ፡ መልስ ፤ ለኛ ፡ ቢደረግልን ፡ የምነወ ደውን ፡ እንደዚሁ ፡ ለወንድሞቻችን ፡ እናድርግ ። ኦሪትም ፡ ነቢያ ትም ፡ ሐዲሳትም ፡ የዓለም ፡ ፍልስናም ፡ ሁሉ ፡ በዚች ፡ ቃል ፡ ውስጥ ፡ ይገኛል ።

እንባቢ ፡ ሆይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ላንድ ፡ ሰው ፡ ወይም ፡ ላንድ፡ አገር ፡ ትልቅ ፡ ተአምራት ፡ ሲሠራ ፡ የተሠራለት ፡ ወገን ፡ ባሸዋ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ጽሑፍ ፡ ከልቡ ፡ ወዲያው ፡ ሲጠርገውና፡ ሲያጠፋው ፡ ዝም ፡ አይልም ። ስለዚህ ፡ በማቴዎስ ፡ ም. ፲፩ ፡ ቍ፡ ፳ ። ም. ፲፪ ፡ ቍ ፡ ፵፪ ፡ የተጻፉትን ፡ መሥመሮች ፡ ዘወትር ፡ ማሰብ ፡ ይገባናል ፡ የማይረሳ ፡ ነገር ፡ ነውና ፤ እንርሳ ።



# መ ቅ ድ ም ።

ባ፲፱፻፳፫ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ከቢትወደድ ፡ መኰንን ፡ እንዳልካቸው ፡ የተጻፈ ፡ ዓለም ፡ ወረተኛ ፡ ከሚባል ፡ ልብ፡ ወለድ፡ ታሪክ ፡ ውስጥ፡ ባጭሩ ፡ ለቲያትር፡ ጨዋታ ፡ እንደሚመች፡ ባ፲፱፻፵፡ ዓ.ም- ተገለበጠ ።

ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ ወይም ፡ ተረት ፡ ሰው ፡ በወንድሙ ፡ ላይ ፡ ክፉ ፡ የጭካኔ ፡ ሥራ ፡ እንዳይሠራ ፡ በጨዋታ ፡ አስመ ስሎ ፡ ነውሩን ፡ በመስተዋት ፡ የሚያሳይ ፡ ነው ። ይህ ፡ ዓለም ፡ ወረተኛ ፡ የተባለ ፡ መጽሐፍ ፡ ፯ ፡ የምግባር ፡ ሥራዎች ፡ ያሉበት፡ (ትራጀዲ ፡ ) ማለት ፡ የሚያሳዝን ፡ ቲያትር ፡ የሚገልጽ ፡ ጽሑፍ፡ ነው ። እንሆ ፡ ፯ቱ ፡ ምግባሮች ፡ ከዚህ ፡ በታች ፡ ተዘርዝረው ፡ ይገኛሉ ።

፩ኛ ፡ እናትና ፡ አባት ፡ ለልጆቻቸው ፡ እንደ ፡ ምን ፡ እንደ ሚጨነቁ ፤ ደግሞ ፡ የሌሎችን ፡ ልጆች ፡ አሽከር፡አድርገው ፡ ሰዎች፡ እንደሚያስጨንቋቸው ።

፪ኛ ፤ ወንበዴዎች ፡ ለራሳቸው ፡ ጥቅም ፡ ሲሉ ፡ የሰውን ፡ ልጆች ፡ ከሕግ ፡ ውጭ ፡ በሆነ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ሥቃይ ፡ ሲያሳዩዋ ቸው ።

፫ኛ ፤ የተማረ፡ ሰው ፡ ለሰው፡ሲል ፡ ታሪክ፡ ባለው፡ሞት፡ ሲሞት።

፬ኛ ፡ ያልተማረ ፡ አረመኔ ፡ ሚስት ፡ ለማግባት ፡ የወንድሙን፡ ደም ፡ ማጫ ፡ ሲያቀርብ ።

፭ኛ ፤ መከራ ፡ የጽድቅ ፡ ማጣሪያ ፡ መሆኑና ፡ የሰው ፡ ጽኑ ፡ ፈቃድና ፡ ሃይማኖት ፡ ካሰቡት ፡ ቦታ ፡ እንዲያደርስ ።

፮ኛ ፤ ዓለም ፡ ወረተኛ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለች ፡ አታላይ ፡ እንደ ፡ ሆነች ።

፯ኛ ፡ ልጆችን ፡ ለማስፈራራት ፡ ሲባል ፡ የምናስተምራቸው ፡ ክፉዎች ፡ ተረቶች ፡ ካደጉ ፡ በኋላ ፡ የሐሳብ ፡ በሽታና ፡ በመምሰል፡ ክፉ ፡ ፍርሃት ፡ እንደሚወድቅባቸው ፡ ይገልጻል ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ ማንኛውንም ፡ መጽሐፍ ፡ ቢሆን ፡ በመጠ ንቀቅ ፡ አንብብ ፡ እንጂ ፡ አትናቅ ። በጥንቃቄ፡ ከተመለከትኽ ፡ በኋላ፡ ለመንቀፍም ፡ ለማመስገንም ፡ ትችላለህ ፤ በብራና ፡ ላይ ፡ ተጽፈው ፡ የሚገኙ ፡ የሰዎች ፡ ሐሳቦች ፡ ሁሉ ፡ የሰውን ፡ ልጆች ፡ ኀሊና ፡ ከፍ ፡ ለማድረግ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የተሰጡ ፡ የነፍስ ፡ ምግቦች ፡ መሆናቸውን ፡ ዕወቅ ። ሰው ፡ በመ

ብል ፡ ብቻ፡ የመንፈስን ፡ ብርታት፡ አያገኝም ፡ መጽሐፍ፡ በማንበብ ግን፡ ነፍስ ፡ መንፈሳዊ ፡ ምግብ ፡ ስለምትመገብ ፡ የመንፈስም ፡ የሥጋም ፡



የማስተዋል ፡ መነጽር ።

ብርታት ፡ ይገኛል። መጻሕፍትን ፡ በምታነብ፡ ጊዜ ፡ የማስተዋልን ፡ መነጽር ፡ በዓይንኽ ፡ ላይ ፡ አድርግ። ማንበብ ፡ ማየት ፡ ብቻ ፡ ስለሆነ ፡ ፍሬ፡ የለውም ፡ ማስተዋል ፡ ግን ፡ የውስጡን ፡ ባሕርይ ፡ መርምሮ ፡ የሚመለከት ፡ ስለሆነ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ጥቅምን ፡ ይሰጣል ።

ለምሳሌ፤ ውሃን ፡ በዓይን ፡ ብቻ ፡ ሲያዩት ፡ እንደ ፡ መስተዋት ፡ ጠርቶ ፡ ይታያል፤ ነገር ፡ ግን ፡ ኀይል ፡ ባለው ፡ መነጽር ፡ ሲመረምሩት ፡ ብዙ ፡ ተሐዋስያንና ፡ ሚክሮፖች ፡ (ረቂቃን ፡ ዕፄያት) ፡ የመሉበት ፡ ለመጠጣትም ፡ የሚያጸይፍና ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ በሽታ፡ የሚያመጣ፡ ሆኖ ፡ ይገኛል ። እንደዚህም ፡ ሁሉ ፡ የማስተዋልን ፡ መነጽር ፡ ዓይን ፡ ላይ ፡ አድርጎ ፡ መጽሐፍን ፡ ሲመለከቱት ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ሀብትና ፡

የሰው ፡ ገናንነት ፡ ወርቅ ፡ አልማዝ ፡ ብርና ፡ ዕንቍም ፡ ዐፈር ፡ ከሰል ድንጋይ ፡ መሆናቸውን ፡ ገልጾ ፡ ያሳያል ።

ስለዚህ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ "እኔ ፡ ሰው ፡ አይደለሁም ፡ ትል ፡ ነኝ ፡ አንሰ ፡ ዕፄ ፡ ወአከ ፡ ሰብእ„ ፡ አለ ። እነሆ ፡ በሩቅ ፡ የሚያስተውል ፡ ልበ ፡ አምላክ ፡ የሆነ ፡ ንጉሥ ፡ የማስተዋልን ፡ መነጽር ፡ ዓይኑ ፡ ላይ ፡ አድርጎ ፡ ራሱን ፡ በራሱ ፡ በመመልከቱ ፡ ትል ፡ መሆኑን ፡ ተረዳው ። ቢሆንም ፡ ሰው ፡ በእግዚአብሔር ፡ መልክ ፡ የተፈጠረ ፡ ክፍ ፡ ያለ ፡ መሆኑን ፡ ለማስረዳት ፡ «ሰው ፡ የከበረ ፡ መሆኑን ፡ ባለማወቁ ፡ ልብ ፡ የሌላቸውን ፡ እንስሶች ፡ መሰለ ፤ ስብእሰ ፡ እንዘ ፡ ክቡር ፡ ውእቱ ፡ ኢያእመረ ፡ ወኮነ ፡ ከመ ፡ እንስሳ ፡ ዘአልቦ ፡ ልብ ፡ ወተመሰሎሙ ፡» ፡ ይላል ። እንግዲህ ፡ ይህ ነን ፡ ጽሑፍ ፡ ስንመለከት ፡ የሚሰጠን ፡ ሐሳብ ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ መሬት ፡ መሬት ፡ ብቻ ፡ በማየታችን ፡ እንስሶችን ፡ መሰልን ፡ እንጂ ፤ ዓይናችንን ፡ ወደሰማይ ፡ አቅንተን ፡ የሰማይ ፡ አባታችንን ፡ ብንመለከት ፡ ከፍ ጥረት ፡ ሁሉ ፡ የበለጥን ፤ እግዚአብሔርን ፡ ለማየትና ፡ የዕውቀቱንም ፡ ጮራ ፡ ለመቀበል ፡ እንደምንችል ፡ መጽሐፍ ፡ ገልጦ ፡ ያሳየናል ።

ነገር ፡ ግን ፡ ዓይኑ ፡ የታመመ ፡ ሰው ፡ ፀሐይን ፡ ትኵር ፡ ብሎ ፡ ለማየት ፡ እንደማይችል ፡ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ በኀጢአት ፡ የታመመ ፡ የሰው ፡ ዐይን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የዕውቀት ፡ ብርሃን ፡ ለማየት ፡ አይችልም ፡ ስለዚህ ፡ ታማሚ ፡ በሆነ ፡ ዓይናችን ፡ በማሰተዋል ፡ መነጽር ፡ አጋዥነት የእግዚአብሔርን ፡ የዕውቀት ፡ ብርሃን ፡ እንድናይ ፡ መጻሕፍትን ፡ በጥልቅ ፡ ባለመሰልቸት ፡ እንድንመለከት ፡ ያስፈልጋል ። ብዙ ፡ የሚያነብ ፡ ዐዋቂ ፡ ይሆናል ፡ ተብሏል ።

---

# ዓለም ፡ ወረተኛ ።

## ቡሔ ፡ የልጆች ፡ በዓል ።

የወይዘሮ ፡ ኑሪቱ ፡ ልጆች ። ቡሔ ፡ በሉ ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ። አባቴ ፡ ቤት ፡ አለኝ ፡ ለከት ፤ እናቴ ፡ ቤት ፤ አለኝ ፡ ለከት ፤ አጎቴ ፡ ቤት ፡ አለኝ ፡ ለከት ፤ አክሥቴ ፡ ቤት ፡ አለኝ ፡ ለከት ። ቡሔ ፡ በሉ ፤ ቡሔ ፤ በሉ ፤ ልጆች ሁሉ ። ወይዘሮ ፡ ኑሪቱ ፦ ኑ ፡ ልጆች ፡ ኅብስቱን ፡ ተካፈሉ ። የወይዘሮ ፤ ኑሪቱ ፡ ወንድም ፡ ከውጭ ፡ መጥተው ፡ ኑ ፡ ልጆቼ ፡ ያመጣሁላችሁን ፡ ኅብስት ፡ ተካፈሉ ፤ አጎቴ ፡ ቤት ፡ አለኝ ፡ ለከት ፡ እያሉ ፡ እየዘፈኑ ፡ ሳሙት ፡

አቶ ፡ ዮሴፍ ፤ — እንቺ ፡ እኅቴ ፡ ድጌን ፡ ስቀዩልኝ ፡ በጨለማ ፡ በፈረስ ፡ ስንገለታ ፡ ስለ ፡ መጣሁ ፡ በጣም ፡ ደክሞኛል ። ወይዘሮ ፡ ኑሪቱ ፤ — እንግዲ ያውስ ፡ እራታችንን ፡ በልተን ፡ ዘቶሎ ፡ ጋደም ፡ ብትል ፡ ይሻላል ። አቶ ፡ ዮሴፍ ፤ — እግዚአብሔር ፡ ይስጥልኝ ፡ እኅቴ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ፈረሴ ፡ ውሃ ፡ አልጠጣምና ፡ እወንዝ ፡ ወርጄ ፡ ካጠጣሁ ፡ በኋላ ፡ እተኛለሁ ። ወይዘሮ ኑሪቱ ፤ — አይሆንም ፡ ዝናቡም ፡ ይዘንባል ፤ ጨለማውም ፡ ውድቅት ፡ ነው ፡ አትሄድም ፤ የኔ ፡ ባሪያ ፡ አለችና ፡ ውሃ ፡ በባልዲ ፡ ቀድታ ፡ ታመጣና ፡ ታጠጣልኻለች ።

ያች ፤ የመካን ፡ ልጅ ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ከናት ፡ ካባቷ ፡ ቤት ፡ የቡሔ ፡ ለት ፡ በዓል ፡ ይደረግላት ፡ የነበረ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ እንኳ ፡ ሥራ ፡ ፈታ ፡ እንድት ጫወት ነፃነት ፡ አጥታ ፡ ስታለቅስ ፡ ወይዘሮ ፡ ኑሪቱ ፤ — ያይኔ ፡ አበባ ነዪ ። ያይኔ ፡ አበባ ፤ እመት ። ወይዘሮ ፡ ኑሪቱ ፤ - እባክሽ ፡ ስለ ፡ ምንድነው ፡ የምታለቅሽው ፡ ሥራሽን ፡ ትተሽ ፡ ከልጆች ፡ ጋራ ፡ አልተጫወትኩ ፡ ብለሽ ፡ ነውን ፡ ደፋር ፡ ውላጅ ፡ ይልቁንስ ፡ ያንን ፡ ትልቁን ፡ ባልዲ ፡ ይዘሽ ፡ ሂደሽ ፡ በቶሎ ፡ ውሃ ፡ አምጥተሽ ፡ ለወንድሜ ፡ ፈረስ ፡ እንድታ ጠጪ ። ያይኔ ፡ አበባ ፤ — እሺ ፡ እመቤቴ ፡ አመጣለሁ ።

ችግረኛዪቱ ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ስንኳን ፡ ውሃ ፡ መልቶበት ፡ ብቻውን ፡ ካቅሟ ፡ በላይ ፡ የሆነውን ፡ ባልዲ ፡ ተሸክማ ፡ በውድቅት ፡ ጨለማ ፡ ትሮጥ ዠመር ፤ ምንጩ ፡ ያለበት ፡ ከቤት ፡ ርቀቱ ፡ ፩ ፡ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ይሆናል ። በሌሊቱ ፡ ግርማ ፡ በዥቡና ፡ በቀበሮው ፡ ድምጥ ፡ በቅምጥል ፡ ያደገች ፡ ያይኔ አበባ ፡ በፍርሀት ፡ ተጨንቃ ፡ በዚያ ፡ ቍልቍለት ፡ ስትወድቅና ፡ ስትነሣ ከወንዙ ፡ ደረሰች ። ውሃውን ፡ ቀድታ ፡ ለማንሣት ፡ ብትሞክር ፡ ባልዲው ፡

ከውሃው ፡ ጋራ ፡ ከሷ ፡ ሚዛን ፡ የሚብልጥ፡ ስለ ፡ ሆነ፡ ያይኔ ፡ አበባ፡ እን ግዴህ ፡ ምን ፡ ላድርግ ፡ ውሃውን ፡ ሳሊዝ ፡ ብሄድ ፡ እመቤቴ ፡ ይገድሉ ኛል ፤ ከዚህም ፡ ዝም ፡ ብዬ ፡ እንዳላድር፡ አውሬ፡ እፈራለሁ ፡ ምን፡ ይሻ ለኛል ፡ ብላ ፡ ውሃውን ፡ ስትጐትት ፡ አንድ ፡ ወፍ ፡ ከደኑ ፡ ውስጥ፡ ቱር፡ ብላ፡ ብትነሣ፡ ከደን፡ ውስጥ፡ አውሬ፡ መጥቶ ፡ የያዛት ፡ መስሏት፡ ጮኻ፡ ውሃውን ፡ ብትለቀው ፡ ፈሰሰ ። ያን ፡ ጊዜ ፡ ያይኔ፡ አበባ፡ በዜማ ፡ እንደ ዚህ ፡ እያለች ፡ ታለቅስ ፡ ጀመር ።

ውሃዬን ፡ ቀድቼ ፡ ለመሄድ ፡ ስጥር ፡
አውሬ ፡ እስደንግጦኝ ፡ ወደቅሁኝ ከዱር ።
ውሃውም ፡ ፈሰሰ ፤ ልብሴም ፡ በሰበሰ ።
በብርድ ፡ ተንቀጠቀጥሁ ፡ ራስሁ ፡ እስካጥንቴ ፤
ወይ ፡ እኔ ፡ ወይ ፡ እኔ ፡ አላየሽ ፡ እናቴ ።
በውድቅት ጨለማ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ብርድ ፤
ደርሶብኝ ፡ አያውቅም ፡ የዚህ ፡ ዐይነት ፡ ጉድ ።
ወዴት ፡ እደርስ ፡ ይሆን ፡ እኔ ፡ ድኻዪቱ ፤
ከዚህም ፡ እንዳልቀር ፡ አውሬው ፡ ማስፈራቱ ።
ባዶ ፡ እጄን ፡ እንዳልሄድ ፡ ሞት ፡ ይጠብቀኛል ፤
ጨካኝዋ ፡ እመቤቴ ፡ ሥቃይ ፡ ያሳዩኛል ።
አባትና ፡ እናቴ ፡ ይህነን ፡ ቢሰሙ ፤
ልጅ ፡ ያገኙበትን ፡ (ቀን)፡ እንዴት ፡ በረገሙ ።

ወይ ፡ እኔ ፡ ወይ ፡ እኔ ፡ ወይ ፡ እኔ ፡ ወዴት ፡ ልድረስ ።

ከወንዙ፡ ራቅ፡ ብለው፡ መምሬ፡ ተክሌ፡ የሚባሉ፡ ቤት ፡ ሠርተው፡ ተቀምጠው ፡ ነበር ። ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚባል ፡ ልጃቸው ፡ የቡ ሔን፡ በዓል፡ አባቱ፡ ቤት፡ ለማክበር ፡ መጥቶ፡ ሰንብቶ ፡ ሳለ ፡ ገብረ፡ እግ ዚአብሔር ፡ ያገሩንም ፡ የውጭ፡ አገርም፡ ትምህርት፡ በጣም፡ የተማረ ፡ አስተዋይ ፡ ልጅ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፤ ከውጭ፡ ወጥቶ፡ እየተንጐራደደ ፡ የእግዚ አብሔርን ፡ ግሩም ፡ ሥራ ፡ ሲያስብ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ሲጸልይ ፡ ከወ ንዝ ፡ ያይኔ ፡ አበባ፡ በዜማ፡ ስታለቅስ ፡ ሰምቶ ፡ በጣም ፡ ተነካና፡እሱም፡

በዜማ ፡ እያንጐራጐረ ፡ ወደሷ ፡ በትሪውን ፡ ይዞ ፡ ሮጠ ። ገብረ ፡ እግ ዚአብሔር ፤ ምንድነው ፡ ይህ ፡ ነገር ።

ብዙ ፡ የጭንቅ ፡ ድምፅ ፡ በሩቅ ፡ እሰማለሁ ፤
ይህነን ፡ ለማወቅ ፡ እገሠግሣለሁ ።
ባትሪዬን ፡ ላብራና ፡ ልፈልግ ፡ በጣም ፤
ድምፅ ፡ ያለመጨነቅ ፡ እንዲህ ፡ አይጮህም ።

ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ — አንቺ ፡ የምትጮኺ ፡ ልጅ ፡ አይዞሽ ፡ ደረስኩልሽ ፡ አትጨነቂ ። ያይኔ ፡ አበባ ፡ — ባልዲዋን ፡ ከግንባሯ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ አድርጋ ፡ ወይ ፡ እኔ ፡ ዕድሉ ፡ ቢሷ ፡ ምን ፡ ወንበዴ ፡ መጣብኝ ፡ ደግሞ ፡ ወዴት ፡ ወስዶ ፡ ሊጥለኝ ፡ ይሆን ፡ ከነዚያ ፡ ወን በዴዎች ፡ ወዲያ ፡ ሰው ፡ ከውሬ ፡ የሚሻልበት ፡ እንደሌለ ፡ ተረድቼዋ ለሁ ፡ ምነው ፡ ሁለተኛ ፡ ከወንበዴዎች ፡ እጅ ፡ ከመውደቅ ፡ አውሬ ዎች ፡ ቢበሉኝ ፡ ይሻለኝ ፡ ነበር ። ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ባትሪውን ፡ አብርቶ ፡ ጥቂት ፡ ከፈለገ ፡ በኋላ ፡ ያይኔ ፡ አበባን ፡ አገኘና ፤ አንቺ ፡ ልጅ ፡ ምን ፡ ሆነሽ ፡ ነው ፡ እንደዚህ ፡ የምትጮኺ ፤ ያይኔ ፡ አበባ ፤ ጌታዬ ፡ የጮኽኩበት ፡ ምክንያት ፡ ይህ ፡ ነው ፤ አሁን ፡ ከምሽቱ ፡ የመቤቴ ፡ ወንድም ፡ መጥተው ፡ ፈረሳቸውን ፡ ለማጠጣት ፡ ጨለማ ፡ ስለ ፡ ሆነባቸው ፡ እኔን ፡ ውሃ ፡ ቅጂና ፡ አምጪ ፡ ብለው ፡ ላኩኝ ።

ይኸውልኽ ፡ አንተ ፡ እንደምታየው ፡ ስንኳን ፡ እኔ ፡ ትልቅ ፡ ሰው ፡ የማይችለው ፡ የውሃ ፡ መቅጃ ፡ ባዶውን ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ይገሮ ፡ መጣሁ ። ውሃውን ፡ ቀድቼ ፡ ለመመለስ ፡ ግን ፡ ከቅሜ ፡ በላይ ፡ ስለ ፡ ሆነብኝ ፡ ተጨነቅሁ ፤ እነሆ ፡ ውሃው ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ ፈሶ ፡ ከዝናሙ ፡ ጋር ፡ ልብሴ ፡ በስብሶ ፡ በብርድ ፡ ልሞት ፡ ነው ። እባ ክኽ ፡ ጌታዬ ፡ አንተ ፡ ወንበዴ ፡ እንደ ፡ ሆንክ ፡ ሁለተኛ ፡ ወስ ደኽ ፡ በጨካኝ ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ ከምትጥለኝ ፡ ከዚሁ ፡ ብትገድለኝ ፡ ትጸድቃለኽ ። ገብረ እግዚአብሔር ፤ — እኔ ፡ ወንበዴም ፡ አይደ ለሁ ፡ የክርስቲያን ፡ የቄስ ፡ ልጅ ፡ ነኝ ፡ ጩኸትሽን ፡ ብሰማ ፡ የመ ጣሁት ፡ አንቺን ፡ ለመርዳት ፡ ነው ፡ እንድታምኚኝ ፡ መስቀሌን ፡ አሳይሻለሁ ። ያይኔ ፡ አበባ ፡ ያባቷንና ፡ የናቷን ፡ ምልክት ፡ በማየቷ የደስታና ፡ የኀዘን ፡ ዕንባዋን ፡ አፍሳ ፡ መስቀሉን ፡ ትስም ፡ ዠመር ።

ገብረ እግዚአብሔር ፤ — እንግዴህ ፡ ምንም ፡ ላድርግልሽ ፡ በምን ፡ አኳኋን ፡ ልረዳሽ ፡ እችላለሁ ። ያይኔ ፡ አበባ ፤ —- በምንም ፡ አኳኋን ፡ የኔን ፡ ዕድል ፡ አሻሽለኸ ፡ ልትረዳኝ ፡ አትችልም ፤ ውሃውን ፡ ሳሊገዘ ፡ ተመልሼ ፡ ወደ ፡ እመቤቴ ፡ ለመግባት ፡ ትልቅ፡ መከራ ፡ አለብኝ ። ውሃውንም ፡ ተሸክመኸልኝ ፡ እንዳትሄድ ፡ እመቤቴ ማንም ፡ ሰው ፡ መከራዬን ፡ ቢያግዘኝ ። አይወዱምና ፡ የበለጠ፡ ነገር ፡ ይደርስብኛል ። እንደምታውቀው ፡ ዛሬ ፡ ቡሔ ፡ የልጆች ፡ በዓል ፡ ነበር ፤ የልጆቻቸውን ፡ ደስታ ፡ በዕንባዬ ፡ ውስጥ ፡ ከበራፍ ፡ ቆሜ ፡ መመልከትን ፡ ስንኳ ፡ እንደ ፡ ደስታ ፡ ስለ ፡ ቆጠሩብኝ ፡ ተቆጥተው ፡ ያላቅሜ ፡ ታዝዤ ፡ ይኸው ፡ ሥቃዬን ፡ አያለሁ ። ስለዚህ ፡ ልታደርግ ፡ የምትችለው ፡ እኔም ፡ ከውለታ ፡ የምቆጥርልኽ ፡ ብትገድለኝ ፡ ነውና ፡ እባክኽ ፡ ግደለኝ ፡ እኔ ፡ ራሴን ፡ እንዳልገድል ፡ የራሴ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ እሆናለሁ ።

ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፤ —እኅቴ ፡ እንግዴህ ፡ አንቺ ፡ በመከራ ፡ ስለ ፡ አበድሽ ፡ ራስሽን ፡ ልትጐጂ ፡ አትችይም ፡ መልካምና ፡ ክፉንም ፡ ሐሳብ ፡ ለማመራረጥ ፡ ተስፋ ፡ በመቍረጥሽ ምክንያት ፡ አትደፍሪም ።

እኔ ፡ ግን ፡ እንዲዚህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ካጋጠመኝ ፡ የማልዘለው ፡ ሥራዬ ፡ ነውና ፤ ይገፍሽ ፡ ለመጥፋት ፡ ቈረጥሁ ፤ እንሂድ። ያይኔ ፡ አበባ ፤—ምንም ፡ ቢሆን ፡ አይሆንልኝም ፡ አልሄድም ፤ አንተ ፡ በትገድለኝ ፡ ከዚሁ ፡ አውሬ ፡ ይበላኛል ።

ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተቈጥቶ ፡ ብድግ ፡ አድርጎ ፡ በትከሻው ፡ ተሸክሞ ፡ ወደ ፡ በረሓው ፡ ሮጠ ፤ ብዙ፡መንገድ ፡ ተሸክሟት ፡ ከተጓዘ ፡ በኋላ ፡ ወገግ ፡ ሲል ፡ ከአዳል ፡ መሬት ፡ አፋፍ፡ ደረሱ ። ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፤—እሮይ ፡ እንግዴህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ከደጋ ፡ የዳንን ፡ ይመስለኛል ። ያይኔ ፡ አበባ፤— እኔም ፡ ይመስለኛል ፤ ወንድሜ ፡ የምሥራቅ ፡ ፀሓይ ፡ ስለ ፡ ወጣች ፡ ከፊታችን ፡ ያለው ፡ አገር ፡ ወለል ፡ ብሎ ፡ ታየኝ ፤ ግን ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ ነው ። ገብረ፡እግዚአብሔር ፤- የአዳል ፡ መሬት ፡ ነው ። ያይኔ ፡ አበባ ፤ -እንግዴህ ፡ መንገዳችን ፡ በዚህ ፡ በረሓ ፡ ውስጥ ፡ ነውን ፡ ወይስ ፡ በሌላ ፡ በኩል ። ገብረ ፡ እግዚአብሔር፡— እኔም ፡ አሁን ፡ ይህንኑ ፡ ሳስብ ፡ ነበር ፤ ላይ ፡ ላዩን ፡ በደጋው ፡

ብንሄድ ፡ መልካም ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ ወይዘሮ ፡ ኑሪቱ ፡ አስጨ ኸው ፡ ያሲዙን ፡ ይሆን ፡ በማለት ፡ ያሠጋል ። በአዳል ፡–በረሓ ፡ ውስጥ ፡ ብንሄድም ፡ አዳሎች ፡ አደጋ ፡ ይጥሉብን ፡ ይመስለ ኛል ፤ አንቺ ፡ ምን ፡ ታስቢያለሽ ። ያይኔ ፡ አበባ ፤–ወንድሜ ፡ ቅድም ፡ እንደ ፡ ነገርኩኽ ፡ ከኔ ፡ ኑሮ ፡ ሞት ፡ ይሻላል ፤ ከወይዘሮ ፡ ኑሪቱ ፡ እጅ ፡ ከመግባት ፡ በአዳል ፡ መሬት ፡ ውስጥ ፡ ሄጄ ፡ መሞ ትን ፡ እመርጣለሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ ፈቃድኽ ፡ ቢሆን ፡ የምለምንኽ ፡ ከኔ ፡ ከዕድለ ፡ ክፉዋ ፡ ጋራ ፡ ሆነኽ ፤ መከራ ፡ ከመቀበል ፡ ከዚህ ፡ ካደረስከኝ ፡ አንተ ፡ ወደ ፡ አባትኽና ፡ ወደ ፡ እናትኽ ፡ ተመለስ ፤ እኔም ፡ ወደ ፡ ክፉ ፡ ዕድሌ ፡ ልኑዋ ። ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፤–እኅቴ ፡ ሆይ ፡ ለሰው ፡ ያለፈቃዱ ፡ የደረሰበት ፡ መከራ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የሚያ ሳዝነው ፡ በፈቃድ ፡ የሆነ ፡ መከራ ፡ ከደስታ ፡ ይቈጠራል ። ያይኔ ፡ አበባ፤ - ማን ፡ ሰው ፡ ነው ፡ ያላንተ ፡ በሰው ፡ መቸር ፡ ዕድል ፡ ውስጥ ፡ የሱን ፡ መልካም ፡ ዕድል ፡ አቀላቅሎ ፡ ሥቃይ ፡ የሚያይ ፡ ለሰው ፡ ሲል ፡ ከሞተው ፡ በቀር ። ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡–ታሪካዊ ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ ቈራጥ ፡ መሆን ፡ ያስፈልጋል ፤ ይልቅስ ፡ ተነሽ ፡ እየተ ጓዝን ፡ እንጫወት ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔርና ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ወደ ፡ አዳል ። በረሓ ፡ መንፈሳዊ ፡ ጨዋታ ፡ እየተጫወቱ ፡ ይጓዙ ፡ ዠመር ። ከጧት ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ ከሄዱ ፡ በኋላ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፤ - ወዳጄ ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ በዚሁ ፡ መከራችን ፡ ደስ ፡ ይበለን ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የከፋውም ፡ ደስ ፡ ያለውም ፡ የለም ፡ ተብሏል ። የሰው ፡ ልጅ ፡ ጊዜውን ፡ በመከራ ፡ ካላሳለፈ ፡ ታሪክ ፡ የለውም ፤ ታሪክን ፡ የሚወልድ ፡ መከራ ፡ ነው ። ያይኔ ፡ አበባ ፤-ወንድሜ ፡ ርግጥ ፡ ነው ፡ በዚህ ፡ ደስ ፡ እንዲለን ፡ ያስፈልጋል ፤ አባቴም ፡ መከራ ፡ የጽድቅ ፡ ማጣሪያ ፡ ነው ፡ ሲሉ ፡ እሰማ ፡ ነበር ። የወርቅ ፡ መፈተኛ ፡ በእሳት ፤ የሰውም ፡ ልጅ ፡ መፈተኛው ፡ በመከራ ፡ መሆኑ ፡ አይዘነጋም ፡ አሁ ንስ ፡ መሽ ፡ ጨረቃ ፡ እንኳ ፡ የለም ፤ ካዳልም ፡ መሬት ፡ ከገባን ፡ ወዲህ ፡ ምንም ፡ መንደር ፡ አላየንም ።

ወደፊትም ፡ ቢሆን ፡ ራሳችንን ፡ የምናስገባበት ፡ ጐጆ ፡ የምናገኝ ፡ አይመስለኝምና ፤ ከዚሁ ፡ አድረን ፡ ጎሕ ፡ ሲቀድ ፡ ጕዟችንን ፡ ብንቀጥል ፡ ይሻል ፡ ይመስለኛል ። ገብረ ፡ እግዚአ

ብሔር ፤ እሺ ፡ እኅቴ ፡ እኔም ፡ ደክሞኛል ፡ ብናርፍ ፡ እወዳለሁ ።
ተስፋ ፡ ያደረግነውም ፡ ተራራ ፡ እየራቀ ፡ ሄደ ፤ ምናልባት ፡
ነገ ፡ ወይም ፡ ተነገ ፡ ወዲያ ፡ ብንደርስበት ፡ ነው ፡ አንቺ ፡
እንዳልሽው ፡ ከዚሁ ፡ ነጠላችንን ፡ አንጥፈን ፡ እንተኛ ።

ገብረ ፡ እግዚአብሔርና ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ነጠላቸውን ፡ አን
ጥፈው ፡ ተኙ ፤ በዚያ ፡ በረሓ ፡ ምንም ፡ መንፈሳዊ ፡ ጨዋታ
ቸውን ፡ እያወጉ ፡ ሲሄዱ ፡ ባይሰማቸው ፡ ሰውነታቸው ፡ ስለ ፡
ደከመ ፡ በጠለቀ ፡ እንቅልፍ ፡ ተውጠው ፡ የሌሊቱን ፡ ግር
ማና ፡ ያውሬዎቹን ፡ ጩኸት ፡ ሳይሰሙ ፡ ማታ ፡ የወደቁ ፡
ጧት ፡ ነቁ ። ያይኔ ፡ አበባ ፡ ወንድሜ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ አደርክ፡
ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ እኔ ፡ በጣም ፡ እንቅልፍ ፡ ወሰደኝ ፡ ነፍሴ
ንም ፡ አላወቅሁም ፤ አንቺስ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ አደርሽ ። ያይኔ ፡
አበባ ፤— እኔ ፡ ሥጋዬ ፡ ስለ ፡ ደከመ ፡ በጠለቀ ፡ እንቅልፍ ፡ ተዋ
ጥሁ ፡ እንጂ ፡ መንፈሴ ፡ አልተኛም ፡ ነበር ፤ ስለዚህ ፡ ሌሊት ፡
ያየሁትን ፡ ሕልም ፡ ብነግርኽ ፡ በጣም ፡ ይገርምኻል ። ገብረ ፡
እግዚአብሔር ፤—እኅቴ ፡ እንግዴህ ፤ እንዳትረሽው ፡ በቶሎ ፡
አጫውችኝ ፡ ምናልባት ፡ ለዚህ ፡ በዳበሳ ፡ ለምንሄድበት ፡ ለማና
ውቀው ፡ መንገድ ፡ አጽናኚ ፡ ይሆነን ፡ ይሆናል ። ያይኔ ፡ አበባ ፤
እንግዴህ ፡ ደህና ፡ አድርገኽ ፡ ስማኝ ፡ ሕልሜን ፡ ልዝምርልኽ ፡
ካንድ ፡ ትልቅ ፡ ከተማ ፡ የገባሁ ፡ ይመስለኛል ፡ ጊዜውም ፡ ከሌ
ሊቱ ፡ አራት ፡ አምስት ፡ ሰዓት ፡ ይሆናል ። እኔም ፡ ከመንገዱ ፡
መካከል ፡ ግራ ፡ ገብቶኝ ፡ ቆሜ ፡ ስመለከት ፡ አንድ ፡ ሰው ፡
ከወደ ፡ ኋላዬ ፡ መጥቶ ፡ አንቺ ፡ ልጅ ፡ ይህንን ፡ ከተማ ፡ እስከ ፡
ዛሬ ፡ አይተሽውም ፡ አታውቂምን ፡ ብሎ ፡ ጠየቀኝ ፤ እኔም ፡
አይቸውም ፡ አላውቅ ፡ ብየ ፡ መለስኩለት ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሰውዬው ፡ ነዪ ፡ ላሳይሽ ፡ ብሎ ፡ ካንድ ፡
ቤተ ፡ መንግሥት ፡ የሚመስል ፡ ግንብ ፡ አጠገብ ፡ ወሰደኝ ፤ ከዚ
ያም ፡ ከትልቅ ፡ ቤት ፡ ግንባር ፡ በኍልህ ፡ ጽሕፈት ፡ የዓለም ፡
ቤት ፡ የሚል ፡ ተጽፎበት ፡ ይታይ ፡ ነበር ። እኔም ፡ የቤቱ ፡
ሥራና ፡ ያደባባዩ ፡ አኳኋን ፡ አስገርሞኝ ፡ ትኩር ፡ ብዬ ፡ ስመ
ለከት ፡ ወዲያው ፡ ከሌሊቱ ፡ ፯ ፡ ሰዓት ፡ ተደወለ ፤ አደባባዩም ፡
ጭር ፡ አለ ፤ መብራቱም ፡ አንዳንዱ ፡ ጠፋ ። እኔም ፡ ተጨንቄ ፡

ወደ ፡ ግንቡ ፡ ስመለከት ፡ የዓለም ፡ ቤት ፡ ከሚለው ፡ ማስታወቂያ ፡ በላይ ፡ በመስኮቱ ፡ አንድ ፡ በጣም ፡ የተዋበች ፡ ቈንጆ ፡ ብቅ ፡ አለች ፤ እኔም ፡ አስተርጓሚዬን ፡ ይህች ፡ የምታምር ፡ ልጅ ፡ ማን ፡ ትባላለች ፡ ብዬ ፡ ጠየቅሁት ። እሱም ፡ ከት ፡ ብሎ ፡ ሥቆ ፤ ልጅ ፡ የምትያት ፡ አሮጌዪቱን ፡ ዓለም ፡ ነውን ፡ የሰውን ፡ ልጆች ፡ ለማጥመድና ፡ ለማታለል ፡ በመቀባበት ፡ ልጅ ፡ ትመስላለች ፡ እያለ ፡ ሲያጫውተኝ ፤ አንድ ፡ መልከ ፡ መልካም ፡ ጐልማሳ ፡ በቤቷ ፡ አጠገብ ፡ ሲያልፍ ፡ ትኩር ፡ ብላ ፡ አይታ ፡ አንተ ፡ ጐልማሳ ፡ ልጅ ፡ ቈየኝ ፡ ቈየኝ ፡ ብላ ፡ ጮኸች ፤ እሱም ፡ ደንገጠና ፡ ቆሞ ፡ ጠበቃት ። እሷም ፡ እንደ ፡ ደረሰች ፡ አንገቱን ፡ ይዛ ፡ ሳመችው ፡ ፊቱንም ፡ ያለኀፍረት ፡ እያየች ፡ እንደዚህ ፡ ትለው ፡ ዠመር ፤ ይህች ፡ በኔ ፡ ዘንድ ፡ የደኅንነት ፡ ቍርባን ፡ ናት ፡ ዛሬ ፡ ስለቴን ፡ ፈጸምኩ ፤ ስለዚህ ፡ ፊትኽን ፡ ብናፍቅ ፡ ልፈልግኽ ፡ መጣሁ ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ እንሂድ ፡ ደስ ፡ ይበለን ፡ ዓለማችንን ፡ እንይ ፤ ባለቤቴ ፡ የለም ፡ ወደ ፡ ሩቅ ፡ አገር ፡ ሄዷል ፡ አይመጣምም ። እኔ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ለዘላለም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፤ እንግዴህ ፡ ካንተ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ወዳጅ ፡ የለኝም ፤ ብላ ፡ እጁን ፡ ይዛ ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ገባች ፡ በሩም ፡ ተዘጋ ።

ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፤ ወይ ፡ ግሩም ፡ ባገራችን ፡ ምሳሌ ፡ ግፍ ፡ ጸሎት ፡ አያሻም ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ያንቺ መከራ ፡ ማየት ፡ ትምህርት ፡ ሆኖሽ ፡ እንዴት ፡ ያለውን ፡ ጸጋ ፡ እግዚአብሔር ፡ ገለጠልሽ ፤ እስቲ ፡ እባክሽ ፡ ጨርሽልኝ ። ያይኔ ፡ አበባ ፦ -በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አስተርጓሚዬ ፡ አዬ ፡ ጉድ ፡ ይህ ጕልማሳ ፡ በሬ ፡ ወደ ፡ መታረድ ፡ እንደ ፡ ሚነዳ ፡ ሰነፍም ፡ ለቅጣት ፡ ወደ ፡ እሥራት ፡ እንደሚጎተት ፡ ተከትሏት ፡ ወደ ፡ ቤቷ ፡ ገባ ፤ እንደ ፡ ምን ፡ ያሳዝናል ፡ ብሎ ፡ በጣም ፡ ተከዘ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዴት ያለ ፡ ግሩም ፡ ነገር ፡ ነው ፤ እግዚአብሔር ፡ ደኅና ፡ ቢያደርገን ፡ ይህንንስ ፡ ከዘመድ ፡ ከወዳጅ ፡ ጋራ ፡ በተጫወትነው ፡ መልካም ፡ ነበር ። ያይኔ ፡ አበባ ፤ -እባክኽ ፡ ተወኝ ፡ አታሥቀኝ ፡ እኛውም ፡ እንደዚሁ ፡ ሕልም ፡ ሳንሆን ፡ አንቀርም ። ከዚህ ፡ በረሓ ፡ ወጥተን ፡ ነው ፡ ከዘመድ ፡ የምንገናኘው ፡ ይልቁንስ ፡ ሕልሜን ፡ ልጨርስልኽ ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ነጋ ። ከተማውም ፡

በሰልፍ ፡ ተሸበረ ፤ ነጋሪቱ ፡ ከደባባይ ፡ ወጥቶ ፡ ይጎሽም ፡ ዠመር ፤ ሰንደቅ ፡ ዓላማውም ፡ በነጋሪቱ ፡ አጠገብ ፡ ይውለበለብ ፡ ነበር ። እኔም ፡ አስተርጓሚዬን ፡ ምንድነው ፡ ይህ ፡ ሽብር ፡ አልኩት ፤እሱም ፡ ያ ፡ ሌሊት ፡ ያየሽው ፡ ጉልማሳ ፡ ሹመት ፡ ሊያገኝ ፡ ነው ፡ ሲለኝ ፡ ከዓለም ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ከእግር ፡ እስከ ፡ ራሱ ፡ በወርቅ ፡ ተሸልሞ ፡ ብቅ ፡ አለ ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ጭብጨባውና ፡ እልልታው ፡ አየሩን ፡ ሞላው ፡ ግማሹ ፡ ለዘላለም ፡ ያኑርኽ ፡ እያለ ፡ ይጮኽ ፡ ነበር ። ያ ፡ ጉል ማሳ ፡ ወደ ፡ ነጋሪቱ ፡ መምቻ ፡ አጠገብ ፡ እንደ ፡ ደረሰ ፡ አጋ ፋሪው ፡ ስማ ፡ ስማ ፡ መስማሚያ ፡ ይንማኽ ፡ ያድባርን ፡ ያው ጋርን ፡ ጠላት ፡ እያለ ፡ ጮኸ ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ፡ ትልቅ ፡ ጸጥታ ፡ ሆነ ። ወዲያው ፡ ለልጄ ፡ ለወዳጄ ፡ ለራስ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ ደስታንና ፡ ኀዘንን ፤ ምኞትንና ፡ ፍትወትን ፡ ሰጥቻ ለሁ ፡ ብሎ ፡ ሲናገር ፡ ጭብጨባውና ፡ እልልታው ፡ ቀለጠ፤ ራስ ፡ ሰው ፡ በከንቱም ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ ቤት ፡ ተመልሶ ፡ ገባ ።

ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፤ — እኅቴ ፡ ይህንን ፡ ሁሉ ፡ መያ ዝሽ ፡ በጣም ፡ ይገርመኛል ፤ እኔ ፡ ብሆን ፡ ይዘነጋኝ ፤ ነበር ። ያይኔ ፡ አበባ ፤ — ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ ሰው ፡ የመከራ ፡ መጽ ሐፍ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ እኔ ፡ አባቴንና ፡ እናቴን ፡ አጥቼ ፡ በወይዘሮ ፡ ኑሪቱ ፡ እጅ ፡ ከወደቅሁበት ፡ ቀን ፡ ዠምሬ፡ የመከራ ፡ ታሪክ ፡ ሆኜ ፡ ተጽፌያለሁ ፡ የማይረሱኝ ፡ ብዙ ፡ ነገ ሮች ፡ አሉ ፤ አሁንስ ፡ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ ሕልሜን ፡ ልቀጥል ልኽ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ ጨለመ ፡ ከሌሊቱ ፡ ስድስት ፡ ሰዓት ፡ የሆነ ፡ ይመስለኛል ። ከዓለም ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ የጭቅጭቅ ፡ ድምፅ ፡ ሰማሁ ፡ ወዲያው ፡ በሩ ፡ ሲከፈት ፡ ዓለም ፡ ያን ፡ ራስ ፡ ሰው ፡ በከንቱን ፡ ከውስጥ ፡ ገፍታ ፡ ከደረጃው ፡ በታች ፡ ጣለችው ። ያ ፡ ችግረኛ ፡ ራስ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ ከደረ ጃው ፡ በታች ፡ ቆሞ ፡ ዓለም ፡ ከበራፍ ፡ ቆማ ፡ ዐይኗን ፡ እየተ መለከተ ፡ ምነው ፡ ወዳጄ ፡ እኅቴ ፡ ለዘላለም ፡ አልተውኽም ፡ አላልሽኝም ፡ ነበርን ፤ እንዴት ፡ በውድቅት ፡ ጨለማ ፡ ሳላስበው ፡ አውጥተሽ ፡ ከማዕርጌ ፡ ትጥዪኛለሽ ፡ እያለ ፡ በግን

ባሩ ፡ ተደፍቶ ፡ ሲለምናት ፡ ዓለም ፡ ከት ፡ ብላ ፡ ሥቃ ፡ ምን፡ ሞኝ ፡ ነኽ ፡ በውነት ፡ እኔ ፡ ያንድ ፡ ሰው ፡ ወዳጅ ፡ ብቻ ፡ ሆኜ ፡ የምኖር ፡ ይመስልኻልን ፤ እኔ ፡ ባሌ ፡ ሳይመጣ ፡ ደስታዬን ፡ ከብዙ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ እያለዋወጥሁ ፡ ለማየት ፡ እንደምፈልግ፡ አታውቅምን ፡ አሁንስ ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ ወደምትሄድበት ፡ ሒድ ፡ እኔም ፡ ባለፋንታውን ፡ ልፈልግ ፡ አለችው ። ያም ፡ አምባ ፡ ገነን፡ ምነው ፡ ወዳጄ ፡ እኅቴ ፡ እንዲህ ፡ በጥቂት ፡ ቀን ፡ ደስታዬን ፡ ሳል ጠግብ ፡ አስወጥተሽ ፡ ትጥዪኛለሽ ፡ አላት ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ዓለም ፡ ወረተኛ ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ የደስታ ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ጠመንዣ ፡ ተኩስ ፡ የፈጠነ ፡ ነው ፡ የተባለውን ፡ አታውቅምን ። ቀኑስ ፡ ብዙ ነው ፡ ባታውቀው ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ አሁንስ ፡ ለባለ ፡ ፋንታዎች፡ ደስታ ፡ ዕንቅፋት ፡ አትሆንባቸው ፡ ወደምትሄድበት ፡ ሒድ ፡ ብላ ፡ በሩን ፡ በኀይል ፡ ዘጋችበት ። ያም ፡ ችግረኛ ፡ ከደረጃው ፡ በታች ፡ ወደ ፡ መሬት ፡ አንገቱን ፡ ደፍቶ ፡ ወይ ፡ እኔ ፡ ወዴት ፡ ልሒድ ፡ እንዲህ ፡ በተከበርኩበት ፡ ከተማ ፡ ለጠላቶቼ ፡ መዘባበቻ፡ ለወዳጆቼ ፡ ኀዘን ልሆን ፡ ነውን ፡ እያለ ፡ የመረረ ፡ ልቅሶ ፡ ያለ ቅስ ፡ ነበር ፤ በዚያ ፡ እኔም ፡ ዕንባዬ ፡ ዕንቢ ፡ ብሎ ፡ ይፈስ፡ ዠመር ።

ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፤ —ወይ ፡ ግሩም ፡ እንደምን ፡ የሰውን ፡ ከንቱነት ፡ ሁሉ ፡ ጠቅሎ ፡ የያዘ ፡ የኛን ተግባር ፡ ለማበረታታት፡ የተገለጸልሽ ፡ ሕልም ፡ ነው ፡ እባክሽ ፡ ጨርሽልኝ ።

ያይኔ ፡ አበባ ፤ —ያ ፡ ራስ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ ጥቂት ፡ ተመርሮ ፡ ራቅ ፡ ብሎ ፡ ከሄደ ፡ በኋላ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ የለም ፡ ወዳጄ ፡ ናትና ፡ በማስወጣቷ ፡ ተጸጽታ ፡ ይሆናል ፡ ሄጄ ፡ ከበሯ ፡ ተቀ ምጬ ፡ ደጅ ፡ ልጥና ፡ ብሎ ፡ ተመለሰ ፤ ከደጃፏ ፡ ተቀምጦ ፡ አሁን፡ ካሁን ፡ ትመጣለች ፡ እያለ ፡ ሲመለከት ፡ በጨለማው ፡ ውጋጋን ፡ አንድ ፡ ዐፅም ፡ የሚመስል ፡ ቀጭን ፡ ሰው ፡ በጁ ፡ ትልቅ ፡ ፋስ ፡ ይዞ ፡ ከወደ ፡ ምዕራብ ፡ ሲመጣ ፡ አየ ፤ ያም ፡ ችጋረኛ ፡ ሰው ፡ ወደሱ ፡ የሚመጣውን ፡ የሚያስፈራ ፡ ሰው ፡ በማየቱ ፡ ምን ፡ ይኾን ፡ እያለ ፡ ሲመለከት ፡ ወደሱ ፡ ቀረበና ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ ከዚህ፡ ምን ፡ ታደርጋለኽ ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ። ያም ፡ ራስ ፡ ሰው ፡ በከንቱ፡ ጌታው ፡ እኔ ፡ የዓለም ፡ ወዳጅ ፡ ነበርኩ ፤ ብዙ ፡ ጊዜም ፡ ከሷ ፡

ጋራ ፡ ለመኖር ፡ ተስፋ ፡ ሰጥታኝ ፡ ነበር ። አሁን ፡ ሳላስበው ፡ በድንገት ፡ አስወጥታ ፡ ጣለችኝ ። ስለዚህ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ወዳጇ ፡ ናትና፡ አትጨክንብኝም፡ በማለት ፡ ከሄድኩ ፡ በኋላ ፡ ደጅ፡ እጠናለሁ፡ ብዬ ፡ ተመለስሁ ፤ ጌታው ፡ እግዚአብሔር ፡ ርስዎን ፡ ካጋጠመኝ ፡ ሽማግሌ ፡ ነዎትና ፡ እባክዎ ፡ ያስታርቁኝ ፡ እያለ ፡ ዐይኑን ፡ ወደሱ ፡ አቅንቶ ፡ ይለምነው ፡ ገ፲መር ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ያ ፡ ዐዕም ፡ የሚመስል ፡ ሰው ፡ ከት ፡ ብሎ ፡ ሥቆ ፡ ውሻ ፡ ወደ ፡ ትፋቱ ፡ ተመለሰ ፡ የተባለው ፡ ባንተ ፡ ደረሰ፡ ወንድሜ ፡ ሆይ ፤ ከዓለም ፡ ወረተኛ ፡ ጋራ ከተጣሉ ፡ ወዲህ ፡ ዓለ ምን ፡ መናቅ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ መቼ ፡ ወደሷ ፡ መመለስ ፡ ይገ ባኽ ፡ ነበር ፤ ብሎ ፡ በቍጣ ፡ ልብሱን ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ ወርውሮ፡ በሚያስፈራ ፡ አስተያየት ፡ እየተመለከተ ፡ እኔ ፡ ሞት ፡ የዓለም ፡ ባል ነኝ ፤ አንተ ፡ ሰነፍ ፡ ባለቤት ፡ እንደ ፡ ሌባ ፡ ባልታሰበበት፡ ፡ ቀን ፡ ይመጣል የተባለውን ፡ አታውቅምን ፡ እያለ ፡ ፋሱን ፡ ቃጥቶ፡ ሲመለከተው ፡ ራስ ፡ ሰው ፡ በከንቱም ፡ ዓለም ፡ አሳተችኝ ፡ እባ ክዎ ፡ ይማሩኝ ፡ ሚስትዎ ፡ መሆኗን ፡ አላውቅም ፡ ነበር ፡ እያለ ፡ ይርበተበት ፡ ገ፲መር ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ሞት ፡ የዓለም ፡ ባል ፡ አንተ፡ ሰነፍ ፡ ከዓለም ፡ ወረተኛ ፡ ከንፈር ፡ የማር ፡ ወለላ ፡ ይንጠባጠ ባል ፤ ፍጻሜው ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ሬት ፡ የመረረ ፡ ነው ፡ የተባለውን፡ አታውቅምን ፡ እያለ ፡ ፋሱን ፡ ቃጥቶ ፡ ትኵር ፡ ብሎ ፡ ሲመለከ ተው ፡ ከወደ ፡ ሰማይ ፡ መልካም ፍሬ ፡ የማያፈራ ፡ ዛፍ ፡ ሁሉ፡ ይቈረጣል ፤ ወደ ፡ እሳትም ፡ ይጣላል ፡ የሚል ፡ ድምፅ ፡ ሰማሁ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ሞት ፡ የዓለም ፡ ባል ፡ ራስ ፡ ሰው ፡ በከንቱን ፡ ልቡን ፡ በፋሱ ፡ መታው ፤ ራስ ፡ ሰው በከንቱም ፡ እንደ ፡ ወፍ፡ ድምፅ ፡ አሰምቶ ፡ ሞተ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ባልንጀራዬ ፡ ርኢኩዎ ፡ ልኆጥእ ፡ ዐብየ ፡ ወተለዐለ ፡ ከመ ፡ አርዘ ፡ ሊባኖስ ፤ ወዕበ ፡ እገብእ ፡ ኀጣእክዎ ፤ ኀሠሥኩ ፡ ወኢረከብኩ ፡ መካኖ ፡ ብሎ፡ እያዜመ ፡ ካጠገቤ ፡ ጠፋ ፤ እኔም ፡ ብቻዬን ፡ ቀረሁ ፤ ዐዕም ፡ የሚመስለው ፡ ሰው ፡ ደም ፡ የተነከረ ፡ ፋሱን ፡ ወደኔ ፡ አዙሮ፡ ሲመለከት ፡ ደንግጬ ፡ ነቃሁ ። ይኸውልኽ ፡ ወዳጄ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደዚህ ፡ የሚያሳዝን ፡ ሕልም ፡ ነው ያየሁት።

ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፤-ይህ ፡ ሕልም ፡ ለመንገዳችን ፡ ረዳ ትና ፡ የታመነ ፡ ባልንጀራ ፡ እንዲሆነን ፡ ተስፋ ፡ አለኝ ፤ ነገር

ግን ፡ እኅቴ ፡ አንቺ ፡ በመከራ ፡ ስላደግሽ ፡ እንደኔ ፡ በጣም ፡ አልተዳከምሽም ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ያለሁት ፡ ከሞት ፡ ጫፍ ነው ፤ ይልቁንም ፡ ጫማ ፡ ስለ ፡ ለመድሁ ፡ በሸዋው ፡ ግለት ፡ እግሬ፡ ተልጦ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ይፈጀኛል ፤ በረኃብና ፡ በውሃ ፡ ጥም ፡ ምክንያት ፡ ጉረሮዬ ፡ ደርቆ ፡ ሰውነቴም ፡ ዛለ ፤ ለመነጋገርም፡ ሊያውከኝ ፡ ነው ፤ እኅቴ ፡ እባክሽ ፡ ከዚህ ፡ ጋደም ፡ ልበል ፡ እስከሁንም ፡ ዝም ፡ ያልኩሽ ፡ አንቺ ፡ እንዳትባቢ ፡ ብዬ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ከሸዋው ፡ ላይ ፡ ወደቀ ። ያይኔ ፡ አበባ ፤-አንገቱን ፡ ከጭኗ ፡ ላይ ፡ አድርጋ ፡ እንግዲህ ፡ ምን ፡ ላድርግ ፡ ያው ፡ የኔ ፡ ክፉ ፡ ዕድል ፡ ስቦኽ ፡ ከዚህ ፡ ለመከራ ፡ መጣህ፡ ወይኔ ፡ ዕድል ፡ ቢሷ ፡ ደግሞ ፡ የሰው ፡ ዕድል ፡ አጥፊ ፡ ሆንኩ ፡ እያለች ፡ ታለቅስ ፡ ዠመር ። ገብረ እግዚአብሔርም ፤ በውሃ ፡ ጥም ፡ ምክንያት ፡ አፉ ፡ ስለ ፡ ተያዘ ፡ በመሐረብ ፡ ዕንባዋን ፡ እየጠረገ ፡ እሱም ፡ ያለቅስ ፡ ነበር ። ያይኔ ፡ አበባ ፤— ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ ሁለት ፡ ሰዎች ፡ በሩቁ ፡ ሲመጡ ፡ አያለሁ ፡ ምን ፡ ይሆኑ ። ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፤—ምናልባት ፡ የኔ ፡ ሞቶች እነዚህ ፡ ጨካኞች ፡ አዳሎች ፡ ይሆናሉ ፤ እንግዴህ ፡ ደኅና ፡ ሰንብች ። ያይኔ ፡ አበባ ፤— ወንድሜ ፡ ምነው ፡ እንደዚህ ፡ ታባባኛለህ ፡ እኔን ሴቲቱን ፡ እንደ ፡ ማጽናናት ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ውሃ ፡ የያዙ ፡ ይሆናሉ ፤ እንደዚህ ፡ በውሃ፡ ጥም ፡ ሰንጨነቅ ፡ ሲያዩ ፡ ያዝኑልናል ፡ ውሃ ፡ ይሰጡን ፡ ይሆናል ፤ ለምን ፡ ወደ ፡ ክፉ ፡ ትተረጒመዋለህ ። ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፤-ርግጥ ፡ ነው ፡ እኅቴ ፤ ሰው የወንድሙ ፡ ጭንቅና፡ መከራ ፡ እንደሚያሳዝነው ፡ ዐውቃለሁ ። ነገር ፡ ግን ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ሰውን ፡ ማጥፋት ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ከለመዱ ፡ በኋላ ፡ ቅብት ፡ እንደሚያርዱ ፡ ሥጋ ፡ ቤቶች ፡ የሰው ፡ ደም፡ እንደ ማያሰቅቃቸው ፡ ስለ ፡ ዐወቅሁና ፡ ይልቁንም ፡ አዳሎች ፡ ለሚስት ፡ ማጫ ፡ የወንድማቸውን ፡ ደም ፡ እንደሚያቀርቡ ፡ ስለ ፡ ተረዳሁት ፡ ፈራሁ ፡ እንጂ ፤ ምናልባት ፡ አንቺ ፡ እንዳልሽው ፡ ይሆን ፡ ይሆናል ፡ ያቅር ፡ በዩኝ ።

ገብረ ፡ እግዚአብሔርና ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ሲነጋገሩ ፡ አዳሎች ፡ በቀርበታ ፡ ውሃ ፡ ተሸክመው ፡ ከፊታቸው ፡ ደረሱ ፤ ያይኔ ፡ አበባ ፤—ብድግ ፡ ብላ ፡ እባካችሁ ፡ ጌቶቼ ፡ በውሃ ፡ ጥም ፡ ልና

ልቀ ነውና ፡ ትንሽ ፡ ውሃ ፡ ስጡን ። አዳሎች ፡ ቋንቋ ፡ ባለማወቃ
ቸው ፡ እየሣቁ ፡ ርስ ፡ በርሳቸው በአዳል ፡ ቋንቋ ፡ ይነጋገሩ ፡
ዠመር ። ያይኔ ፡ አበባ ፡ ቋንቋዋ ፡ እንዳልገባቸው ፡ ዐውቃ ፣
በጅዋ ፡ እንደሚጠጣ ፡ ሰው ፡ እያሳየች ፡ ትለምን ፡ ዠመር ። አንዱ ፡
አዳል ፡ ውሃ ፡ ስጠኝ ፡ ማለቷ ፡ ገብቶት ፡ ካቅማዳው ፡ ውሃ ፡ እን
ድትጠጣ ፡ ማሰሪያውን ፡ ፈቶ ፡ ሰጣት ፤ ያይኔ ፡ አበባም ፡ ትንሽ ፡
ተጐንጭታ ፡ አቅማዳውን ፡ ይዛ ፡ እባክኽ ፡ ለዚህ ፡ ሰው ፡
ትንሽ ፡ አጠጣው ፡ በውሃ ፡ ጥም ፡ ሊሞት ፡ ነው ፡ ብላ ፡ አቅማ
ዳውን ፡ ሳበችው ። ጨካኙ ፡ አረመኔ ፡ በአዳል ፡ ቋንቋ ፡ ዕንቢ ፡
ብሎ ፡ ሲነጥቅ ፡ ውሃው ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ ፈሰሰ ፤ ገብረ ፡ እግዚ
አብሔር ፡ ውሃው ፡ ሲፈስ ፡ አይቶ ፡ እየተንፏቀቀ ፡ ሄዶ ፡ ውሃ
ውን ፡ ከሸዋው ፡ ላይ ፡ ይልስ ፡ ዠመር ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አንደ
ኛው ፡ አዳል ፡ ውሃውን ፡ በመላሱ ፡ ተቈጥቶ ፡ ራሱን ፡ ረግጠ ፣
አስጣለው ። ያይኔ ፡ አበባ ፡ ሰው ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ እንደዚህ ፡
ያለ ፡ ጭካኔ ፡ በመሥራቱ ፡ ተናዳ ፡ በርግጫ ፡ የመታውን ፡ አዳል ፡
ጕረሮውን ፡ አንቃ ፡ አንት ፡ ጨካኝ ፡ አረመኔ ፡ እንዴት ፡ ሰው ፡
ሆነኽ ፡ ለወንድምህ ፡ አታዝንም ፡ እያለች ፡ ትጮኽ ፡ ፊቱን ፡ ትቧ
ጥጥ ፡ ዠመር ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቅማዳ ፡ የያዘው ፡ አዳል ፡ እገ
ብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሆድ ፡ ላይ ፡ ዘሎ ፡ ወጥቶ ፡ በጩቤ ፡ ልቡን ፡
ወግቶ ፡ ገደለውና ፡ ሮጠ ፤ ሁለተኛውም ፡ አዳል ፡ ያይኔ ፡ አበባን ፡ ገፍ
ትሮ ፡ ጥሎ ፡ ተከተለው ። ያይኔ ፡ አበባም ፡ ከወደቀችበት ፡ ተነ
ሥታ ፡ ወደ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ብትመለከት ፡ በጩቤ ፡
ተወግቶ ፡ በደም ፡ ተጨማልቆ ፡ አየችና ፡ እንዳበደ ፡ ሰው ፡ እየ
ጮኸች ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ ወድቃ ፡ ትስመው ፡ ነበር ። ከጥቂት ፡
ሰዓት ፡ በኋላ ፡ እልፍ ፡ ብላ ፡ ራሷን ፡ ይዛ ፡ በዜማ ፡

አለመማር ፡ ክፉ ፡ አለመመልከት ፤
ወንድሙን ፡ ይገድላል ፡ ሚስት ፡ ለማግባት ።
ለትዳሩ ፡ ብሎ ፡ ሰው ፡ የሚገድል ፤
ከአውሬዎች ፡ ተራ ፡ ስሙ ይጻፋል ።
እንዴት ፡ ተሰወረ ፡ ከሰዎች ፡ ኀሊና ፤
እጁን ፡ በደም ፡ መንከር ፡ ሳይመስለው ፡ ፈተና ።
ጲላጦስ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ይህነን ፡ ያሰበ ፤
ከደሙ ፡ ንጹሕ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ የታጠበ ።

ብፈልግ ፡ አጣሁኝ ፡ በምድር ፡ በሰማይ ፤
እንደ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጌታውን ፡ መሳይ ።
ያልተማረ ፡ ክፉ ፡ ወንድሙን ፡ ይገድላል ፡
የተማረ ፡ መልካም ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ይሠዋል ።
ልሩጥ ፡ ወደ ፡ ፊቴ ፡ ሞትን ፡ እስካገኝ ፡
አንተ ፡ ዐፈር ፡ ስትሆን ፡ እኔም ፡ ዕብድ ፡ ነኝ ።

እያለች ፡ ካለቀሰች ፡ በኋላ ፡ ዘወር ፡ ብላ ፡ ብታይ ፡ ወዳጅዋ ፡ በደም ፡ ተለውሶ ፡ መልኩ ፡ ዐፈር ፡ መስሎ ፡ በመሬት ፡ ወድቆ ፡ ዐይኑ ፡ ፈጦ ፡ እሷን ፡ እሷን ፡ የሚመለከት ፡ መስሎ ፡ ባየች ፡ ጊዜ ፤ ነጠላዋን ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ ጥላ ፡ ወይ ፡ እኔ ፡ ጨካኝዋ ፡ ጥዬኽ ፡ ሄድኩ ፡ አንተ ፡ ብትሆን ፡ እንደዚህ ፡ አታደርግም ፡ ነበር ፡ ብላ ፤ ወደ ፡ ፊቷ ፡ በለጋራው ፡ እንደሚያሰድደው ፡ ትሮጥ ፡ ዠመር ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ የሚሰማት ፡ የኀሊናዋ ፡ አሳብ ፡ ምን ፡ ይሆን ፡ ኀዘን ፡ አደንዝዟት ፡ ስትሮጥ ፡ እንደ ፡ ሰከረ ፡ ሰው ፡ ትንገደገድ ፡ ነበር ። በኀዘን ፡ የሰከረች ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ልትወድቅ ፡ ስትነሣ ፡ ከሌሊቱ ፡ በ፰ ፡ ሰዓት ፡ ከተራራው ፡ ሥር ፡ ደርሳ ፡ በኀዘንና ፡ በመከራ ፡ ስለደከመች የሌሊቱን ፡ ግርማና ፡ አውሬዎችን ፡ ሳትፈራ ፡ እንቅልፍ ፡ ወሰዳት ፡ ተራራውም ፡ ከአዳል ፡ መሬት ፡ ውስጥ ፡ የሚገኝ ፡ አዘሎ ፡ የሚባል ፡ ነው ፡ ይህም ፡ ተራራ ፡ የዓለም ፡ ምሬት ፡ የተሰማቸው ፡ መናንያን ፡ ተሰውረው ፡ የሚኖሩበት ፡ ቅዱስ ፡ ተራራ ፡ ነው ። ጎሕ ፡ ሲቀድ ፡ አንድ ፡ መናኒ ፡ ውሃ ፡ ለመቅዳት ፡ ወደ ፡ ምንጭ ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ዜማ ፡ እያዜመ ፡ ይወርድ ፡ ነበር ፡ ዜማውም ፡ እንደዚህ ፡ ነው ። እመኒ ፡ ሖርኩ ፡ ማዕከለ ፡ ጽላሎተ ፡ ሞት ፤ ኢይፈርሆ ፡ ለእኩይ ፡ እስመ ፡ አንተ ፡ ምስሌየ ፡ እያለ ፡ በቍልቍለቱ ፡ ሲንደረደር ፡ መንገዱ ፡ ካጠገቧ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ብንን ፡ አለች ። ያይኔ ፡ አበባም ፡ በዚህ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ የሰው ፡ ድምፅ ፡ በመስማቷ ፡ ደንግጣ ፡ ወደ ፡ ቍልቍል ፡ ሮጠች ። ያም ፡ ባሕታዊ ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ስትሮጥ ፡ አይቶ ፡ አይዞሽ ፡ ይህ ፡ ቦታ ፡ የመናንያን ፡ ቦታ ፡ ነው ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ ወደዚህ ፡ ተራራ ፡ ቢመጣ ፡ ያገሩ ፡ ጌታ ፡ ይቀበለዋል ፤ ከሽክሙም ፡ ያሳርፈዋል ፡ አለና ፡ እሮጠ ፡ ያዛት ። ያይኔ ፡ አበባ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ እንደዚህ ፡ የሚያጽናና ፡ ድምፅ ፡ በመስማቷ ፡ ይልቁንም ፡ ጨለማው ፡ በጣም ፡ ስላልለ

ቀቀ ፡ የሰውም ፡ መልክ ፡ ስለማይለይ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ መሰ
ላትና ፡ ወዳጄ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ በጨካኞች ፡ አዳሎች ፡
እጅ ፡ የሞተ ፡ መስሎኝ ፡ ሳዝን ፡ በሕልሜ ፡ ኖሯል ፡ ብላ ፡ ደስ፡ አላት፡
መናኒውም ፡ አንቺ ፡ ልጅ ፡ ከወዴት ፡ መጣሽ ፡ አገርሽስ ፡ ወዴት



ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ በጨካኞች ፡ አዳሎች ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ተገደለ ።

ነው ፡ እያለ ፡ ይጠይቃት ፡ ዠመር ። ያይኔ ፡ አበባ ፡ የመጣችበ
ትን ፡ በመጠየቁ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ አለመሆኑን ፡ ተረዳችውና፡
ለጥያቄው ፡ ሳትመልስ ፡ ፀዜማ ፡ ቃለቅስ ፡ ዠመር ። ያይኔ አበባ ፤

አለመማር ፡ ክፉ ፡ አለመመልከት ፤
ወንድሙን ፡ ይገድላል ፡ ሚስት ፡ ለማግባት ።

ለትዳሩ ፡ ብሎ ፡ ሰውን ፡ የሚገድል ፤
ከአውሬዎች ፡ ተራ ፡ ስሙ ፡ ይጻፋል ።

እንዴት ፡ ተሰወረ ፡ ከሰዎች ፡ ኅሊና ፤
እጁን ፡ በደም ፡ መንከር ፡ ሳይመስለው ፡ ፈተና ።

ጲላጦስ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ይህነን ፡ ያሰበ ፡
ከደሙ ፡ ንጹሕ ፡ ነኝ ፡ ብሎ ፡ የታጠበ ።



ያይኔ ፡ አበባ ፡ ከዘሎ ፡ ተራራ ፡ በኀዘንና ፡ በመከራ ፡ ደክማ ፡ የከበደ ፡
እንቅልፍ ፡ እንደ ፡ ወሰዳት ።

ብፈልግ ፡ አጣሁኝ ፡ በምድር ፡ በሰማይ ፤
እንደ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጌታውን ፡ መሳይ ።

ያልተማረ ፡ ክፉ ፡ ወንድሙን ፡ ይገድላል ፤
የተማረ ፡ መልካም ፡ ስለ ፡ ሰው ፡ ይሠዋል ።

ልኑጥ ፡ ወደፊቴ ፡ ሞትን ፡ እስካገኝ ፤
አንተ ፡ አፈር ፡ ስትሆን ፡ እኔም ፡ ዕብድ ፡ ነኝ ።

ወይ ፡ እኔ ፡ ዕድለ ፡ ቢሷ ፡ እንደማያጐድል ፡ ዕቃ ፡ ጥዬኽ ፡ መጣሁ ፡ አንተ ፡ ብትሆን ፡ እንደኔ ፡ አታደርግም ፡ ነበር ። በሕታዊው ፤– ምንድነው ፡ እንዲህ ፡ በዜማ ፤ የምታለቅሽው ፡ እዚህ ፡ ከኛ ፡ ዘንድ ፡ የሚመጣ ፡ አባት ፡ እናቱን ፤ ሚስቱን ፤ ልጁን ፤ ቤቱን ፤ የተወ ፡

ነው ፤ አንቺ ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ብለሽ ፡ እንደ ፡ ዓለማዊት ፡ ሴት ፡ ከመነንሽ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ጥለሽው ፡ ለመጣሽው ፡ ወዳጅሽ ፡ ባዜማ ፡ ታለቅሽለሽ ፤ ይህ ፡ ለኛ ፡ ኑሮ ፡ የሚስማማ ፡ አይደለም ። ያይኔ ፡ አበባ ፤—እኔ ፡ ወደዚህ ፡ የመጣሁት ፡ ዓለምን ፡ በመናቅ ፤ አይደለም ፡ የመቤቴ ፡ ጽኑ ፡ አገዛዝ ፡ ምሬትና ፡ የባርነት ፡ ቀን በር ፡ ክብደት ፡ አስመርሮኝ ፡ ነው ። የማለቅሰውም ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚባለው ፡ ወዳጄ ፡ ለኔ ፡ ሲል ፡ በውሃ ፡ ጥምና ፡ በችጋር ፡ ሲንገላታ ፡ በጨካኝ ፡ አዳል ፡ እጅ ፡ ስለ ፡ ሞተብኝ ፡ ነው ። መናኙ ፤—አትዘኝ ፡ ወዳጅሽ ፡ ዋጋውን ፡ በማግኘት ፡ ስለ ፡ ቀደመሽ ፡ መቅናት ፡ ይገባሻል ። ያይኔ ፡ አበባ ፤—እግዚአብሔር ፡ አድርጎልኝ ፡ ቢሆንማ ፡ የሱን ፡ የሥቃይ ፡ ሞት ፡ ሳላይ ፡ እኔ ፡ ሞቼ ፡ ቢሆን ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ዕድለኛ ፡ ነበርኩ ፡ አሁንስ ፡ እባ ክዎ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እንዳለ ፡ ሬሳውን ፡ ከዚያ ፡ አምጥተን ፡ እንቅበረው ፡ የትም ፡ ወድቆ ፡ አይቅር ።

መናኙ ፤— ለሰው ፡ ሲል ፡ የሞተ ፡ ምን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ያስፈልገዋል ፡ እሱ ፡ ራሱ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ነው ፡ አሁንስ ፡ ትነሽ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እንሂድ ። ከተራራው ፡ ጫፍ ፡ አንዲት ፡ የተለየች ፡ ለመናንያን ፡ ሃይማኖታቸውንና ፡ ምግባራቸ ውን ፡ የምትደግፍላቸው ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ነበረች ። በማለዳ ፡ ጎሕ ፡ ሲቀድ ፡ መናንያን ፡ ተሰብስበው ፡ የመድኅኒታችንን ፡ ሥን ፡ ስቅለት ፡ በመካከላቸው ፡ አድርገው ፡ ማዕንጠንታቸውን ፡ ይዘው ፡ የተለመደ ፡ ጸሎታቸውን ፡ ያደርሱ ፡ ነበር ፡ ጸሎቱም ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ሰ ታ ት ።

ይትባረክ ፡ እግዚአብሔር ፡ አምላከ ፡ እስራኤል ፡ ዘገብረ ፡ ዐቢየ ፡ ወመንክረ ፡ ባሕቲቱ ፡ ወይትባረክ ፡ ስመ ፡ ስብሐቲሁ ፡ ቅዱስ ፡ ወይምላዕ ፡ ስብሐቲሁ ፡ ኵሉ ፡ ምድረ ፡ ለይኩን ፡ ለይኩን ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ጸባኦት ፡ ፍጹም ፡ ምሉዕ ፤ ሰማያተ ፡ ወምድረ ፡ ቅድሳተ ፡ ስብ ሓቲከ ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፤
ዘእምቅድመ ፡ ዓለም ፡ ሀሎ ፡ ወይሄሉ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ።

ቅዱስ ፣ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘይሴባሕ ፡ እምትጉሃን ፡ ወትቄደስ ፡ እምቅዱሳን ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘይፈርህዎ ፡ ኪሩቤል ፡ ወእምግርማሁ ፡ ይርዕዱ ፡ ሱራፌል ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘይመይጦ ፡ ለመብረቅ ፡ ወያጸንዖ ፡ ለነጐድጓድ ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘይከዕዎ ፡ ለጽልመት ፣ ፍና ፡ ሠርክ ፡ ወይመጦ ፡ ለብርሃን ፡ መንገለ ፡ መሥዕ ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘአኰነኖ ፡ መዓልተ ፡ ለፀሐይ ፡ ከመ ፡ ያብርህ ፡ ለነ ፡ ውስተ ፡ ጠፈረ ፡ ሰማይ ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘአኰነኖሙ ፡ ለወርኅ ፡ ወለከዋክብት ፡ ከመ ፡ ይሠልጡ ፡ ምግቦሙ ፡ በሌሊት ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘይሬስዮሙ ፡ ለመላእክቲሁ ፡ መንፈስ ፡ ወለእለ ፡ ይትለአክዎ ፡ ነደ ፡ እሳት ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፤
ዘረበቦ ፡ ለሰማይ ፡ ከመ ፡ ሐይመት ፡ ወአጽንዓ ፡ ለምድር ፡ ዲበ ፡ ማይ ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘገብሮ ፡ ለአዳም ፡ በዘዚአሁ ፡ አርአያ ፡ ወአምሳል ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘምስለ ፡ ኖኅ ፡ ኪዳነ ፡ ዘአቀመ ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘሠርዓ ፡ ለአብርሃም ፤ ወመሐለ ፡ ለይስሐቅ ፤ ወአቀመ ፡ ስምዓ ፡ ለያዕቆብ ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘምስለ ፡ ዮሴፍ ፡ ተሠይጠ ፡ ከመ ፡ ይስፍር ሲሳየ ፡ ለሕዝብ ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘወሀበ ፡ ሕገ ፡ ለሙሴ ።

ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘቀደሰ ፡ ክህነቶ ፡ ለአሮን ።
ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘቀብዖ ፡ ለዳዊት ፡ ቅብዐ ፡ ትንቢት ፡ ወመንግሥት ።
ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ፡
ዘበነቢያት ፡ አስተንፈሰ ፡ ከመ ፡ ያስምዕ ፡ ቃሎ ፡ ለሕዝብ ።
ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅዱስ ፡ እግዚአብሔር ።
ዘይሴብሕዎ ፡ መላእክት ፡ ወየአኰትዎ ፡ ሥልጣናት ።

◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆ ◆

መናኙ ፡ በጸሎታቸው ፡ መጨረሻ ፡ በር ፡ ከፍቶ ፡ ገባና ፡ እንሆ ፡ ይህችን ፡ ልጅ ፡ ውሃ ፡ ልቀዳ ፡ ስሄድ ፡ አገኘኋት ፤ ሁሉም ፡ ደንግጠው ፡ እሷን ፡ ራሷን ፡ ከተመለከቱ ፡ በኋላ ፡ የማኅበሩ ፡ አለቃ ፡ አባ ፡ ኖኅተ ፡ ብርሃን ፡ አንቺ ፡ ልጅ ፡ በዚህ ፡ ባበባ ፡ ጊዜሽ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ምሬት ፡ ተሰምቶሽ ፡ ወደዚህ ፡ ተራራ ፡ መጣሽ ። ያይኔ ፡ አበባ ፤-ብፁዕ ፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡ እኔ ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ምሬት ፡ ተሰምቶኝ ፡ አልመጣሁም ። አባ ፡ ኖኅተ ፡ ብርሃን ፤-እንግዲያስ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይህንን ፡ በረሓ ፡ አቋርጠሽ ፡ መጣሽ ፤ እንደ ሚመስለኝ ፡ ያማራ ፡ ዘር ፡ መልክ ፡ አይብሻለሁ ፤ አገርሽም ፡ ሩቅ ፡ ይመስለኛል ። ያይኔ አበባ ፤-አገሬም ፡ ተጕለት ፡ ውስጥ ፡ ነው ፤ ብቻዬንም ፡ ይህንን ፡ በረሓ ፡ አቋርጬ ፡ ለመምጣት ፡ አልችልም ፡ ነበር ፤ ነገር ግን ፡ የባርነት ፡ ቀንበሬ ፡ ከብዶኝ ፡ ከወንዝ ፤ በኩለ ፡ ሌሊት ፡ ውሃ ፡ ልቀዳ ፡ ሄጄ ፡ ሳለቅስ ፡ አንድ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚባል ፡ የቄስ ፡ ልጅ ፡ የሞቀ ፡ ቤቱን ፡ ትቶ ፡ ስለኔ ፡ በዚህ ፡ በረሓ ፡ መንፈሳዊ ፡ ጨዋታ ፡ እያጫወተኝ ፡ ሲመጣ ፡ አዳሎች ፡ ገደሉት ። ስለዚህ ፡ ኀዘኔ ፡ ዕጥፍ ፡ ነው ፤ በኔ ፡ በዕድለ ፡ ቢሷ ፡ ምክንያት ፡ በመሞቱ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ እባላለሁ ፡ እንጂ ፡ መናኝ ፡ አይደለሁም ። አባ ፡ ኖኅተ ፡ ብርሃን ፤-አንችም ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ አይደለሽም ፡ እግዚአብሔር ፡ በቸርነቱ ፡ ወዳጅሽን ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔርን አስነሥቶ ፡ እንደ ፡ ብርቱ ፡ መርከበኛ ፡ ከዚህ ዓለም ፡ ማዕበልና ፡ ሞገድ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ እየተጋፋ ፡ እንደ ፡ ኖኅ ፡ መርከብ ፡ ከዚህ ፡ ከመናንያን ፡ ተራራ ፡ ስላደረሰሽ ፡ ልታመሰግኚው ፡ ይገባል ፡ እንጂ ፡ ልታዝኚ ፡ አይገባሽም ።

ያይኔ ፡ አበባ ፤-እያለቀሰች ፡ አባቴ ፡ በጣም ፡ የሚያሳዝነኝ ፡ ከዚህ ፡ ተራራ ፡ ጫፍ ፡ ለመድረስ ፡ ሲጓጓ ፡ ከበረሓ ፡ ወድቆ ፡ መቅረቱ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

አባ ፡ ኖኅተ ፡ ብርሃን ፤ — ልጄ ፡ ሆይ ፡ ወዳጅሽ ፡ ከዚህ ፡ ተራራ ፡ ጫፍ ፡ ባለመድረሱ ፡ አትዘኚ ፡ እሱ ፡ ከሁሉ ፡ ከሚበልጠው ፡ ከጽዮን ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ ወጥቷል ፤ ካዲሲቱ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ከተማ ፡ ውስጥ ፡ ደስታውን ያያል ፤ አንቺንም ፡ ከዚህ ፡ ስላደረሰሽ ፡ ዕድለኛ ፡ ነሽ ፤ የምትሠሪውም ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ይጠብቅሻል ። ያይኔ ፡ አበባ ፤—ብፁዕ ፡ አባታችን ፡ ማንኛውንም ፡ ብርቱ ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት የተዘጋጀሁ ፡ ነኝ ፤ ይልቁንም ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንድረሳ ፡ ጊዜዬን ፡ ሁሉ ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ እንዳውለው ፡ ነው ፡ የምፈቅደው ። አባ ፡ ኖኅተ ፡ ብርሃን ፤—ሥራው ፡ ብርቱ ፡ ነው ፤ ይልቁንም ፡ የድካም ፡ ሥራ ፡ ሳይሆን ፡ የምግባርና ፡ የርኅራኄ ፡ ጉዳይ ፡ ነው ። አሁን ፡ የምናዝሽ ፡ ሥራ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ምሬት ፡ ስለ ፡ ተሰማቸው ፡ መንነው ፡ የመጡ ፡ አንዲት ፡ መበለት ፡ አሉ ። እሳቸውም ፡ አይናገሩም ፡ ፊታቸውም ፡ አይታይም ፤ ካንድ ፡ ቤት ፡ ዘግተው ፡ ነው ፡ የሚኖሩት ። ስለዚህ ፡ አንቺ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ልብሽ ፡ በመከራ ስለ ፡ ታነጸ ፡ እንደናትሽ ፡ ልታዝኚላቸው ፡ በቅንነትም ፡ እንድታገለግያቸው ፡ እና ምናለንና ፡ አደራ ፡ እንልሻለን ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ እናት ፡ አባቷን ፡ እያሰበች ፡ ዕንባዋ ፡ እየፈሰሰ ፡ እሺ ፡ በፍጹም ፡ ታዛዥዎ ፡ ነኝ ፤ የተቻለኝን ፡ ያኽል ፡ እረዳቸዋለሁ ። አባ ፡ ኖኅተ ፡ ብርሃን ፤—አንዱን ፡ መነኵሴ ፡ አባቴ ፡ ይህችን ፡ ልጅ ፡ ለማሆይ ፡ ይውሰዱና ፡ ያገናኟዋት ። አንቺ ፡ ልጅ ፡ ስምሽ ፡ ማነው ፤ ያይኔ ፡ አበባ ፤—ያይኔ አበባ ፡ እባላለሁ ። አባ ፡ ኖኅተ ፡ ብርሃን ፤— ከዛሬ ፡ ዠምረሽ ፡ ፍሬ ፡ ሕይወት ፡ እንድትባዪ ፡ ምክንያቱም ፡ አበባ ፡ መሆንሽ ፡ ቀርቶ ፡ ፍሬ ፡ ስለ ፡ ሆንሽ ፡ ነው ። የታዘዙት ፡ መነኵሴ ፡ ወደ ፡ እማሆይ ፡ ገብተው ፤ እንሆ ፡ ይህች ፡ ልጅ ፡ ርስዎን ፡ ለማገልገል ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ታዛ ፡ ስለ ፡ መጣች ፡ መምህር ፡ እንዳገናኛት ፡ አዘዙኝ ።

ፍሬ ፡ ሕይወት ፡ እማሆይን ፡ በሚያስፈልገው ፡ ሁሉ ፡ በተቀደሰ ፡ ማገልገል ፡ በፍጹም ፡ ልቧ ፡ ትረዳቸው ፡ ዠመር ። ነገር ፡ ግን ፊታቸውን ፡ ባለማየቷና ፡ ድምፃቸውን ፡ ባለመስ ማቷ ፡ በጣም ፡ ታዝንና ፡ ታለቅስ ፡ ነበር ። የተለመደ ፡ ሥራ ዋም ፡ ልብሳቸውን ፡ ከበራፍ ፡ ውጭ ፡ ያስቀምጡላትና ፡ ወስዳ ፡ አጥባ ፡ ከዚያው ፡ ትመልስ ፡ ነበር ፤ ውሃ ፡ ቀድታ ፡ የሚበ ሉትን ፡ ቅጠል ፡ ቀጥፋ ፡ ውሃውንም ፡ ቅጠሉንም ፡ ከበራፍ ፡ ታደርግላቸውና ፡ ትሄድ ፡ ነበር ። ዐርብና ፡ እሑድ ፡ ብቻ ፡ ሌሊት ፡ መጥታ ፡ ከራስጌያቸው ፡ መብራት ፡ አብርታ ፡ ትሄድ ፡ ነበር ፤ ፍሬ ፡ ሕይወት ፡ ከሥራዋ ፡ ጋራ ፡ ጸሎቷን ፡ ስትጨ ርስ ፡ ሁለተኛ ፡ በጸሎቷ ፡ መድኃኒቴ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ካንተ ፡ አጠገብ ፡ አኑረው ፤ እኔህንም ፡ ሴት ፡ እንደበታቸውን ፡ ፈተኽ ፡ የመጡበትን ፡ ችግርና ፡ የመጣሁበትን ፡ ችግር ፡ እንድንጫወት ፡ አድርገን ፡ ትል ፡ ነበር ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፡ አንድ ፡ ዓመት ፡ በቅንነትና ፡ በርኅራኄ ፡ ካገለገለች ፡ በኋላ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ሌሊት ፡ እማሆይ ፡ ተኝተው ፡ ሳሉ ፡ በሕልማቸው ፡ መልአክ ፡ ተገልጦ ፡ እማሆይ ፡ እማሆይ ፡ እማሆይ ፡ ይህች ፡ የምታገለግልሽ ፡ ልጅ ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ነች ፤ የሰው ፡ ፍቅር ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ልጅ ፡ ወደ ዚህ ፡ ዓለም ፡ ስቦ ፡ እንዳመጣው ፡ ያንቺም ፡ ጽኑ ፡ ሃይማ ኖትሽና ፡ ኀዘንሽ ፡ ልጅሽን ፡ ስቦ ፡ ከዚህ ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ አመ ጣልሽ ፤ እንግዴህ ፡ አፍሽን ፡ ክፈችና ፡ ከልጅሽ ፡ ጋራ ፡ ተጫወቺ ።

ይቶት ፤— ብንን ፡ ብለው ፡ በስመ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመ ንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ አሐዱ ፡ አምላክ ፡ ወይ ፡ ግሩም ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ኖራለች ፡ የምትረዳኝ ። እኔስ ፡ የልጄን ፡ ናፍቆት ፡ የዚህን ፡ ዓለም ፡ ጣዕም ፡ ከባሌ ፡ ሞት ፡ ወዲህ ፡ ከቤቴ ፡ ውስጥ ፡ ዘግቼበት ፡ መጥቼ ፡ ነበር ፤ እንግዴህ ፡ ምን ፡ ላድርግ ፡ ያንተ ፡ ፈቃድ ፡ ይሁን ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤ እሑድ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ እንደ ፡ ተለመደው ፡ መብራት ፡ ለማብራት ፡ በሩን ፡ መታ ፡ ገብታ ፡ መብራቱን ፡ አብርታ ፡ ለመውጣት ፡ ስትመለስ ፡ እማ ሆይ ፤— አንቺ ፡ መብራቱን ፡ ያበራሽ ፡ ልጅ ፡ ማነሽ ። ፍሬ ፡

ሕይወት ፤–ሰምታ ፡ የማታውቀውን ፡ ድምፅ ፡ በመስማቷ ፡ ደንግጣ ፡ እየተንቀጠቀጠች ፡ እኔ ፡ ፍሬ ፡ ሕ ይወት ፡ ነኝ ። እማሆይ ፤ ነዪ ፡ ቀና ፡ አድርጊኝና ፡ አስቀምጪኝ ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፡ አንገታቸውን ፡ ይዛ ፡ አቀናችና ፡ አስቀመጠቻቸው። እማሆይ ፤–ተቀመጭ ፡ ፍሬ ፡ ሕይወት ፡ ተቀመጠች ። እማ ሆይ ፤–ይኸውልሽ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ብዙ ፡ ቀን፡ ድዳ ፡ ሆኜ ፡ ሰኖር ፡ አንደበቴ ፡ ተፈታ ። ፍሬ ፡ ሕይወት፡ -እኔም ፡ ይህነን ፡ በመስማቴ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ አለኝ ፤ እግዚአብሔርንም ፡ አመሰገንኩ ። ይህነን ፡ ተአምር ፡ ለመም ህሩ ፡ ሄጄ ፡ ልንገርን ። እማሆይ ፤—አይሆንም ፡ እስኪ‚ነጋ፡ ካንቺ ፡ ጋራ ፡ ተጫውተን ፡ ከነጋ ፡ በኋላ ፡ ትሄጂና ፡ ትነ ግሪያቸዋልሽ ። እማሆይ ፤—እባክሽ ፡ ይህነን ፡ ሁሉ ፡ በረሓ፡ አቋርጠሽ ፡ ከየት ፡ መጣሽ ፡ አገርሽስ ፡ ወዴት ፡ ነው ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤ __ይህነን ፡ በረሓ ፡ አቋርጬ ፡ የመጣሁት ፡ አልዩ ፡ አምባ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ነው ፤ አገሬ ፡ ግን ፡ ተጕለት ፡ ውስጥ ፡ ጉዶ ብረት ፡ ይባላል ።

ይቶት ፤-እናት ፡ አባት ፡ አሉሽን ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፡ ጥያ ያቸው ፡ ተመጣሁ ፡ ብዙ ፡ ጊዜዬ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እናትም ፡ አባትም ፡ አሉኝ ። ይቶት ፤-ማን ፡ ማን ፡ ይባላሉ ። ፍሬ ፡ ሕይወት፤ -አባቴ ፡ መምሬ ፡ ዘወልዴ ፡ ይባላሉ ፤ እናቴም ፡ ወይዘሮ ፡ በላ ይነሽ ፡ ይባላሉ ። ይቶት ፤-አንቺ ፡ ከነሱ ፡ ተለይተሽ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ወደዚህ ፡ መጣሽ ። ፍሬ ፡ ሕይወት -፤አንድ ፡ ቀን፡ እናትና ፡ አባቴ ፡ ከመካከል ፡ አድርገውኝ ፡ ተኝተው ፡ ሳሉ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ በሌሊት ፡ በር ፡ መቶ ፡ ወይዘሮ ፡ ልክም ፡ የለሽ ፡ የናቴ፡ እኅት ፡ በድንገት ፡ ታመው ፡ ጠንቶባቸዋል ፡ ብሎ ፡ ነገራቸው። እናቴም ፡ እኅታቸውን ፡ በጣም ፡ ስለሚወዷቸው ፡ እየጮኹ ፡ በሩን ፡ ከፍተው ፡ በረሩ ፤ አባቴም ፡ ተከትለው ፡ ሮጡ ። እኔም ተንቅልፌ ፡ ነቅቼ ፡ እሰማ ፡ ነበር ፡ ወዲያው ፡ ተኛሁ ። በዚያ፡ ጊዜ ፡ ጭራቅ ፡ ገብቶ ፡ በላዬ ፡ ላይ ፡ ወደቀብኝ ፤ ብንን ፡ ብዬ ፡ ባይ ፡ ከደጁ ፡ ውጋጋን ፡ ጋራ ፡ ዐይኑ ፡ እንደ ፡ ፋኖስ፡ ሲያበራ ፡ አየሁት ። ደንግጬ ፡ አማማ ፡ አባባ ፡ እያልኩ ፡ እና ቴና ፡ አባቴ ፡ ያሉ ፡ መስሎኝ ፤ አልጋውን ፡ ብዳብስ ፡ አያ ፡

ድብልብሌ ፡ የሚባለው ፡ እድብኝቱ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ ከራስጌ ፡ ተን
ከባሎ ፡ ከላዬ ፡ ላይ ፡ ወደቀብኝ ፤ እኔም ፡ እንደ ፡ ዕብድ ፡ ዕራ
ቍቴን ፡ ከቤቴ ፡ ወጥቼ ፡ ላይ ፡ ላዩን ፡ ደጋውን ፡ አገር ፡ እሮጥ፡
ዠመር ። ይቶት ፤-ይገርማል ፡ ምናልባት ፡ አንቺ ፡ እደጅ ፡ እን
ዳትወጪ ፡ ጭራቅ ፡ አለ ፤ አያ ፡ ድብልብሌም ፡ የሚባል ፡ አውሬ፡
አለ ፡ ብለው ፡ የማስፈራሪያ ፡ ተረት ፡ ነግረውሽ ፡ ይሆናል ፡ እንጂ፡
ጭራቅ ፡ የመሰለሽም ፡ ድመት ፡ ሳይሆን ፡ አይቀርም ፡ ድብልብ
ሉም ፡ ያባትና ፡ የናትሽ ፡ የቈዳ ፡ ትራስ ፡ ይሆናል ። ፍሬ ፡
ሕይወት ፤-እረ ፡ እባክዎ ፡ እናቴ ፡ የማን ፡ ድመት ፡ ነው ፡ ጠጕ
ርን ፡ በጥፍር ፡ የሚይዝ ፡ እኔ ፡ እወጣለሁ ፡ ስል ፡ ጠጕሬን ፡
በጥፍሩ ፡ ይዞኝ ፡ ነጥቄ ፡ ወጣሁ ። ይቶት ፤-ይህም ፡ ምናልባት ፡
የናትና ፡ ያባትሽ ፡ የተሰቀለ ፡ ማጭድ ፡ ሳይሆን ፡ አይቀርም ፡
ልጅ ፡ ሆይ ፡ እናትና ፡ አባት ፡ ልጆቻቸው ፡ ከውጭ ፡ እንዳይ
ወጡ ፡ ማስፈራሪያ ፡ የሚያደርጉት ፡ ነገር ፡ የልጆች ፡ የሐሳብ ፡
በሽታ ፡ ይሆናል ። ብዙ ፡ ልጆች ፡ በዚሁ ፡ ምክንያት ፤ በድን
ጋጤ ፡ የታመሙ ፡ አሉ ፤ ይህ ፡ የሐሳብ ፡ በሽታ ፡ ብዙ ፡ ልጆች፡
ጎድቷል ። ይህነን ፡ እንተወውና ፡ ከዚህ ፡ በኋላስ ፡ እንደ ፡ ምን፡
ሆንሽ ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤-በዚያ ፡ በውድቅት ፡ ጨለማ ፡ በነፋ
ስና ፡ በብርድ ፡ እየተንቀጠቀጥሁ ፡ ኸቡና ፡ ቀበሮው ፡ ሲጮኽ
ብኝ ፡ እየወደቅሁ ፡ እየተነሣሁ ፡ እማማ ፡ አባባ ፡ እያልኩ ፡ ወደ፡
ፊቴ ፡ ስሮጥ ፡ ሁለት ፡ ወንበዴዎች ፡ አገኙኝ ። እማሆይ ፤—እባክሽ፡
ምን ፡ አደረጉሽ ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤-ጨለማ ፡ ስለ ሆነ ፡ የሰው ፡
መልክ ፡ አይለይም ፡ ነበርና ፡ አይዞሽ ፡ አባትሽና ፡ እናትሽ ፡
ነን ፡ እያሉ ፡ ሳሙኝ ። እኔም ፡ እጅግ ፡ ስለ ፡ ፈራሁ ፡ የሰው ፡
ድምፅ ፡ አለይም ፡ ነበርና ፡ ብውነት ፡ መስለውኝ ፡ የደረሰብኝን ፡
እያጫወትኋቸው ፡ ስንጓዝ ፡ ነጋ ። ይቶት ፤-ከዚያ ፤ በኋላስ ፡ እባ
ክሽ ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤-ከነጋ ፡ በኋላ ፡ ሌሎች ፡ ሰዎች ፡ መሆ
ናቸውን ፡ ባወቅሁ ፡ ጊዜ ፡ እጮኽ ፡ ዠመር ፤ እነዚያ ሁለት ፡
ወንበዴዎች ፡ ይህች ፡ ልጅ ፡ እንደዚህ ፡ ስትጮኽ ፡ የሰማና ፡
የተያዝን ፡ እንደሆን ፡ እንሰቀላለን ፡ በረሓ ፡ በረሓውን ፡ ይዘናት፡
እንሂድ ፡ ብለው ፡ በበረሓ ፡ ውስጥ ፡ እግር ፡ እግሬን ፡ እየገረፉ፡
ይዘውኝ ፡ ይሮጡ ፡ ዠመር ።

እናቴ ፡ በውነት ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ የኔን ፡ መከራ ፡ ቢያዩ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሰው ፡ ሆኖ ፡ መፈጠር ፡ አያስፈልግም ፡ ይሉ ፡ ነበር ። ይቶት ፤—ወሰዱና ፡ ምን ፡ አደረጉሽ ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤ —ወሰዱና ፡ ላንዲት ፡ ወይዘሮ ፡ ኑሬቱ ፡ ለሚባሉ ፡ ሴት ፡ አልዩ ፡ አምባ ፡ ሸጡኝ ። ይቶት ፤-ሴትዮዋ ፡ ደግ ፡ ሴት ፡ ኖረዋልን ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤ ይህነን ፡ ይተዉኝ ፡ ወይዘሮ ፡ ኑሬቱ ፡ የሚባሉ በምድር ፡ ዲያብሎስ ፡ ናቸው ፤ ወፍራም ፡ ሽፋላቸው ፡ የቀጭኔ ፡ ጭራ ፡ የመሰለ ፡ ከጧት ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ እንደ ፡ ተቈጡ ፡ የሚውሉ ፤ ስለዚህ ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ አሽከርነት ፡ የሚገባላቸው ፡ የለም ፤ ቤታቸውም ፡ ከሰው ተለይተው ፡ ካፋፍ ፡ ላይ ፡ ነው ። ውሃውም ፡ ከቤታቸው ፡ ፳ ፡ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ይሆናል ፤ እናቴ ፡ ይሽውልዎ ፡ የዚህን ፡ ሁሉ ፡ መከራና ፡ ሥቃይ ፡ ጽኑ ፡ ሥራ ፡ በትር ፡ ችዬ ፡ ኖርኩ ። ይቶት ፤-እንደ ፡ ምን ፡ ወደዚህ ፡ ለማምለጥ ፡ ቻልሽ ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤—ታሪኩ ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ ባጭሩ ፡ የቡሔ ፡ ለት ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ሲዘፍኑ ፡ የወይዘሮ ፡ ኑሬቱም ፡ ልጆች ፡ እየዘፈኑ ፡ ከናታቸው ፡ ከወይዘሮ ፡ ኑሬቱ ፡ ጎብስት ፡ ተቀብለው ፡ ሲበሉ ፡ እኔ ፡ እናቴና ፡ አባቴ ፡ ትዝ ፡ እያሉኝ ፡ ሳለቅስ ፡ አይተው ፡ አንቺ ፡ ምናምንቴ ፡ ባሪያ ፡ ከልጆች ፡ ጋራ ፡ መጫወት ፡ አምሮሽ ፡ ነው ፡ የምታለቅሽው ፡ ቈይ ፡ አሳይሻለሁ ፡ ብለው ፡ ለወንድማቸው ፡ ፈረስ ፡ ውሃ ፡ ቀድቼ ፡ እንድመጣ ፡ በውድቅት ፡ በዝናም ፡ እኔን ፡ የሚያክል ፡ ባልዲ ፡ ተሸክሜ ፡ እወንዝ ወረድሁ ፤ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ውሃውን ፡ ቀድቼ ፡ ለማውጣት ፡ ባነሣው ፡ እኔም ፡ ውሃውም ፡ ወደቅን ፤ ልብሴ ፡ በሰበሰ ፡ ብርድም ፡ ያዘኝ ፡ አውሬዎቹም ፡ ከየደኑ ፡ በጮኹ ፡ ጊዜ ፡ ጨነቀኝና ፡ እጮኽ ፡ ዠመር ፤ ኋላም ፡ በዜማ ፡ አለቅስ ፡ ነበር ። ይቶት ፤-እባክሽ ፡ እንደ ፡ ምንድነው ፡ ዜማው ። ፍሬ ሕይወት ፤—በዜማ ፡ ያለቀስኩት ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ወይ ፡ እኔ ፡ ወይ ፡ እኔ ፡ ወይ ፡ እኔ ።

ውሃዬን ፡ ቀድቼ ፡ ለመሄድ ፡ ስጥር ፡
አውሬ ፡ አስደንግጦኝ ፡ ወደቅሁኝ ፡ ከዳር ።
ውሃውም ፡ ፈሰሰ ፡ ልብሴም ፡ በሰበሰ ።



በብርድ ፡ ተንቀጠቀጥሁ ፡ ራስሁ ፡ እስካጥንቴ ፤
ወይ ፡ እኔ ፡ ወይ ፡ እኔ አላየሽ ፡ እናቴ ።
በውድቅት ፡ ጨለማ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ብርድ ፡
ደርሶብኝም ፡ አያውቅ ፡ የዚህ ፡ ዐይነት ፡ ጕድ ።
ወዴት ፡ እደርስ ፡ ይሆን ፡ እኔ ፡ ድኻዪቱ ፤
ከዚህም ፡ እንዳልቀር ፡ አውሬው ፡ ማስፈራቱ ።
ባዶ ፡ እጄን ፡ እንዳልሄድ ፡ ሞት ፡ ይጠብቀኛል ፤
ጨካኝዋ ፡ እመቤቴ ፡ ሥቃይ ፡ ያሳዩኛል ።
አባቴና ፡ እናቴ ፡ ይህነን ፡ ቢሰሙ ፤
ልጅ ፡ ያገኙበትን ፡ (ቀን) ፡ እንዴት ፡ በረገሙ ።

ወይ ፡ እኔ ፡ ወይ ፡ እኔ ፡ ወይ ፡ እኔ ፡ ወዴት ፡ ልድረስ ። ይቶት ፤—አገሚቸውን ፡ ይዘው ፡ እያለቀሱ ፡ አባትና ፡ እናት ፡ የለሽ ፡ ማን ፡ ይደርስልሽ ፡ ይሆን ፡ ፍሬ ፡ ሕይወት ፤—አንድ፡ ገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚባል ፡ ልጅ ፡ ጩኸቴ ፡ አሳዝኖት ፡ በሩቅ ፡ እሱም ፡ በዜማ ፡ ምንድነው ፡ ይህ ፡ ነገር ።

ብዙ ፡ የጭንቅ ፡ ድምፅ ፡ በሩቅ ፡ እሰማለሁ ፤
ይህነን ፡ ለማወቅ ፡ እገሠግሣለሁ ።
ባትሪዬን ፡ ላብራና ፡ ልፈልግ ፡ በጣም ፤
ድምፅ ፡ ያለመጨነቅ ፡ እንዲህ ፡ አይጮኽም ።

እያለ ፡ መብራቱን ፡ እያበራ ፡ መጥቶ ፡ ለምንድነው ፡ እንደዚህ ፡ የምትጮኺው ፡ ብሎ ፡ ጠየቀኝ ። እኔም ፡ ችግሬን ፡ ሁሉ ፡ በሰ ፊው ፡ ካስረዳሁት ፡ በኋላ ፡ ይገርሽ ፡ ልሂድ ፡ አለኝ ፤ ከዚህ ፡ አልሄድም ፡ እዚሁ ፡ እሞታለሁ ፡ ስል ፡ በግድ ፡ ተሸክሞ ፡ እኔን፡ ዕድሉ ፡ ቢሷን ፡ ከባርነት ፡ ነጻ ፡ ለማውጣት ፡ ወደ ፡ አዳል ፡ በረሓ ፡ ገሠገሠ ።

ባጭሩ ፡ ነገሬን ፡ ሳላስረዝም ፣ የኔ ፡ ወዳጅ ፡ ገብረ ፡ እግዚ አብሔር ፡ መንፈሳዊ ፡ ጨዋታ ፡ እያወጋኝ ፡ ወደዚህ ፡ ተራራ ፡ ለመ ድረስ ፡ ሲናፍቅ ፡ በጨካኞች ፡ አዳሎች ፡ እጅ ፡ ሞተብኝ ። በዚያ ፡ በረሓ ፡ የሚያጽናናኝ ፡ ሰው ፡ ሳይኖር ፡ የወዳጄን ፡ ሬሳ ፡ ተጋድሞ ፡

በማየቴ ፡ እንደ ፡ ዕብድ ፡ ሆኜ ፡ ስወድቅ ፡ ስነሣ ፡ ከዚህ ፡ ደረስሁ ፡ ይኸውልዎ ፡ እናቴ ፡ ባጭሩ ፡ የኔ ፡ ታሪክ ። እንግዴህ ፡ ድፍረት ፡ አያድርጉብኝና ፡ የርስዎን ፡ ታሪክ ፡ እንድጠይቅዎ ፡ ይፍቀዱልኝ። ይቶት ፡ -በደስታ ፡ ለጥያቄሽ ፡ መልስ ፡ እሰጣለሁ ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤-አገርዎ ፡ ወዴት ፡ ነው ። ይቶት ፤ አገሬ ፡ በጣም ፡ ሩቅ ፡ ነው ፡ ብነግርሽም ፡ አታውቂውም ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፡ ባል ፡ አግብተው ፡ ልጅ ፡ ወልደው ፡ ኖረዋልን። ይቶት ፤-አዎን ፡ ባል ፡ አግብቼ ፡ ልጅ ፡ ወልጄ ነበር ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤-እንግዲያው ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ባልዎንና ፡ ልጅዎን ፡ ትተው ፡ ወደዚህ መጡ ፤ ይቶት ፤-የመጣሁበት ፡ ምክንያት ፡ በጣም ፡ የሚያሳዝን ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በሥራት ፡ ስሚኝ ፤ እኔና ፡ ባለቤቴ ፡ ካረጀን ፡ ወዲህ ፡ አንዲት ፡ ልጅ ፡ ወለድን ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ የነበረውን ፡ ደስታ ፡ ላወራልሽ ፡ አልችልም ፤ ባሌም ፡ ቤታቸው ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ አጠገብ ፡ ካፋፍ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፤ ዘወትር ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሲመለሱ ፡ ያችን ፡ በስተርጅና ፡ ያገኙዋትን ፡ ልጅ ፡ ከጐናቸው ፡ አስቀምጠው ፡ ያገሩን ፡ ከፍና ፡ ዝቅ ፡ ያሉ ፡ ተራሮች ፡ አረንጓዴ ፡ በሆኑ ፡ ለምለም ፡ ሣሮች ፡ ተሸፍነው ፡ በትንንሽና ፡ በትልልቅ ፡ ዛፎች ፡ ተከበው ፡ ብዙ ፡ ወንዞችና ፡ ፏፏቴዎች ፡ በተራራው ፡ ላይ ፡ ሲፈሱ ፡ ከፀሓዩ ፡ ውጋጋን ፡ ጋራ ፡ የመሬቱን ፡ ልዩነት ፡ ቀለም ፡ በማየት ፡ የአንክሮ ፡ ጸሎት ፡ ያደርጉ ፡ ነበር ። ይልቁንም ፡ ሰሶችና ፡ ሚዳቋዎች ፡ ከግልገሎቻቸው ፡ ጋራ ፡ ሲራወጡ ፡ በማየት ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ አመሰግንሃለሁ ፡ ይህችን ፡ ልጅ ፡ የሰጠኸኝ ፡ መካን ፡ በሆንኩበት ፡ ዘመን ፡ ስንኳን ፡ በሰዎችና ፡ በእንስሶችም ፡ ልጆች ፡ እቀና ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ደስታዬን ፡ ስለ ፡ መላኽልኝ ፡ ላንተ ፡ ምን ፡ ዋጋ ፡ እከፍልኻለሁ ፡ እያሉ ፡ የደስታ ፡ ዕንባ ፡ ያፈሱ ፡ ነበር ። እኔም ፡ ባሌም ፡ ያችን ፡ የመካን ፡ ልጃችንን ፡ ዘወትር ፡ እንደሚሰበር ፡ ብርጭቆ ፡ እንጠብቃትና ፡ እንሣሣላታለን ፤ እውጭም ፡ በወጣች ፡ ጊዜ ፡ ተመልሳ ፡ እስክትገባ ፡ ድረስ ፡ መኖሯን ፡ አናምንም ፤ ሌሊትም ፡ ከመካከላችን ፡ የጠፋች እየመሰለን ፡ ያችን ፡ የብርቅ ፡ ልጃችንን ፡ ስንዳብስ ፡ የኔና ፡ የባሌ ፡ እጅ ፡ ይገናኛል ፤ ልጅቷም ፡ በውነት ፡ የምታሣሣ ፡ መልከ ፡ መልካም ፡ ዐመለ ፡ ቅን ፡ ነበረች ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤-ከዚህ ፡ በኋላስ ፡ ያች ፡ ልጅ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ሆነች ። ይቶት ፤-ልጄ ፡ ሆይ ፡ የሰው ፡ ደስታው በመልካም ፡ አይፈጸምምና ፡ ያች ፡ እንደ ፡ ዐይን ፡ ብሌን ፡

የምንጠነቀቅላት ፡ ልጃችን ፡ ጠፋችብን ፤ በዱር ፡ በገደልም ፡ ብንፈ ልጋት ፡ አጣናት ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ያች ፡ ደስታ ፡ የመላባት ፡ ጕዠዋችን ፡ በኀ ዘን ፡ ጨለማ ፡ ተዋጠች ። ባሌም ፡ ከልጃቸው ፡ መጥፋት ፡ ወዲህ ፡ ከፋፍ ፡ ላይ ፡ ሆነው ፡ ሲመለከቱ ፡ ማሩም ፡ ዛፉም ፡ ውሃውም ፡ የልጃቸው ፡ ደመኛ ፡ ስለ ፡ መሰላቸው ፡ እያለቀሱ ፡ ልጃቸውን ፡ በዕንባቸው ፡ ጭጋግ ፡ ውስጥ ፡ እያዩዋት ፡ እባክሽ ፡ ክልቤ ፡ ጥፊ ፡ ካይኔም ፡ ራቂ ፡ እያሉ ፡ ሲጮኹ ፡ በኀዘን ፡ ምክንያት ፡ በሽታ ፡ ወድቀው ፡ ሞቱ ። ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ እኔም ፡ ከልጄ ፡ መጥፋትና ፡ ከባሌ ፡ መሞት ፡ ወዲያ ፡ ቤቴ ፡ ለኔ ፡ አልተፈቀደችልኝም ፡ በማ ለት ፡ በውጭ ፡ በኩል ፡ ዘግቼባት ፡ ቤቴ ፡ ደኅና ፡ ሰንብች ፡ ብዬ ፡ መጣሁ ። ይኸውልሽ ፡ ልጄ ፡ ፍሬ ፡ ሕይወት ፡ ሆይ ፡ በዚህ ፡ ምክ ንያት ፡ ነው ፡ ከዚህ ፡ የደረስኩት ።

ፍሬ ፡ ሕይወት ፤–እማማ ፡ እማማ ፡ እማማ ፡ እባክዎን ፡ አባቴም ፡ አገሬም ፡ ወለል ፡ ብለው ፡ ታዩኝ ፡ ስምዎን ፡ ይንገሩኝ ፡ ይህ ፡ ታሪክ ፡ የኔ ፡ ይመስላል ፡ እያለች ፡ ታለቅስ ፡ ዠመር ። ይቶት ፤– አንገቷን ፡ ይዘው ፡ አንቀው ፡ እየሳሙ ፡ አታልቅሽ ፡ እኔ ፡ እናትሽ ፡ ወይዘሮ ፡ በላይነሽ ፡ ነኝ ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤–እኔም ፡ ልጅዎ ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ነኝ ፡ ብላ ፡ አንገታቸውን ፡ ይዛ ፡ እያለቀሰች ፡ እንግዴህ ፡ እማማ ፡ ላልቅስ ፤ ወይም ፡ ልሣቅ ፡ አንቺን ፡ አገኘሁሽ ፡ አባባም ፡ ሞተ ። ይቶት ፡ በላይነሽ ፤–በዚህ ፡ ዓለም ፡ አታልቅሽም ፡ አትሣ ቂም ፡ ይልቅስ የዚህን ፡ ተራራ ፡ ዘፈን ፡ እንዝፈን ፡ ።

ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ማዕበል ፡ ታግሎ ፡ የሚዘልቅ ፡
ጕርፍ ፡ በላዩ ፡ ሲሄድ ፡ ነጐድጓድ ፡ ሲበርቅ ፡
ሲሰጥምም ፡ ሲወጣ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ሲታገል ፡ ከነፋሱ ፡ ጋራ ፡
መናኒ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ለመውጣት ፡ የሚችል ፡ ወደዚህ ፡ ተራራ ።
የሰው ፡ ብርቱ ፡ ፈቃድ ፡ ተዋግቶም ፡ ተዳምቶ ፡
ይደርሳል ፡ ካሰበው ፡ አይቀርም ፡ ሰው ፡ ፈርቶ "
በብርቱ ጭንጫ ፡ ላይ ፡ የተሠራ ፡ ቤት ፡
እንዲህ ፡ በሚያልፍ ፡ ጕርፍ ፡ አይወድቅም ፡ በጥቂት ።
የዚህ ፡ ዓለም ፡ ማዕበል ፡ ምንም ፡ ሳይነካው ፤
በላዩ ፡ የሄደ ፡ እሱ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ዳዊት ፡ አባታችን ፡ ጮኸ ፡ ተናገረ ፤
ማዕበልና ፡ ጐርፍ ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ ሲሄድ ፡ ስለ ፡ ተቸገረ ።
የእግዚአብሔርን ፡ ልጅ ፡ ያመጣ ፡ ፍቅር ፤
አንቺን ፡ ስቦ ፡ አመጣሽ ፡ እኔን ፡ ለመጦር ፡ ብለው ፡ ተቃቀፉ ።



ይቶት ፡ በላይነሽና ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ በናፍቆት ፡ ሰቀቀንና ፡ በደስታ ፡ ተቃቅፈው ፡ ሲላቀሱ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አባ ፡ ኖኅተ ፡ ብርሃን ፡ ስለ ፡ ይቶት ፡ በላይነሽ ፡ ሌሊቱን ፡ ራእይ ፡ አይተው ፡ ኖሮ ፡ ሊጠይቋቸው ፡ ማልደው ፡ መጡ ። በሩን ፡ ከፍተው ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ ይቶት በላይነሽ ፡ ከፍሬ ፡ ሕይወት ፡ ጋራ ፡ አንገት ፡ ላንገት ፡ ተቃቅፈው ፡ ከልጋቸው ፡ ላይ ፡ ተጋድመው ፡ ሲያለቅሱ ፡ ደርሱ ። አባ ፡ ኖኅተ ፡ ብርሃን ፡ በጣም ፡ ደንግጠው ፣ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ቆመው ፡ ከተመለከቱ ፡ በኋላ ፡ እማሆይ ፡

መቼም ፡ አይነጋገሩም ፡ በማለት ፡ ፍሬ ፡ ሕይወትን ፡ ምንድር ፡ ነው ፡ እንደዚህ ፡ ተቃቀፋችሁ ፡ የትምላቀሱት ። ፍሬ ፡ ሕይወት ፤ -ብፁዕ ፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡ ቸሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚገርም ፡ ተአምራት ፡ ስለ ፡ ሠራልን ፡ የደስታና ፡ የናፍቆት ፡ ልቅሶ ፡ እናላቅሳለን ።

ብፁዕ ፡ አባታችን ፡ እንደሚገነዘቡት ፡ መዠመሪያ ፤ ከዚህ ፡ ተራራ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ረድኤት ፡ ተመርቼ ፡ በደረስሁ ፡ ጊዜ ፡ ብፁዕ ፡ አባታችን ፡ እኒህን ፡ ይቶትን ፤ ለማገልገል ፡ ሲመርጡኝ ፡ እንደ ፡ እናትሽ ፡ በቅን ፡ ኅሊና ፡ እንድታገለግያቸው ፡ ብለውኝ ፡ ነበር ፤ እኔም ፡ በተቻለኝ ፡ አኳኋን ፡ በቅን ፡ ኅሊና ፡ እናቴን ፡ እየመሰሉኝ ፡ አገለገልኳቸው ። ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ በተቀደሰ ፡ ጥበቡ ፡ ከዚህ ፡ ያመጣኝ ፡ እንደ ፡ ዓይን ፡ ብሌን ፡ የሚሣሡልኝንና ፡ የሚወዱኝን ፡ እናቴን ፡ ለመጦር ፡ ኖሯል ።

አባ ፡ ኖኅተ ፡ ብርሃን ፤–ምን ፡ የማይመስል ፡ ነገር ፡ ትናገሪያለሽ ፡ እናትሽ ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ በምን ፡ ዐወቅሽው ፡ እማሆይ ፡ ድዳ ፡ በመሆናቸው ፡ ምክንያት ፡ አይነጋገሩ ፡ ማን ፡ ነገረሽ ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ይቶት ፡ በላይነሽ ፡ ከንገታቸው ፡ ቀና ፡ ብለው ፡ ብፁዕ ፡ አባታችን ፡ ርግጥ ፡ ፍሬ ፡ ሕይወት ፡ ልጄ ፡ ነች ፡ የቀድሞ ፡ ስሟም ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ነው ፡ ከዚህ ፡ ተራራ ፡ መንኜ ፡ የመጣሁትም ፡ ስለሷ ፡ መጥፋትና ፡ ባሌም ፡ በልጃቸው ፡ ኀዘን ፡ ምክንያት ፡ ስለ ፡ ሞቱብኝ ፡ ነው ። እንደ ፡ ድዳ ፡ ሆኜ ፡ ይህነን ፡ ያኽል ፡ ዓመት ፡ የተቀመጥሁት ፡ ከልጄ ፡ መጥፋትና ፡ ከባሌ ፡ መሞት ፡ ወዲህ ፡ ዐይኔ ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ እንዳያይ ፤ አፌም ፡ ክፉና ፡ በጎም ፡ እንዳይናገር ፤ በሕርመት ፡ ጾም ፡ ዘግቻቸው ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ የሰው ፡ ፍቅር ፡ ስቦ ፡ ወደዚህ ፡ ዓለም ፡ ያመጣው ፡ ቸሩ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ልጄን ፡ ሳላውቃት ፡ እንዳልሞት ፡ ዛሬ ፡ ሌሊት ፡ በሕልሜ ፡ መልአኩን ፡ ልኮ ፡ ይህች ፡ የምታገለግልሽ ፡ ልጅ ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ ነችና ፡ አፍሽን ፡ ከፍተሽ ፡ ተናገሪ ፡ ብሎ ፡ አዘዘኝ ። ብፁዕ ፡ አባታችን ፡ ሆይ ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ በማልኩት ፡ መሐላ ፡ ምክንያት ፡ ሳላነጋግርዎ ፡ በመቈየቴ ፡ ይቅር ፡ ይበሉኝ ፡ ብለው ፡ ከእግራቸው ፡ ሥር ፡ ወደቁ ። አባ ፡ ኖኅተ ፡ ብርሃንም ፡ በጣም ፡ ተገርመው ፡ ምን ፡ በደሉኝና ፡ ይቅርታ ፡ ይጠይቁኛል ፡ ከመናገር ፡ አለመናገር ፡ ይሻላል ፡ በማለት ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ የማይቻለውን ፡ የዝምታና ፡ የአርምሞ ፡

ጾም ፡ በማድረግዎ ፡ የተመሰገኑ ፡ ነዎት ፤ ይህ ፡ በገዳማችን ፡ የተደ
ረገው ፡ ተአምራት ፡ ለኛ ፡ ዋና ፡ መመኪያ ፡ ነው ። እኔም ፡ ይህነን ፡
ያሰማኝን ፡ ቸሩ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እያመሰገንሁ ፡ ስለናንተም ፡
ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ጸሎት ፡ ማድረግ ፡ ይገባኛል ፡ ብለው ፡ በጉልበታቸው
ተንበርክከው ፡ ከጸለዩ ፡ በኋላ ፡ ሁለቱንም ፡ ባርከው ፡ ወደ ፡ በአታቸው ፡ ሄዱ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ያይኔ ፡ አበባ ፡ መንኵሳ ፡ ከናቷ ፡ ጋራ ፡ በዚሁ ፡
ገዳም ፡ ተቀመጠች ። ሁለቱም ፡ እግዚአብሔርን ፡ እያመሰገኑ ፡ በቅ
ዱስ ፡ ኑሮ ፡ ሰማያዊ ፡ ነገር ፡ እያሰቡ ፡ ጥቂቶች ፡ ዓመቶች ፡ ከተቀ
መጡ ፡ በኋላ ፡ ባንድነት ፡ ታመው ፡ ዐረፉ ፡ ካባቶቻቸውም ፡ ከመ
ናንያን ፡ ጋራ ፡ በሰላም ፡ አንቀላፉ ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ እንሆ ፡ መከራ ፡ የጽድቅ ፡ ማጣሪያ ፡ መሆኑ
ንና ፡ የሰው ፡ ጽኑ ፡ ፈቃድና ፡ ሃይማኖት ፡ ካሰቡት ፡ ቦታ ፡ እንደ
ሚደርስ ፡ ይህ ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ ይገልጻል ።



# የደም ፡ ድምፅ ፡፡

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ በሰማዕትነት ፡ ሲሞቱ ፡

የሚያሳይ ፡ ቲያትር ፡፡

ታርሞ ፡ አራተኛ ፡ ታተመ ፡፡

# የደም ፡ ድምፅ ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

ክቡር ፡ እምክቡራን ፡ ግራዚያኒ ፡ ማርሻል ፡ ግራዚያኒ ።

ግራዚያኒ ፡ ደወል ፡ ይደውላል ፤ አሽከር ፡ ይገባል ። ግራዚያኒ፡ መኳንንቱን ፡ ጥራ ፡ ይላል ። አሽከር ፡ መኳንንቱን ፡ ይጠራል ። መኳንንቱ ፡ ይመጣሉ ።

ግራዚያኒ ፡ ተቀመጡ ፡ ይልና ፡ ይቀመጣሉ ።

ግራዚያኒ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ በሰላሌ ፡ ያሉትን ፡ ሽፍቶች ፡ አስከትለው ፤ ከደጃዝማች ፡ አበራና ፡ ከደጃዝማች ፡ አስፋ ፡ ወሰን፡ ጋራ ፡ ሲያስጨንቁን ፡ የነበሩት ፡ ተያዙ ፡ እንግዲህ ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡ ይሻላል ።

ጀኔራል ፡ ማሌቲ ፤—ክቡር ፡ ሆይ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ በ፲፱፻ ፳ ዓ. ም. በቅዱስ ፡ ማርቆስ ፡ ወንበር ፡ ካለው ፡ በትረያርክ ፡ ጳጳስነት ፡ የተቀበሉና ፡ መንዝና ፡ ወሎን ፡ በመንፈሳዊ ፡ አስተዳደር ፡ የሚጠብቁ ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ሰው ፡ ስለሆኑ ፡ እሳቸውን ፡ መገደል ፡ በዓለም ፡ ሁሉ ፡ ኀሊና ፡ ያስፈርድብናል ፤ ስለዚህ ፡ ስለጥፋታቸው ወቅሶ ፡ የቢክቶርዮ ፡ ዔማኑኤልን ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥነታቸውን ፡ አስፈርሞ ፡ ለመስበኪያ ፡ ብዙ ፡ ገንዘብ ፡ ሰጥቶ ፡ መሣሪያ ፡ ማድረግ ፡ የተሻለ ፡ ይመስለኛል ።

ግራዚያኒ ፤—የኔም ፡ አሳብ ፡ የጀኔራል ፡ ማሌቲን ፡ አሳብ ፡ ይደግፋል ።

ጀኔራል ፡ ጋሊኒ ፤—እኔ ፡ በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ አሳብ ፡ አልስማማም ፡ ምክንያቱም ፡ ከፋሽስት ፡ መሠረት ፡ የወጣ ፡ የስንፍና ፡ ፖለቲካ ፡ ስለሆነ ፡ ነው ።

የኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ከሦስት ፡ ሺሕ ፡ ዘመን ፡ የሚበልጥ ፡ በነፃነቱና ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ክብር ፡ የሚኰራ ፡ መሆኑን ፡ አለመርሳት ፡ ይገባናል ። አሁኑኑ ፡ ከነዚህ ፡ መምህራኖች ፡ የሚሰማው፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ እስከ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ይመለሳሉ ፡ የሚባል ፡ ስብከት ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ልብ ፡ በገንዘብ ፡

እመልሳለሁ ፡ ማለት ፡ በገንዘብ ፡ ላይ ፡ በከንቱ ፡ መፍረድ ፡ ነው ። ቢሆንም ፡ ባይሆንም ፡ እንደዚሁ ፡ በየምክንያቱ ፡ መፍጀትና ፡ ማሳ ነስ ፡ የተሻለ ፡ ነው ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስንም ፡ ለሕዝቡና ፡ ለቤተ ፡ ክህነቱ ፡ ሁሉ ፡ ማስፈራሪያ ፡ እንዲሆኑ ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ መደብደብ ፡ ዋና ፡ ጥቅም፡ መስሎ ፡ ይታየኛል ።

ግራዚያኒ ፤—የለም ፡ ይህ ፡ የማይሆን ፡ ነው ፤ ምክንያቱም ፡ የፋሽስት ፡ መንግሥት ፡ ምንም ፡ መሠረታዊ ፡ አሳቡ ፡ የኢትዮጵያን ሕዝብ ፡ በየምክንያቱ ፡ መፍጀትና ፡ ማሳነስ ፡ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ ለጊ ዜው ፡ የኢትዮጵያን ፡ መንግሥት ፡ በኀይል ፡ በመደምሰሳችን ፡ የዓ ለም ፡ ኅሊና ፡ ፈርዶብናል ። ስለዚህ ፡ መንግሥቱ ፡ እስኪታወቅ ልን ፡ ድረስ ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ሰው ፡ ብንታገሥ፡ የተሻለ ፡ ነው ። ይልቁንም ፡ የቢክቶሪዮ ፡ ዔማኑኤልን ፡ የኢትዮ ጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትነታቸውን ፡ አምነው ፡ ከፈረሙና ፡ ገንዘብ ፡



አቡነ ፡ ጴጥሮስን ፡ ግራዚያኒ ፡ ለፋሽስት ፡ እንዲገዙ ፡ እንደለመናቸው ።

ሰጥተናቸው ፡ እንዲሰብኩልን ፡ ከሆነ ፡ ለጊዜው ፡ በጣም ፡ መልካም፡ ይመስለኛል ፤ እስኪ ፡ እናንተ ፡ ውጡና ፡ ለብቻዬ ፡ ልጠይቃቸው ።

ግራዚያኒ ፡ ደወል ፡ ይደውላል ፡ አሽከር ፡ ይገባል ። ግራዚያኒ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስን ፡ አስገባ ፡ ይላል ፡ አሽከር ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስን ፡ ይግቡ ፡ ይላል ። አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ይገባሉ ።

ግራዚያኒ ፤—ብፁዕ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ሆይ ፡ ስለምንድነው ፡ ለጣልያን ፡ መንግሥትና ፡ ለገናናው ፡ ሙሶሊኒ ፡ አልገዛም ፡ ብለው ፡ ለጳጳስ ፡ በማይገባው ፡ ሕግ ፡ ከደጃዝማች ፡ አበራና ፡ ከደጃዝማች ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ ጋራ ፡ ሊወጉን ፡ የመጡት ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡—ክቡር ፡ ሆይ ፡ እኔ ፡ የጦር ፡ አለቃ ፡ አይደለሁም ፤ ለመዋጋትም ፡ አልመጣሁም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ስላገሬና ፡ ስለ ፡ ሃይማኖቴ ፡ ስለ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቴ ፡ ክብር ፡ ለመሞት ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ የመጣሁት ።

ግራዚያኒ ፤—ቢሞቱ ፡ ምን ፡ ይጠቀማሉ ፤ ማንንስ ፡ ይጎዳሉ ። አያውቁምን ፡ ገናናው ፡ ሙሶሊኒ ፡ ዓለምን ፡ ሊገዛ ፡ እንደ ፡ ቃጣ ፡ የማንም ፡ ብርታት ፡ የሱን ፡ አሳብ ፡ ሊቃወም ፡ አይችልም ፡

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤—ዐውቃለሁ ፡ ምንም ፡ ለማድረግ ፡ እንደማልችል ።

ነገር ፡ ግን ፡ ላገሬ ፡ ደሚ ፡ በመሬቴ ፡ ላይ ፡ ቢፈስ ፡ ጥቅም ፡ እንዲሆን ፡ አምናለሁ ፤ ዐውቃለሁም ። ክቡር ፡ ሆይ ፡ ያውቃሉን ፡ የደም ፡ ድምፅ ፡ አየርን ፡ ሰንጥቆ ፡ እንዲወጣ ፡ ዕንባም ፡ የነፍስ ፡ ደም ፡ ተራራን ፡ ሁሉ ፡ እንዲፈነቅል ፡ እንዳሉት ፡ ርግጥ ፡ ነው ፡ ገናናው ፡ ሙሶሊኒ ፡ ዓለምን ፡ ሊገዛ ፡ እንደቃጣ ።

ደግሞ ፡ ከዚህ ፡ መጨረሻው ፡ ምን ፡ እንደሆነ ፡ በቅርብ ፡ ይታየኛል ፡ እንድጨርሰውም ፡ ክቡርነትዎ ፡ ይፈቅድልኛል ።

ግራዚያኒ ፤—ይጨርሱ ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤—ገናናው ፡ ሙሶሊኒ ፡ አሁን ፡ የሚሠሩት ፡ ግፍ ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ አይደለም ፤ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ በዱሮው ፡ በሮማውያን ፡ መንግሥት ፡ እጅግ ፡ ጨካኞችና ፡ እብሪተኞች ፡ ነገሥታት ፡ ተነሥተው ፡ ዓለምን ፡ ያስጨንቁ ፡ ነበር ። በነሱ ፡ ክፋትና ፡ እብሪት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ብዙ ፡ ልጆች ፡ ወለደች ፡ ከነዚሁ ፡ ከሮማውያን ፡ ነገሥታት ፡ አንዱ ፡ ኔሮን ፡ የሚባለው ፡ የእብሪቱ ፡ ብዛት ፡ ቤት ፡ ሲቃጠል ፡ ማየት ፡ አምሮኛል ፡ ብሎ ፡ የሮማን ፡

ከተማ ፡ በማቃጠሉ ፡ በገዛ ፡ ሕዝቡ ፡ ተደብድቦ ፡ በውርደት ፡ ሞተ የገናናው ፡ ሙሶሊኒም ፡ ዕድል ፡ እንደዚሁ ፡ ሁሉ ፡ ሳይሆን ፡ አይ ቀርም ።

ግራዚያኒ ፤—ወይግሩም ፡ ከተወለድኩ ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ እንደርስዎ ፡ ያለ ፡ ደፋር ፡ አላየሁም ፡ በማን ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ቆመው ፡ ነው ፡ ገናናው ፡ ሙሶሊኒን ፡ የሚሰድቡ ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤—ክቡር ፡ ሆይ ፡ ስለጠየቁኝ ፡ ቃል ፡ ባጭሩ ፡ በኔው ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ቆሜ ፡ ነው ፡ የምናገረው ።

ነገር ፡ ግን ፡ የጣልያን ፡ መሬት ፡ ነች ፡ ብለው ፡ ስላስታወቁኝ ለኢትዮጵያ ፡ እስክትመለስ ፡ ድረስ ፡ ሞትን ፡ መርጫለሁ ፡ በጠ ላት ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ልመላለስ ፡ አልፈቅድም ።

ግራዚያኒ ፡—ስቆ ፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡ ከመሞት ፡ መሰንበት ፡ ይሻ ላል ፤ ይልቁንስ ፡ የቪክቶርዮ ፡ ዔማኑኤልን ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትነታቸውን ፡ አምነው ፡ ፈርመው ፡ በፍጹም ፡ ልብዎ ፡ ለደጉ ፡ ጣልያን ፡ መንግሥት ፡ እንዲያገለግሉና ፡ ለመስበኪያም ፡ ብዙ ፡ ገን ዘብ ፡ እንድንሰጥዎት ፡ ቢደረግ ፡ በጣም ፡ የተሻለ ፡ ነው ፤ ምክሬን ይስሙኝ ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤—ክቡር ፡ ሆይ ፡ ማነው ፤ ዕብድ ፡ ከሆነ ፡ ሰው ፡ በቀር ፡ እናቱን ፡ ለገደለበት ፡ ባለጋራ ፡ የልብ ፡ አገልጋይ ፡ የሚሆን ፡ ለመስበኪያ ፡ የሚሆን ፡ ብዙ ፡ ገንዘብ ፡ ይሰጥዎታል ፡ ስላሉን ፡ በጣም ፡ አዘንኩ ።

ማን ፡ ሰው ፡ ነው ፤ አእምሮ ፡ ከሌለው ፡ ሰው ፡ በቀር ፡ ለራሱ መግደያ ፡ መርዝ ፡ በብዙ ፡ ገንዘብ ፡ የሚገዛ ።
አሁንም ፡ ለክቡርነትዎ ፡ የመጨረሻ ፡ ቃሌን ፡ የምሰጥዎ ፡ ገንዘብዎ ፡ ለራስዎ ፡ ለጥፋትዎ ፡ ይሁን ፤ እኔ ፡ ሃይማኖቴንና ፡ አገ ሬን ፡ በገንዘብ ፡ አልሸጥም ።

ብዙ ፡ ኋርናውን ፡ ለሙብል ፡ እንደሸጠ ፡ እንደ ፡ ዔሳው ፤ ጌታ ውን ፡ ለገንዘብ ፡ እንደ ፡ ሸጠ ፡ እንደ ፡ ይሁዳ ፡ አልሆንም ፡ ከቀዳ ማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ አላውቅም ።

ግራዚያኒ ፤- አስወጣቸው ፡ ግድ ፡ የለም ፡ የሚደርስብዎትን ፡ መከራ ፡ወደ ፡ፊት ፡ ያገኙታል ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤— ጌታዬን ፡ በገደሉ ፡ በሮማውያን ፡ እጅ ፡ መከራ ፡ መቀበልና ፡ የሱን ፡ መስቀል ፡ ተሸክሜ ፡ መከተል ፡ ደስ፡ ይለኛል ።

ግራዚያኒ፤- ደወል ፡ ይደውላል ፤ አሽከር ፡ ይገባል ። ግራዚያኒ— መኳንንቱን ፡ አስገባ ፡ ይላል ። መኳንንቱ፡ይገባሉ ።ግራዚያኒ፤—፡ ይኸውላችሁ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ የቢ ክቶርዮ ፡ ዔማኑኤልን ፡ የኢትዮጵያን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትነት ፡ አላ ውቅም ፡ አልፈርምም ፡ አሉ ። ስለ ፡ ገንዘብም ፡ መስጠት ፡ ብነግ ራቸው ፡ ላንተ ፡ ለጥፋትኸ ፡ ይሁንኽ ፡ ብለው ፡ ሰደቡኝ ፤ በዕ ድሜዬ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ እንደዚህ ፡ ያሉ ፡ ሐሳብ ፡ ጽኑ፡ ደፋር ፡ ሰው ፡ አላየሁም ፤ ስለዚህ ፡ የኔም ፡ አሳብ ፡ ወደ ፡ መግ ደሉ ፡ አዘነበለ ።

ፍራንካ ፤--ክቡር ፡ ሆይ ፡ እንደዚህ ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ በብር ታታቸውና ፡ በሃይማኖታቸው ፡ ጠንክረው ፡ ሲሞቱ ፡ ሌሎች ፡ ብዙ፡ የሃይማኖት ፡ ልጆች ፡ ይወልዳሉ ፤ መከራና ፡ ሥቃይ ፡ የሚያስ ነሣቸው ፡ ሰዎች ፡ ከደም ፡ በቀር ፡ በሌላ ፡ ነገር ፡ አይመከሩም፤ በደም ፡ የተጣበቀውንም ፡ አንድነት ፡ ማንም ፡ ሊያላቅቀው ፡ አይችልም ።

ስለዚህ ፡ የኒህ ፡ ሰው ፡ መገደል ፡ ለፖለቲካችን ፡ ዕንቅፋት ይሆንብን ፡ ይመስለኛል ።

ማሌቲ ፤-የኔም ፡ አሳብ ፡ እንደ ጄኔራል ፡ ጋሊኒ ነው ።

እንደዚህ ፡ ሆኖ ፡ ነው ፡ አፍሪቃ ፡ የምትገዛው ፡ የኢትዮ ጵያን ፡ ሕዝብ ፡ በመለማመጥ ፡ እንገዛለን ፡ ማለት ፡ ከንቱ ፡ ነው። ደግሞም ፡ ብዙ ፡ ድኾች ፡ ከምንደበድብ ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ ሰው፡ ብንገድል ፡ የሕዝቡን ፡ ልብ ፡ ይሰብረዋል ፡ ስለዚህ ፡ የሥራ ። ጓደኞቼ ፡ ያሳሰቡትን ፡ የፍርሃት ፡ ፖለቲካ ፡ አልስማማበትም ።

ግራዚያኒ ፤—የሁላችሁም ፡ አሳብ ፡ በጣም ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የኔም ፡ አሳብ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ እሺ ፡ ቢሉን ፡ በወገኖቻቸው ፡ አስመክረን ፡የቢክቶርዮ ፡ዔማኑኤልን ፡

የኢትዮጵያ ፡ ንጉሥ ፡ ነገሥትነታቸውን ፡ ካወቁ ፡ ለጊዜው ፡ ብን ተዋቸው ፡ የተሻለ ፡ ይመስለኛል ፡ ስለምን ፡ ሰውዬው ፡ በፊታ ቸው ፡ ላይ ፡ እንደሚታየው ፡ ትልቅ ፡ ታሪክ ፡ በኛ ፡ ላይ፡ ጥለው፡ እንዲሞቱ ፡ የቀረበ ፡ መሆናቸው ፡ ይታወቃል ።

ግራዚያኒ ፤—ደወል ፡ ይደውላል ፤ አሽከር ፡ ይመጣል ። ግራዚያኒ ፡ የተጠሩትን ፡ መኳንንትና ፡ አለቃ ፡ ጥራ ፤ አሽከር ፡ መኳንንትና ፡ አለቃውን ፡ ይጠራል ፤ ግራዚያኒ ፡ ተቀመጡ ፡ ይላል ፤ መኳንንቱና ፡ አለቃው ፡ ይቀመጣሉ ።

ግራዚያኒ ፤—ዛሬ ፡ እዚህ ፡ የተጠራችሁበት ፡ ጉዳይ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ገናናው ፡ የኢጣሊያ ፡ ንጉሥ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሥ፡ ነገሥትነቱን ፡ አላውቅም ፤ ብትምሩኝም ፡ አልማርም ፡ ብለው ፡ ስላስቸገሩን ፡ እንድትመክሯቸው ፡ ብዬ ፡ ነው ።

መኳንንቱና ፡ አለቃው ፤—ክቡር ፡ እምክቡራን ፡ ሆይ ፡ ሰው ፡ ሆኖ ፡ ማነው ፡ ገናናው ፡ ቢክቶርዮ ፡ ዔማኑኤል ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሥ፡ ነገሥት ፡ አይደሉም ፡ የሚል ። አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ የተማሩ ፡ ትልቅ ፡ ሰው ፡ ናቸው ፡ ዕንቢ ይሉን ፡ አይመስለንም ፡ እሺ ፡ እንመክ ራቸዋለን ።

ወደ ፡ እስር ፡ ቤት ፡ ሂዱ፤ዘበኛው ፡ ብፁዕ ፡ አባታችን ፡ አንድ አለቃና ፡ አንድ ፡ መኰንን ፡ ከክቡር ፡ እምክቡራን ፡ ግራዚያኒ ፡ ተልከው ፡ መጥተዋል ፡ አለ ። አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤—ግቡ ፡ በላቸው ።

መልእክተኞች ፤—እንደ ፡ ምን ፡ ሰነበቱ ፡ አባታችን ፡ እንኳን፡ እግዚአብሔር ፡ ከጦር ፡ አደጋ አድኖ ላገርዎ ፡ መሬት አበቃዎ ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤—ወንድሞቼ ፡ ከናንተ ፡ ጋራ ፡ ለመተያየት፡ ያበቃኝ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግናለሁ ። ከጦር ፡ አደጋ ፡ ለመዳኔ ፡ ግን ፡ ኢትዮጵያ ፡ ከጠላት ፡ እጅ ፡ ካልወጣች ፡ ከደጋው ፡ ድኛለሁ ፡ ለማለት ፡ አልችልም ።

አዲስ ፡ አበባ ፡ ዛሬ ፡ የደም ፡ መሬት ፡ ስለ ፡ ሆነች ፤ በእ ግሬ ፡ በመርገጤ ፡ እንኳ ፡ በጣም ፡ አዝኛለሁ ። መምህር፤ -አባ ታችን ፡ ምነው ፡ ብዙ ፡ ነገር ፡ ሲያውቁ ፡ እንደዚህ ፡ ተስፋ ፡ ቈርጠው ፡ ይናገራሉ ። ማነው የኢትዮጵያ ፡ ተወላጅ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ ነፃነቱ ፡ መጥፋት ፡ የማያዝን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በጦር ፡

ኀይል ፡ አንድ ፡ መንግሥት ፡ ከተያዘ ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሰጠው መገዛት ፡ የበለጠ ፡ መሥዋዕትነት ነው ፤ ከመሥዋዕት፡ መታዘዝ ፡ ይበልጣል ተብሏል ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤—መምህር ፡ ሆይ ፡ መታዘዝ ፡ ከመሥዋዕት፡ የሚበልጥበትን ፡ መንፈሳዊ ፡ አስተያየት ፡ አልተመለከቱትም ፤ እን ዲያው ፡ በፊደሉ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ያነበቡልኝ ። ኍራት ፡ የምትሆን፡ ሃይማኖታዊ ፡ መታዘዝ ፡ ስለ ፡ ሃይማኖት ፡ ስላገር ፡ ስለ ፡ ንጉሠ፡ ነገሥት ፡ ክብር ፡ መሥዋዕት ፡ መሆን ፡ ነው ።

ደግሞም ፡ ይህነን ፡ የመሰለውን ፡ መታዘዝ ፡ ስለ ፡ ማልንበት፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ በፍርሃት ፡ ሳይተረጐም ፡ በቃል ፡ ኪዳኑ ፡ መሥ ዋዕት ፡ መሆን ፡ ነው ።

መኰንኑ ፤ —ብፁዕ ፡ አባታችን ፡ እግዚአብሔር ፡ ለሰጠው ፡ ለፋሺስት ፡ መንግሥት ፡ መታዘዝ ፡ ከመሥዋዕት ፡ አይበልጥም ፡ ይላሉን ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤—ክቡር ፡ ሆይ ፡ የሰውን ፡ አገርና ፡ ሕይወት፡ የሚዘርፍ ፡ የሚያጠፋ ፡ ፋሺስት ፡ ምን ፡ ማለት ፡ መሆኑን ፡ ባለ ማወቅዎ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይቅር ፡ ይበልዎ ።

ፋሺስት ፡ አንድ ፡ የሆነ ፡ በክፋት ፡ ማሰሪያ ፡ የተሳሰረ ፡ የሽፍታ ፡ ማኅበር ፡ ማለት ፡ ነው ። ስለ ፡ ምን ፡ ለሽፍታ ፡ መታ ዘዝ ፡ መሥዋዕት ፡ ነው ፡ ይላሉ ፤ ስንኳን ፡ ባገርና ፡ በርስቱ ፡ ላይ ፡ የሞተ ፡ ሰው ፡ የተመሰገነ ፡ ነው ፡ ተብሏል ።

መምህሩ ፤—ብፁዕ ፡ አባታችን ፡ ሳልዘነጋው ፡ ቀድም ፡ ስለ፡ ማሉበት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ መሞት ፡ እንደሚገባ፡ የተናገሩትን ፡ ምን ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ገብተዋል ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤ —እግዚአብሔር ፡ ያክብርዎ ፡ የዘነጉት ፡ መስ ሎኝ ፡ ነበር ። እንደዚህ ፡ ያለ ፡ መሠረታዊ ፡ ጥያቄ ፡ እወዳለሁ ፡ ክቡር ፡ ሆይ ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ ሕይወቴ ፡ ድረስ ፡ አንዱ ፡ ዋናው ፡ መታዘዝ ፡ የተቀደሰ ፡ መሥዋዕት ፡ ነው ፡ ብዬ ፡ የምተማ መንበት ፡ ይህ ፡ ነው ።

የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መንግሥት ፡ ጳጳስነት ፡ ባባቴ ፡ በቅዱስ ፡ ማርቆስ ፡ ወንበር ፡ ፊት ፡ በተቀመጥሁ ፡ ጊዜ ፡ ከቀዳማዊ ፡ ኀይለ ፡ ሥላሴና ፡ ከርሳቸው ፡ ዘር ፡ በቀር ፡ በኢትዮ

ጵያ ፡ ገዢነት ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ እንዳልቀበል ፡ ምያለሁ ፡ ተገዝቻለሁ ። ዘወትር ፡ አንበሳው ፡ ማርቆስ ፡ አትፍራ ፡ ሥጋን ፡ ከሚገድሉ ፤ ነፍስን ፡ ግን ፡ መግደል ፡ አይቻላቸውም ፡ እያለ ፡ ያጽናናኛል ፡ ስለዚህ ፡ ለገባሁት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ የተወደደ ፡ መሥዋዕት ፡ ለመሆን ፡ የቈረጥኩበትን ፡ ሐሳብ ፡ ማንም ፡ በትርጉም ፡ ሊያሳስተኝ ፡ አይችልም ።

መኰንኑ ፤— ብፁዕ ፡ አባታችን ፡ ምነው ፡ ያስቸግሩናል ፡ ባፍዎ ፡ ቢክቶርዮ ፡ ዔማኑኤል ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መሆናቸውን ፡ ይመኑ ፡ እግዚአብሔር ፡ የልብን ፡ ስለሚያውቅ ፡ ምንም ፡ አይፈርድብዎትም ፡ ለኛም ፡ ለርስዎም ፡ ይዘኑልን ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤— ወይ ፡ ግሩም ፡ እንደ ፡ ምን ፡ የሚያሳዝን ፡ አስተያየት ፡ ነው ፡ ጌታችን ፡ በውነት ፡ ስለናንተ ፡ ተናግሯል ። ማየት ፡ ታያላችሁ ፡ አታስተውሉም ። ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ ይህን ፡ ስትነግሩኝ ፡ አንድ ፡ ታሪክ ፡ ትዝ ፡ አለኝ ፤ ታሪክ ፡ ዘወትር ፡ አዲስ ፡ ነው ።

በዲዮቅልጥያኖስ ፡ ዘመን ፡ ክርስቲያኖች ፡ እየተፈለጉ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ሥቃይ ፡ ሲገደሉ ፡ አንዲት ፡ ነፍሰ ፡ ጡር ፡ የሆነች ፡ ክርስቲያን ፡ በክርስቲያን ፡ ሃይማኖት ፡ ስላመነችና ፡ ባደባባይም ፡ ስለ ፡ መሰከረች ፡ ወደሚባሉ ፡ ግሩማን ፡ አራዊት ፡ ጕድጓድ ፡ እንድትጣል ፡ ተፈረደባት ፤ አባቷም ፡ ልጄ ፡ እባክሽ ፡ ለኔ ፡ ለሽማግሌው ፡ አባትሽ ፡ እዘኚልኝ ፤ በማሕፀንሽ ፡ ላለው ፡ ሕፃንም ፡ ራሪለት ፡ እግዚአብሔርን ፡ በልብሽ ፡ እመኚው ፡ ነፍስሽን ፡ ለማዳን ፡ ባፍሽ ፡ ካጂው ፡ ብሎ ፡ እጫማዋ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ለመናት ።

ልጅቱም ፡ አባቴ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ተነሣና ፡ ልጠይቅህ ፡ ብላው ፡ ሲነሣ ፡ አንዲት ፡ የሸክላ ፡ ዕቃ ፡ አንሥታ ፡ ይህ ፡ ምንድነው ፡ ብላ ፡ ጠየቀችው ።

አባቷም ፡ ይህማ ፡ ሸክላ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ መለሰላት ። እሷም ፡ እንግዲያስ ፡ እግዚአብሔር ፡ እግዚአብሔር ፡ ሲሆን ፡ ሌላ ፡ ስም ፡ ልሰጠው ፡ አይገባኝም ፤ ልቤን ፡ የፈጠረ ፡ አፌንም ፡ የፈጠረ ፡ እሱ ፡ ነውና ። ስለዚህ ፡ ባፌም ፡ በልቤም ፡ እግዚአብሔርን ፡ አምኜ ፡ እሞታለሁ ፡ ብላ ፡ አባቷን ፡ ስማ ፡ ወደ ፡ አውሬዎቹ ፡ ጕድጓድ ፡ ተጣለች ፤ እዚያው ፡ ውስጥ ፡ ሕፃኑን ፡ ተገላግላ ፡ ሞተች ።

እኔም ፡ እንደዚሁ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ኃዘን ፡ እንዳረገዝሁ ፡ እሞ
ታለሁ ፡ በመቃብርም ፡ ውስጥ ፡ እገላገላለሁ ።

ምንም ፡ ቢሆን ፡ ቢክቶርዮ ፡ ዔማኑኤል ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡
ነገሥት ፡ ነው ብዬ ፡ አልፈርምም ፡ እባካችሁ ፡ ውጡልኝ ።

መኰንኑና ፡ መምህሩ ፡ እያዘኑ ፡ ይወጣሉ ።

በረኛ ፡ ይደውላል ፤ ግራዚያኒ ፡ ግባ ፡ ይላል ። ክቡር ፡ እምክቡ
ራን ፡ ከአቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ዘንድ ፡ የተላኩት ፡ መጥተዋል ።

ግራዚያኒ ፡ አስገባቸው ፡ ይላል ፤ መልክተኞች ፡ ይገባሉ ።

ግራዚያኒ ፡-እህ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ሆናችሁ ። መልክተኞቹ ፤-
ክቡር ፡ እምክቡራን ፡ ሆይ ፡ አቡነ፡ጴጥሮስን ፡ በብዙ፡ማስረጃ፡ጭምር፡
መክረናቸው ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ የሚመለሱ ፡ ሰው ፡ አይደሉም ።
በመሞታቸው ፡ ቈርጠዋል ፤ ጥንትም ፡ እንደምናውቃቸው ፡ አሳብ ፡
ጽኑ ፡ በሚሄዱበት ፡ መንገድ ፡ ዐለሙት ፡ ሥፍራ ፡ ለመድረስ ፡
የማንም ፡ አሳብ ፡ የማይመልሳቸው ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ አሁን ፡ ሃይማኖት ፡
ብለው ፡ የተደገፉት ፡ መሠረት ፡ ብርቱ ፡ ስለ ፡ መሰላቸው ፡ በግ
ልጥ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ቢክቶርዮ ፡ ዔማኑኤል ፡ የኢትዮጵያ ፡
ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መሆኑን ፡ አላምንም ፡ አልፈርምም ፡ ብለው ፡
አስታወቁን ፤ ምን ፡ ይደረግ ፡ ከክቡርነትዎ ፡ ምንም ፡ አልጐደ
ለም ፡ ታንቀው ፡ እንደ ፡ መሞት ፡ ያለ ፡ ነው ።

ግራዚያኒ ፡—ብዙ ፡ ካሰበ ፡ በኋላ ፡ ምን ፡ ቸገረኝ ፡ በራሳቸው ፡
ፈርደው ፡ መሞት ፡ ከፈለጉ ፡ ምን ፡ ይደረግ ፡ እንግዴህ ፡ ሂዱ ።

ግራዚያኒ ፡ ደወል ፡ ደወለ ፤ አሽከር ፡ ገባ ።

ግራዚያኒ ፡ መኳንንቱን ፡ ጥራ ፡ አለ ፤ መኳንንቱ ፡ መጡ ።

ግራዚያኒ ፤- አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ በወገናቸውም ፡ ባስመከራቸው ፡
እንቢ ፡ አሉ ፤ ከእንግዴህ ፡ ወዲያ ፡ ብንተዋቸውም ፡ የመንግሥታ
ችን ፡ ክብር ፡ ይነካል ።

ቅድም ፡ እንዳመለከተው ፡ የኢትዮጵያን ፡ ሕዝብ ፡ መግዛት ፡
በጥል ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ በመለማመጥ ፡ የማይሆን ፡ መሆኑን ፡
ተረዳነው ፤ ምንም ፡ የፋሺስት ፡ መሠረታዊ ፡ አሳብ ፡ ሕዝቡን ፡
ጥቂት ፡ በጥቂት ፡ ማጥፋት ፡ ቢሆን ፡ እንኳ ፡ ዛሬ ፡ በኒህ ፡
መነኵሴ ፡ እንዲጀመር ፡ አልፈቅድም ፡ ነበር ፤ እንግዴህ ፡ ምን ፡
ይደረግ ፡ እንዲደበደቡ ፡ ግድ ፡ ሆነብን ።

አሁንም ፡ ነገ ፡ ለሕዝቡ ፡ መቀጣጫ ፡ እንዲሆኑ ፡ በሕዝቡ ፡ ፊት ፡ አራዳ ፡ እንዲደበደቡ ፡ ቈረጥሁ ።

ጄኔራል ፡ ጋሊኒ ፡ ምን ፡ ይደረግ ፡ እኔም ፡ እስማማለሁ ፡ እኔ ፡ ፊቱኑ ፡ ተናግሬያለሁ ።

ግራዚያኒ ፡ ደወል ፡ ደወለ ፡ አሽከር ፡ ገባ ።

ግራዚያኒ ፡ ካንቲባውን ፡ ጥራ ፡ አለ ፡ አሽከር ፡ ከንቲባውን ፡ ጠራ ።

ግራዚያኒ ፤–ነገ ፡ በምስት ፡ ሰዓት ፡ ለሕዝቡ ፡ አራዳ ፡ እንዲሰበሰብ ፡ ይነገርና ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ በጊዮርጊስ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አጠገብ ፡ እንዲደበደቡ ።

ከንቲባው ፤- በፍጹም ፡ ታዛዥዎ ፡ ነኝ ።

ልፍ ፤ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ በገናናው ፡ የኢጣልያ ፡ መንግሥት ፤ ላይ ፡ ስለ ፡ ሸፈቱ ፡ ይደበደባሉና ፡ ነገ ፡ በምስት ፡ ሰዓት ፡ አራዳ ፡ በቅዱስ ፡ ጊዮርጊስ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አጠገብ ፡ እንድትሰበሰቡ ።

ም ዕ ራ ፍ ፡ ፪ ።

ያቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ጸሎት ፡ ሌሊት ፡ በወህኒ ፡ ቤት ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ መብራት ፡ ያበራሉ ።

በስመ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ አሐዱ ፡ አም ላክ ፡ አሜን ። አቤቱ ፡ ያች ፡ የምታስደነግጥ ፡ የሞት ፡ ጽላ ፡ በላዬ ፡ ላይ ፡ ልትወድቅ ፡ ነው ፤ ያችም ፡ የምትመር ፡ የሞት ፡ ጽዋ ፡ ቀረበች ። ነገር ፡ ግን ፡ አንተ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ከሆንክ ፡ አል ፈራም ፡ የሞትም ፡ ጽላ ፡ አያስደነግጠኝም ፡ የሞትንም ፡ መራራ ፡ ጽዋ ፡ ስላንተ ፡ ፍቅርና ፡ ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ጥፋት ፡ እጠጣታለሁ ።

አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ችላ ፡ ትለናለኽ ፡ በኛ ፡ በክፉዎችስ ፡ ምክንያት ፡ እን ዴት ፡ የወዳጅኽ ፡ የዳዊት ፡ ዙፋን ፡ በጠላት ፡ ጫማ ፡ ይረገጥ ።

በዓለም ፡ ላይ ፡ የታወቀች ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰንደቅ ፡ ዓላማስ ፡ ከቤተ ፡ መንግሥታችን ፡ ላይ ፡ ተነቅላ ፡ እንዴት ፡ ትውደቅ ።

የባዕድ ፡ ቀንበር ፡ ተሸክማ ፡ የማታውቅ ፡ ኢትዮጵያ ፡ በፋሺ ስት ፡ መዝገብ ፡ በባርነት ፡ እንዴት ፡ ትጻፍ ።

አቤቱ ፡ መድኀኒታችን ፡ በባሪያኽ ፡ በያዕቆብ ፡ አድረኽ ፡ ያንበሳ ፡ ግልግል ፡ ይሁዳ ፡ ተንበርክከኽ ፡ ተኛ ፡ ማንስ ፡ ይች

ላል ፡ ያስነሣኽ ፡ ዘንድ ፡ በትር ፡ ከይሁዳ ፡ አይጠፋም ፤ የገዢ ዘንግም ፡ ከእግሮቹ ፡ መካከል ፡ የሰላም ፡ ንጉሥ ፡ እስኪመጣ ፡ ድረስ ፡ የሚል ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ሰጥተኸው ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ አሸናፊው ፡ የኢትዮጵያ ፡ አንበሳ ፡ አንተ ፡ ስለ ፡ ተለየኸው ፡ ተመቶ ፡ ወደቀ ፡ የገዢነቱም ፡ በትር ፡ ከእጁ ፡ ወድቃ ፡ ተሰበረች ። ስለዚህ ፡ እረኛችን ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ በሐሳብና ፡ በኀዘን ፡ እንደ ፡ ምናሴ ፡ በብረት ፡ ቀፎ ፡ ውስጥ ፡ ተይዞ ፡ ወዳንተ ፡ ይጮኻል ።

አቤቱ ፡ በቸርነትኽ ፡ ይቅር ፡ ብለኸው ፡ ወደ ፡ ዙፋኑ ፡ እንዲመለስና ፡ የኢትዮጵያም ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ከሥልጣኑ ፡ በታች ፡ እንዲሰበሰብ ፡ አድርግ ።

እኔም ፡ የተናቅሁ ፡ ባርያኽ ፡ ያንተን ፡ የመከራ ፡ ጽዋ ፡ ተካፋይ ፡ ለመሆን ፡ ስለ ፡ ተዘጋጀሁ ፡ በጣም ፡ አመሰግንኻለሁ ።

አቤቱ ፡ የባሪያኽን ፡ የእስጢፋኖስን ፡ የሃይማኖት ፡ ብርታት ፡ አሳድርብኝ ፤ ምግባሬም ፡ እንድትበረታ ፡ አንተ ፡ ባባትኽ ፡ ቀኝ ፡ ተቀምጠኽ ፡ ልይኽ ፤ በመሬቱ ፡ ላይ ፡ የምትፈሰው ፡ የኔ ፡ የኀጢአተኛው ፡ ደም ፡ በፊትኽ ፤ የተቀደሰች ፡ መሥዋዕት ፡ ሆና ፡ እንደ ፡ አቤል ፡ ደም ፡ ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ትካሰስ ። አቤቱ ፡ መምህሬ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ጌታዬ ፡ ዦሮኽን ፡ አዘንብለኽ ፡ ስማት ፡ አሜን ።

እንግዴህ ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ የሕይወቱ ፡ ብርሃን ፡ ጠፋች ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የሚመጣው ፡ ዓለም ፡ የሕይወቱ ፡ ብርሃን ፡ የበለጠ ፡ እንዲያበራ ፡ አምናለሁ ። አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ተመልሰው ፡ ተኙ ።

የወህኒ ፡ ቤቱ ፡ ብርሃን ፡ አበራ ።

መልአክ ፡ ጽዋ ፡ ይዞ ፤ ቦ ፡ እለ ፡ በእሳት ፡ ወቦ ፡ እለ ፡ በመጥባሕት ፡ ሃሌ ፡ ሃሌ ፡ ሉያ ፡ ዐስበ ፡ ጻማሆሙ ፡ ነሥኡ ፡ ሰማዕት ፡ እያለ ፡ በሚያሳዝን ፡ ዜማ ፡ ይመጣል ።

መልአክ ፤—ጴጥሮስ ፡ ጴጥሮስ ፡ ጴጥሮስ ፡ አይዞኽ ፡ አትፍራ ፡ ሥጋኽን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ነፍስኽን መግደል ፡ አይችሉም ።

አስቀድሞ ፡ ገና ፡ በልጅነትኽ ፡ ለመናኒው ፡ ላባ ፡ ተድላ ፡ ረድ ፡ ሆነኽ ፡ ስታገለግል ፡ ለዚህ ፡ ከፍ ፡ ላለው ፡ ጸጋ ፡ ተመርጠኻል ፡

ደምኽም ፡ ለኢትዮጵያ ፡ ነፃነት ፡ በጸጋው ፡ ዙፋን ፡ ፊት ፡ ቀርበ ፡ አስታዋሽ ፡ ትሆናለች ፣ አንተም ፡ ብቻ ፡ ሳትሆን ፡ ባደግኽበት ፡ ገዳም ፡ በደብረ ፡ ሊባኖስ ፡ ብዙዎች ፡ ወንድሞችኽ ፡ በሰማዕትነት ፡ ይሞታሉ ፣ ደማቸውም ፡ ካንተ ፡ ደም ፡ ጋራ ።

አቤቱ ፡ ስለ ፡ ኢትዮጵያና ፡ ስለኛ ፡ ደም ፡ መቺ ፡ ትበቀልልናለኽ ፡ እያሉ ፡ ሊጮኹ ፡ ነው ። አይዞኽ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ነፃነት ፡ ይመለሳል ፣ ንጉሠ ፡ ነገሥቱም ፡ በዙፋኑ ፡ ላይ ፡ ሊያበራ ፡ ነው ።

እብሪተኛው ፡ ሙሶሊኒም ፡ በሰፈረው ፡ ቊና ፡ ሊሰፈር ፡ ነው ። በሳቮያ ፡ ቤተ ፡ መንግሥትም ፡ ላይ ፡ ተመዘንኽ ፡ ቀለልኽ ፡ መንግሥትኽ ፡ ለባዕድ ፡ ተሰጠች ፡ ተብሎ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ ተጻፈበት ። የንጽሕት ፡ ኢትዮጵያ ፡ ደም ፡ የዓለሙን ፡ ደም ፡ ሊያፋስስ ፡ ነው ፣ እንሆ ፡ ጽዋኽን ፡ ልትጠጣው ፡ ጥቂት ፡ ቀረኽ ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ —ብንን ፡ ብለው ፡ በስመ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ፫ ፡ ደቂቃ ፡ አገጫቸውን ፡ በጕልበታቸው ፡ ላይ ፡ አድርገው ፡ ትኵር ፡ ብለው ፡ የሚያዩ ፡ መስለው ፡ በኀዘን ፡ ይታያሉ ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፦ ወይ ፡ ግሩም ፡ ቦ ፡ እለ ፡ በእሳት ፡ ወቦ ፡ እለ ፡ በመጥባሕት ፡ ሃሌ ፡ ሃሌ ፡ ሉያ ፡ ዐስበ ፡ ጻማሆሙ ፡ ነሥኡ ፡ ሰማዕት ፡ ይላል ። እንግዴህ ፣ በማንኛው ፡ ዐይነት ፡ ይሆን ፡ የኔ ፡ ጽዋ ፡ ዕድሌ ፡ በድንጋይ ፡ መወገር ፡ ነውን ፡ ወይስ ፡ በጕራዴ ፣ ፈጣሪዬ ፡ በማንኛውም ፡ ቢሆን ፡ አልፈራም ፡ አንተ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ነኽና ።

አንድ ፡ ዘበኛ ፡ ምንድነው ፡ የማየው ፡ ብርሃን ፡ እኚህ ፡ ሰው ፡ ባትሪ ፡ ይዘው ፡ ገብተው ፡ ይሆን ፣ አንደኛው ፡ ዘበኛ ፣ እስቲ ፡ ገብተን ፡ እንፈትሻቸው ፣ አባቴ ፡ ባትሪ ፡ በኪስዎ ፡ ይዘዋልን ፡ ወህኒ ፡ ቤቱን ፡ ብርሃን ፡ መላው ። አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፦ ልጆቼ ፡ ሆይ ፡ ምንም ፡ መብራት ፡ በኪሴ ፡ አልያዝኩም ፣ በኪሴ ፡ የያዝኩት ፡ ወንጌል ፡ ብቻ ፡ ነው ። እኔም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ወንጀለኛ ፡ ነኝ ፣ ይህን ፡ ትርጕም ፡ ታውቃላችሁን ።

ዘበኛው ፦ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ እኔ ፡ አላውቅም ። ወንጀለኛ ፡ ነኝ ፡ የሚሉት ፡ ከወንጀልም ፡ ወንጀል ፡ ለገናናው ፡ ሙሶሊኒ ፡ አልገዛም ፡ ብለው ፡ አይደለምን ፡ ይህ ፡ የደረሰብዎ ፣ ለዚህ ፡ ምን ፡ ትርጕም ፡ ያስፈልጋል ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤ ጊዜ ፡ ጽድቅን ፡ እንደ ፡ ኀጢአት ፡ ስለሚ
ቈጥረው ፡ ወንጀለኛ ፡ የተባለበትን ፡ ላስረዳችሁ ፡ ይገባኛል ። ዮዲት
(ጕዲት ፡ ) የምትባል ፡ የይሁዲ ፡ ንግሥት ፡ ተንሥታ ፡ ክርስቲያኖ
ችን ፡ በፊጀች ፡ ጊዜ ፤ ወንጌል ፡ በእጁ ፡ የተገኘ ፡ ሁሉ ፡ እየተ
ፈለገ ፡ እንዲገደል ፡ ዐዋጅ ፡ ስለ ፡ ተነገረ ፡ ወንጌል ፡ የተገኘበት ፡
ሁሉ ወንጀለኛ ፡ ነው ፡ እየተባለ ፡ ይደበደብ ፡ ነበር ፤ ስለዚህ ፡
በዚህ ስም ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ ድረስ ፡ አጥፊ ፡ ሁሉ ፡ ወንጀለኛ ፡
እየተባለ ፡ ይነገራል ። አሁንም ፡ እኔ ፡ ወንጀለኛ ፡ ነኝ ፡ እንጂ ፡ መብ
ራት ፡ አልያዝኩም ።

ዘበኛ ፤—እባክዎን ፡ አባቴ ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ቀልድ ፡
ይተውትና ፡ ይበርብሩ ።

ከተበረበሩ ፡ በኋላ ፡ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ እባካችሁ ፡ ልጆቼ ፡ አንድ ፡
ነገር ፡ ልጠይቃችሁ ፡ ስለ ፡ ምንድነው ፡ ለጠላታችሁ ፡ የታመነ ፡
አገልጋይና መሣሪያ ፡ የሆናችሁት ። ወይስ ፡ አልሰማችሁምን ፡
እናታችሁን ፡ ኢትዮጵያን ፡ እንደ ፡ ገደለ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ለናቱ ፡
ገዳይ ፡ ሰው ፡ አገልጋይ ፡ ይሆናል ፡

አንዱ ፡ ዘበኛ ፡ ጕድ ፡ ፈላልኝ ፡ እኚህ ፡ ሰውዬ ፡ ገና ፡ ይዘ
ባርቃሉ ። ይስሙ ፡ አባቴ ፡ እናታችን ፡ ኢትዮጵያ ፡ ዛሬ ፡ ገና ፡
ነው ፡ ባል ፡ ያገባችው ፡ እያበበች ፡ እያማረባት ፡ ስትሄድ ፡ ማነው ፡
የገደላት ፡ ይልቅስ ፡ ለገናናው ፡ ሙሶሊኒ ፡ ዕድሜ ፡ ይስጠውና ፡ የኛን ፡
ንጉሥና ፡ ባላባት ፡ መሳፍንት ከባድ ፡ ሸክም ፡ ሆነው ፡ ያስጨን
ቁን ፡ የነበሩትን ፡ ከትከሻችን ፡ አውርዶ ፡ ጣለልን ፡ እንደ ፡ ምን ፡
የናታችን ፡ ገዳይ ፡ ይሉታል ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤-አዬ ፡ ጕድ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያሳዝናል ፡ ክሦ
ስት ፡ ሺሕ ፡ ዘመን ፡ የሚበልጥ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ነፃነት ፡ የተጠበቀበትን ፡
የኢትዮጵያን ፡ ኰራትና ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥትን ፡ ክብር ፡ የመሳፍ
ንትንና ፡ የባላባትን ፡ ውለታ ፡ በገንዘብና ፡ በፍራት ፡ ምክንያት ፡
ወርውራችሁ ፡ ጣላችሁት ።

አንዱ ፡ ወታደር ፡ እስቲ ፡ ርስዎ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መሳፍንት ፡
ባላባት ፡ ለኢትዮጵያና ፡ ለሕዝቡ ፡ የሠሩትን ፡ ይንገሩን ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤—እኛ ፡ ልጆቼ ፡ ስሙኝ ፡ እነግራችኋለሁ ። የቀድሞ ፡ ነገሥታትና ፡ መሳፍንት ፡ ባላባት ፡ የኢትዮጵያን ፡ ነፃነት ፡ በደማቸው ፡ የመሠረቱ ፡ ሰውን ፡ ከገንዘብ ፡ በላይ ፡ ገምተው ፡ ገንዘብ ፡ ለነሱ ምናቸውም ፡ አልነበር ፤ ገንዘባቸው ፡ ሰው ፡ ነበር ። ስለዚህ ፡ ርስታቸው ፡ የግል ፡ ገንዘባቸው ፡ ሳይቀር ፡ ለናንተ ፡ አባቶች ፡ ሲሳይ ፡ ነበር ፤ የነዚህ ፡ ጌቶች ፡ ገንዘብ ፡ የሕዝብ ፡ ገንዘብ ፡ በመሆኑ ፡ አንድ ፡ ወታደር ፡ ወይም ፡ አሽከር ፡ የጌታውን ፡ ቤት ፡ ቤታችን ፡ ይለው ፡ ነበር ።

ጌታውም ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ ኢትዮጵያን ፡ ላገለገለ ፡ ጭፍራውና ፤ አሽከሩ ፡ እንደ ፡ ልጁ ርስቱን ፡ ገንዘቡን ፡ ይናዘዝለት ፡ ነበር ። የነዚህ ፡ ጌቶች ፡ ደስታና ፡ ሀብት ፡ ያሽከሮቻቸው ፡ መደርጀትና ፡ ፈረሶቻቸው ፡ እየተቀለቡ ፡ መጠንከር ፡ ብቻ ፡ ነበር ። በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ የገዢና ፡ የሕዝብ ፡ አንድነት ፡ የኢትዮጵያ ፡ ነፃነት ፡ ተጠብቆ ፡ ቈየች ። ልጆቼ ፡ ሆይ ፡ ስንቱን ፡ ልንገራችሁ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ገዢዎች ፡ ለሕዝባቸው ፡ ያደረጉለትን ፡ ውለታ ፡ በጠቅላላው ፡ የነሱ ፡ ቤት ፡ የድኾች ፡ ማስተዳደሪያ ፡ ጽሕፈት ፡ ቤት ፡ ነበር ፡ እንጂ ፤ የግል ፡ ቤታቸው ፡ አልነበረም ።

ዘበኞች ፡ ከሳቸው ፡ እልፍ ፡ ብለው ፡ ይነጋገራሉ ፤ አንዱ ፡ ዘበኛ ፡ ወንድሜ ፡ እኚህ ፡ ሰው ፡ የሚናገሩት ፡ ነገር ፡ እኮ ፡ እውነት ፡ ነው ፤ የኔ ፡ አባት ፡ የራስ ፡ መኰንን ፡ አሽከር ፡ ነበር ። ስላገልግሎቱ ፡ ቋና ፡ ርስታቸውን ፡ ሰጥተውት ፡ እስከ ፡ አሁን ፡ ቤተ ፡ ዘመዶቻችንን ፡ የያዘልን ፡ እሱ ፡ ነው ። በራስ ፡ መኰንን ፡ ቤት ፡ ያባቴ ፡ ሥራ ፡ በኢትዮጵያ ፡ ላሉ ፡ ድኾች ፡ ምጽዋት ፡ ለሚያካፍሉ ፡ ሰዎች ፡ አለቅነት ፡ ነበር ። ካመት ፡ ዓመት ፡ ገንዘብ ፡ እያስጫኑ ፡ በየገዳሙ ፡ ለወደቁ ፡ በሽተኞችና ፡ የዓለም ፡ ምሬት ፡ ስለ ፡ ተሰማቸው ፡ ንብረታቸውን ፡ ጥለው ፡ መንነው ፡ በበረሓ ፡ ለሚኖሩ ፡ መናንያን ፡ ማካፈል ፡ ነበር ፤ ይህ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ አስተያየት ፡ ዛሬ ፡ እኮ ፡ የለም ።

ሁለተኛው ፡ ወታደር ፡ ኧረ ፡ ታልክስ ፡ የኔም ፡ አባት ፡ የራስ ፡ ተሰማ ፡ አሽከር ፡ ነበር ። ራስ ፡ ተሰማ ፡ ሲሞቱ ፡ ላባቴ ፡ በኑዛዜ ፡ እንደ ፡ ልጆቻቸው ፡ ትልቅ ፡ ርስት ፡ ስለ ፡ ሰጡት ፡ አሁንም ፡ ይዘን ፡ ያለ ፡ እሱ ፡ ነው ።

የራስ ፡ ተሰማ ፡ ኑዛዜ ፡ ሲፈስ ፡ እዚያው ፡ ነበርኩና ፡ ምንም ፡ ልጅ ፡ ብሆን ፡ ትዝ ፡ ይለኛል ። ርስታቸውን ፡ ሁሉ ፡ ለልጆቻቸው ፡ ለዘመዶቻቸው ፡ ላሽከሮቻቸው ፡ ከካፈሉ ፡ በኋላ ፡ ገንዘቤ ፡ ግን ፡ በናቴ ፡ እጅ ለድኾች ፡ ይሰጥልኝ ፡ አሉ ። አየ'ኸ ፡ ወንድሜ ፡ ከድኾች ፡ ያገኘሁትን ፡ ገንዘብ ፡ ለድኾች ፡ መመለስ ፡ ይገባኛል ፡ በማለት ፡ የተረፈውን ፡ ለድኾች ፡ ወንድሞቻቸው ፡ ማካፈል ፡ እን ዴት ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ አስተያየት ፡ ነው ።

ሦስተኛው ፡ ዘበኛ ፡ እኔ ፡ ምንም ፡ አገሬ ፡ ሐማሴን ፡ ቢሆን ፡ እዚህ ፡ ከመጣሁ ፡ ያየሁት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ በጣም ፡ ይገርመኛል ። በበቾ ፡ ወጊዶ ፡ በኩል ፡ ሽፍታ ፡ ስናሳድድ ፡ ትልቅ ፡ ዥረት ፡ ተሻግረን ፡ ወደያያና ፡ ጉለሌ ፡ ስናቃና ፡ አንድ ፡ የሰማይ ፡ ስባሪ ፡ የሚያኽል ፡ ውሃው ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ የሚፈስ ፡ መሬት ፡ አየሁ ፤ አንድ ፡ ሽማግሌ ፡ ባላገር ፡ ጠርቼ ፡ ይህ ፡ የማነው ፡ መሬት ፡ ብዬ ፡ ጠየቅኋቸው ። ሽማግሌውም ፡ የራስ ፡ ዳርጌ ፡ አሽከር ፡ መሬት ፡ ነው ፡ ብለው ፡ መለሱልኝ ፤ ማነው ፡ የሰጠው ፡ ብዬ ፡ ብጠይቃቸው ጊታው ፡ ስላገለገላቸው ፡ ርስት ፡ አድርገው ፡ ሰጡት ፡ አሉኝ ። እኔም ፡ ገርሞኝ ፡ ዕብድ ፡ ናቸው ፤ ለልጆቻቸው ፡ ምን ፡ ሊሰጡ ፡ ነው ፡ ላሽከሮቻቸው ፡ ይህን ፡ የሰጡት ፡ ብዬ ፡ ብጠይቃ ቸው ፡ ሽማግሌውም ፡ በትካዜ ፡ ቃል ፡ የዱሮዎቹ ፡ መሳፍንትና ፡ ባላባቶች ፡ ልጆቻቸው ፡ ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ነፃነት ፡ የሚከላከሉ ፡ አሽከሮቻቸው ፡ ነበሩ ፤ ለልጆቻቸው ፡ ግን ፡ አባታቸው ፡ ንጉሡ ፡ ነገሥቱ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ አሉኝ ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤ - እኔ ፡ ሞት ፡ እበራፊ ፡ ስለ ፡ ቆመ ፡ ሰዓቴ ፡ ጥቂት ፡ ነችና ፡ ምነው ፡ ልጆቼ ፡ ርቃችሁ ፡ ቆማችሁ ፡ የምትጠ ይቁኝ ፡ ለምንድነው ።

የሐማሴን ፡ ዘበኛ ፡ ብፁዕ ፡ አባታችን ፡ ሆይ ፡ እስቲ ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ልጠይቅዎ ፡ የርስዎ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትና ፡ መሳፍንት ፡ ባላ ባት ፡ ብቻቸውን ፡ በወርቅና ፡ በልሻን ፡ እያጌጡ ፡ አንድ ፡ ወታደር ፡ ይቅርና ፡ የሻምበል ፡ እንኳ ፡ ቢሆን ፡ ልሻን ፡ የለውም ።

ደጉ ፡ የፋሺስት ፡ መንግሥት ፡ ግን ፡ ለኔ ፡ ላንድ ፡ ወታደር ፡ ስንኳ ፤ የሸለመኝ ፡ ልሻን ፡ እነሆ ፡ በደረቴ ፡ ላይ ፡ ያበራል ፤ የርስዎ ፡ መንግሥት ፡ ቢሆን ፡ እንደዚህ ፡ ያደርጋልን ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤ -ባልሳሳት ፥ ባነጋገርኽ ፡ የሐማሴን ፡ ተወላጅ ፡ መሆንኽን ፡ ዐወቅሁት ፤ ልጄ ፡ ታውቃለኽን ፡ ካንተ ፡ አገር፥ እንዴት ፡ ያሉ ፡ አርበኞች ፡ እንደ ወጡ ። የነፃነት ፡ ማጣት ፡ ምሬት ፡ ስለ ተሰማቸው ፡ ቤታቸውን ፡ ንብረታቸውን ፡ ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ነፃነት ፡ ሲሉ ፡ ጥለው ፡ በበረሓ ፡ ወድቀው ፡ እንደ ፡ ቀሩ ፤ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ላንተ ፡ ምሳሌ ፡ የሚሆን ፡ ያገርኽ ፡ ተወላጅ ፡ በወንድሟ ፡ ላይ የሠራችውን ፡ አሳስብኻለሁ ፤ አንዲት ፡ ያማሴን ፡ ሴት ፡ የተወለደችበትን ፡ ቀን ፡ በዓል አድርጋ ፡ ከዘመድ ፡ ከወዳጅ ፡ ጋራ ፡ ስትበላ ፡ ስትጠጣ ፡ ታላቅ ፡ ወንድሟ ፡ ልሻኑን ፡ በደረቱ ፡ መልቶ ፡ መጣና ፡ እኅቴ ፡ እንኳን ፡ እዚህ ፡ ዘመን ፡ አደረሰሽ ፡ ብሎ ፡ ሳማት ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ያች ፡ ያገር ፡ ፍቅር ፡ የመላባት ፡ ሴት ፡ በደረቱ ፡ የተደረደረውን ፡ ልሻን ፡ አይታ ፡ ደሟ ፡ ፈልቶ ፡ አትሳመኝ ፡ አንተ ፡ ከሐዲ ፡ የወንድሞችኽን ፡ ደም ፡ በደረትኽ ፡ ተለቅልቀኽ ፡ ብላ ፡ ገፍታ ፡ ጣለችው ።

ወንድሟም ፡ ከዚያ ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ወጣና ፡ ከኅሊናው ፡ ጋራ ፡ ቢጫወት ፤ በውነትም ፡ የወንድሞቼን ፡ ደም ፡ ኖሯል ፡ በደረቱ ፡ የተሸከመው ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ወንድሟ ፡ ከኅቴ፥ አፍ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ፍርድ ፡ የተቀበልኩ ፡ ከእግዚአብሔር ፊት ፡ ምን ፡ ፍርድ ፡ ልቀበል ፡ ይሆን ፤ እኔ ፡ እንግዴህ ፡ የወንድሞቼ ፡ ገዳይ ፡ ሆኜ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ መኖር ፡ አይገባኝም ፡ ብሎ ፡ ሽጒጡን ፡ ጠጥቶ ፡ ራሱን ፡ ገደለ ።

እኅቱም ፡ የሽጒጥ ፡ ድምጥ ፡ ሰማችና ፡ ደንግጣ ፡ ብትወጣ ፥ ወንድሟ ፡ ወድቆ ፡ ደሙ ፡ በልሻኑ ፡ ላይ፡ ፈሶ ፡ አየችውና ፡ የውነት ፍርድ ፡ በራስኽ ፡ ላይ ፡ ፈረድኽ ፡ ብላ ፡ አስነሥታ ፡ አስቀበረችው ፡ ይባላል ። ስለዚህ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ፍርድ ፡ እንዳይደርስብኽ ፡ ይልቁንስ ፡ የወንድሞችኽን ፡ ደም ፡ ከደረትኽ ፡ ላይ ፡ እጠበው ።

## ም ዕ ራ ፍ ፲ ።

### ጥሩምባ ፡ ተነፋ ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤ -ልጆቼ ፡ እንግዴህ ፡ ደኅና ፡ ሰንብቱ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ነፃነቷ ፡ አይጠፋም ፤ እናንተ ፡ ግን ፡ አደራችሁን ፡ መልካም፥ ፍሬ ፡ በመሆን ፡ ፈንታ ፡ እሾኽና ፡ አሜከላ ፡ ሆናችሁ ፡ እንዳትቈዩ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ነጻነት ፡ አስቡ ፥

የዘበኛው ፡ አለቃ ፡ ወደ ፡ ወህኒ ፡ ቤቱ ፡ ይገባል ።

የዘበኛው ፡ አለቃ ፡ ይነሡ ፡ ወደሚደበደቡበት ፡ ሊሄዱ ፡ ነው ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤— በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፤ እኔም ፡ የምጠብቀው ፡ ይኸንኑ ፡ ነበር ። በየመንደሩ ፡ ይለፈፋል ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ በገናናው ፡ የጣልያን ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ሸፈቱ ፡ አራዳ ፡ ይደበደባሉና ፡ ባ፰ ፡ ሰዓት ፡ እንድትሰበሰቡ ፡ ባ፰ ፡ ሰዓት ፡ አራዳ ፡ ወደ ፡ መደብደቢያው ፡ ቦታ ፡ ደረሱ ። ሕዝቡም ፡ ተሰብስቦ ፡ ነበር ፤ ዘበኞቹ ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ተሰልፈዋል ።

የዘበኛ ፡ አለቃው ፡ ዐይናቸው ፡ ላይ ፡ ጥቍር ፡ ጨርቅ ፡ አሰረላቸው

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤ አይሆንም ፡ ስለ ፡ ሀገሬ ፡ ሞትን ፡ ለማየት ፡ ስለምፈቅድ ፡ ለሞት ፡ መደለያ ፡ ዐይኔ ፡ ላይ ፡ በጥቍር ፡ ጨርቅ ፡ እንድሸፈን ፡ አልፈልግም ፡ ብለው ፡ ጣሉት ።

የዘበኛው ፡ አለቃ ፡ እንግዴህ ፡ የመጨረሻ ፡ ቃል ፡ ለመናገር ፡ ይፈቀዱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይናገሩ ።



አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ በፋሽስት ፡ እጅ ፡ እንደ ፡ ተገደሉ ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፡ የኔም ፡ ልጆች ፡ ደኅና ፡ ሰንብቱ ፡ ባለችኝ ፡ በመጨረሻ ፡ ደቂቃ ፡ ውስጥ ፡ የም

ነግራችሁ ፡ ቃል ፡ አደራ ፡ ለጠላታችሁ ፡ ለፋሽስት ፡ መንግሥት፡ እንዳትገዙ ፡ ስንኳን ፡ እናንተ ፡ መሬቷ ፡ እንዳትገዛ ፡ ገዝቻለሁ ።

የዘበኛው ፡ አለቃ ፡ አነጣጥሮ ፡ ተኰሰ ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ልክ ፡ እንደ ፡ መስቀል ፡ ሆነው ፡ በልበ ቻው ፡ ወደቁ ። የዘበኛ ፡ አለቃ ፡ በገሮሯቸው ፡ ላይ ፡ በሽጉጥ ፡ ተኰሰ ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፤— ዐሥር ፡ ደቂቃ ፡ ያኽል ፡ እንደ ፡ ተዘረጉ ፡ ካህናተ ፡ ሰማይ ፡ ወምጋሆሙኒ ፡ ለጻድቃኒከ ፡ ለአራዊተ ፡ ገዳም፡ ወከዐው ፡ ደሞሙ ፡ ከመ ፡ ማይ ፡ ዐውዳ ፡ ለኢትዮጵያ ፡ ወኀ ጥኡ ፡ ዘይቀብሮሙ ። ወዲያው ፡ መልአክ ፡ የተጠቀለለ ፡ ሰሌዳ ፡ ይዞ ፡ ይመጣል ። ነፍስ ፡ በአቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ራስጌ ፡ ተቀምጣ ፡ ትታያለች ። መልአክ ፡ ካቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ግርጌ ፡ ቆሞ ፡ ሰሌዳ ውን ፡ ያነብና ፡ ይሰጣል ፤ ወዲያው ፡ ዘውድ ፡ ይጭንላታል ።

የመልአክ ፡ ንባብ ።

ቅድስት ፡ ነፍስ ፡ ሆይ ፤ እንሆ ፡ ከነገሥታት ንጉሥ ፡ ከጌቶች ፡ ጌታ ፡ የተላከልሽ ፡ ሰሌዳ ፡ ይኸውም ፡ ሰሌዳ የቅዱስ ፡ ኑሮሽን ፡ ታሪክ ፡ የሚዘረዝር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ልትሰሚው ፡ ይገባሻል ።
ወደ ፡ ጽዮን ፡ ተራራ ፡ ካዲሲቱ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ትሄጃለሽ ። ከዚያም ፡ የማይቆጠሩ ፡ አእላፍ ፡ መላእክትና ፡ የፍጹማን ፡ ፅማ ዕታት ፡ ነፍሳት ፡ ይጠብቁሻል ፤ ወደ ፡ እግዚአብሔርም ፤ ገነት ፡ ትሄጃለሽ ።

የማያልፍ ፡ ፍሬም ፡ ትፀያለሽ ፤ እንደ ፡ ደረስሽም ፡ ነጭ ፡ ልብስ፡ ታገኛለሽ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ለዘላለም ፡ ከንጉሡ ፡ ጋራ ፡ ትመላለ ሻለሽ ፤ ትጫወችማለሽ ። በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሳለሽ ፡ እንዳገኘሽ ፡ ያለ ፡ መከራና ፡ ትካዜ ፤ ሕማምና ፡ ኀዘን ፡ ሞት ፡ አይታይም ። ስለ ፡ ሠራሽው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ መጽናናትን ፡ ታገኛለሽ ፤ ደስታም፡ ስለ ፡ ኀዘንሽ ። ከዚያም ፡ የዘራሽውን ፡ ታጭጃለሽ ፡ ማለት ፡ የጸ ሎትሽንና ፡ የዕንባችሽን ፡ ፍሬ ፡ ትለቅሚያለሽ ። ከዚያም ፡ በኋላ ፡ የወርቅ ፡ ዘውድ ፡ ትጭኛለሽ ። ወደ ፡ አብርሃም ፡ ወደ ፡ ይስ ሐቅ ፡ ወደ ፡ ነቢያት ፡ ይወስዱሻል ። ሁል ፡ ጊዜ ፡ ቅዱሳን ፡ በማ

የት ፡ ደስ ፡ ይልሻል ። ከዚያም ፡ ደግሞ ፡ በብዕዕና ፡ ታጌጪለሽ ። በእሥራኤልም ፡ ሠረገላ ፡ ትቀመጪለሽ ። ከነገሥታት ፡ ንጉሥ ፡ ጋራ ፡ ለመዘር ፡ በደመና ፡ በመለከት ፡ በነፋስ ፡ ክንፍ ፡ ሲመጣ ፡ አንቺ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ትሄጃለሽ ። በፍርድ ፡ ዙፋኑም ፡ ሲቀመጥ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ትቀመጪለሽ ። በዐመፀኞች ፡ ሁሉ ፡ ላይ ፡ በመላእክትም ፡ ቢሆን ፡ ወይም ፡ በሰዎች ፡ ሲፈርድ ፡ እንዲሁም ፡ አንቺ ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ትፈርጃለሽ ፤ የርሱና ፡ ያንቺ ፡ ጸላቶች ፡ ናቸውና ። እንግዴህ ፡ ለቅሶ ፡ የለም ፤ ጩኸትም ፡ ሕማምም ። ሥቃይም ፡ ያገሩ ፡ ጌታ ፡ ዕንባሽን ፡ ካይንሽ ፡ ያብሳል ። ከዚያም ፡ ሱራፌል ፡ ኪሩቤል ፡ ባልንጀሮችሽ ፡ ይሆናሉ ። አሁን ፡ ብርሃናቸው ፡ ዐይንሽን ፡ የሚያንጸበርቀው ፡ በመከራሽና ፡ በሃይማኖትሽ ፡ ይልቁንም ፡ ለወዳጅሽ ፡ ስትይ ፡ የዚህን ፡ ዓለም ፡ ድሎት ፡ እንደ ፡ ጉድፍ ፡ ስለ ፡ ቈጠርሽው ፡ የብርሃን ፡ ልጅ ፡ ትባያለሽ ፤ ከደጁ ፡ ሰላሙም ፡ በደረስሽ ፡ ጊዜ ፡ ከበራፉ ፡ ላይ ፡ በወርቅ ፡ ቀለማት ፡ የተጻፉ ፡ እንደዚህ ፡ የሚሉ ፡ ቃላት ፡ ታያለሽ ።



ያቡን ፡ ጴጥሮስን ፡ ነፍስ ፡ መልአክ ፡ እንደ ፡ ተቀበላት ።

ብፁዓን ፡ ናቸው ፤ ትእዛዙን የሚጠብቁ ፡ ቅንነትን ፡ ያገኙ ፡

ዘንድ ፤ ወደ ፡ ሕይወት ፡ ዛፍ ፡ በደጅ ፡ ሰላሙ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ይገቡ ፡ ዘንድ ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ደጅ ፡ ስትመች ፡ በሩ ፡ ይከፈታል ።

ብዙ ፡ እልፍ ፡ አእላፍ ፡ መላእክት ፡ ሊቀበሉሽ ፡ ይመጣሉ ። ከነሱም ፡ ጋር ፡ ሙሴና ፡ ኤልያስ ፡ ሄኖክ ፡ ዕዝራና ፡ ዳዊት ፡ ሌሎችም ፡ አባቶች ፡ አሉ ።

ብፅዕት ፡ ነፍስ ፡ ሆይ ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ይህንን ፡ በደሙ ፡ የታተመውን ፡ ሰሌዳ ፡ ማኅተም ፡ ማሳየት ፡ ይገባሻል ። ምስክርሽ ፡ ነውና ። የቅዱስ፡ጴጥሮስ ፡ ነፍስ ፡ ሆይ ፡ አትዘኝ ፡ አትተክዥ ፤ ይልቁንስ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እመኚና ፡ ይኸንን ፡ መዋቲ ፡ ሥጋሽን ፡ ላራዊት ፡ መብል ፡ ጥለሽ ፡ ተነሺ ፡ ወደ ፡ ወዳጅሽ ፡ እንሂድ ፡ እሱም ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡ ይጠብቅሻል ። መልአክ ፡ ነፍስን ፡ ይዞ ፡ ይሄዳል ፤ የዘበኛው ፡ አለቃ ፡ ከዘበኞቹ ፡ ጋራ ፡ ይመጣል ።

ይኸንን ፡ ሬሳ ፡ በካሚዎን ፡ አድርገኽ ፡ በቀኝ ስቋም ፡ በኩል ፡ ወደ ፈፋ ፡ ውስጥ ፡ ጣለውና ፡ አውሬ ፡ ይብላው ፤ ደሙን ፡ ከመሬት ፡ ላይ ፡ ጥረገው ።

ዘበኛው ፤ ደሙን ፡ ከመሬት ፡ ላይ ፡ ጥረገው ፡ አለ ፤ ወይ ፡ ግሩም ፡ ደም ፡ ያለደም ፡ በሳሙና ፡ ቢያጥቡት ፡ አይሄድም ።

የደም ፡ ድምፅ ።

በቀለ ፡ ደሞሙ ፡ ለአግብርቲከ ፡ ዘተክዕወ ፡ ይባእ ፡ ቅድሜከ ፡ ገዓሮሙ ፡ ለሙቁሓን ፡ ወበከመ ፡ ዕበየ ፡ መዝራዕትከ ፡ ።

ዘበኛው ፡ ወይ ፡ ግሩም ፡ የደም ፡ ድምፅ ፡ እንዲህ ፡ ያሳዝናል ።

የሕዝብ ፡ ክርክር ፡ ባንድ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ።

ሸዬ ፡ አደፍርሰው ፤ ወንደሞቼ ፡ ዛሬ ፡ ባቡን ፡ ጴጥሮስ ፡ ላይ ፡ በተደረገው ፡ የግፍ ፡ አገዳደል ፡ እስከ ፡ ዐጥንቴ ፡ ተሰማኝ ። ይህ ፡ ታሪካዊ ፡ የሆነ ፡ የአርበኝነት ፡ አሻሻት ፡ ለኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ኩራት ፡ ነው ።

በመሬታችን ፡ ላይ ፡ የፈሰሰው ፡ የኒህ ፡ የቅዱስ ፡ ንጹሕ ፡ ደም ፡ የኢትዮጵያን፡ሕዝብ፡ሁሉ፡ባንድነት ፡ የሚያስተሳስር ፡ ሳይሆን ፡ አይቀርም ። እንግዲህ ፡ ያገሬ ፡ የሸዋ ፡ መሬት ፡ ለጠላት ፡ እሾኽ፡ መሆን ፡ ይገባታል ። እኔም ፡ ወዳገሬ ፡ ሂጄ ፡ በዱር ፡ በገደል ፡ ስላገሬ ፡ አውሬ ፡ መሆኔን ፡ መረጥሁ ፡ በተረገመችና ፡ በተገዘተች ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ከጠላት ፡ ጋራ ፡ መኖርን ፡ አልፈልግም ።

ትግሬ ፡ ካሣ ፤ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፤ አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ልጆቼ ፡ ደኅና ፡ ሰንብቱ ፡ ብለው ፡ በወደቁ ፡ ሰዓት ፡ የዘበኛ ፡ አለቃው ፡ በዡርጅቸው ፡ ላይ ፡ ሽጉጥ ፡ ሲተኵስባቸው ፡ ባየሁ ፡ ጊዜ ፡ በውነት ፡ ልንገራችሁ ፡ ያንዱን ፡ የጦር ፡ አለቃ ፡ ጕራዴ ፡ መዝገሮ ፡ ልፈጃቸውና ፡ እኔም ፡ እዚያው ፡ ለመሞት ፡ አስቤ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ለሌላ ፡ ቀን ፡ ብሎኝም ፡ እንደሆን ፡ አላውቅም ፡ ወዲያው ፡ በረድሁ ። አሁንም ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ የኒህ ፡ ሰው ፡ አሟሟት ፡ እስከ ፡ መቼም ፡ ከልቤ ፡ አይጠፋም ።

ጕዝሜ ፡ በለው ፤ እኔ ፡ በዘመኔ ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ዛሬ ፡ ያለ ፡ ከልብ ፡ የማይጠፋ ፡ ነገር ፡ ደርሶብኝም ፡ አያውቅ ፤ ይልቁንም ፡ ሞትን ፡ እንዳያዩ ፡ ዐይናቸውን ፡ ቢሸፍኗቸው ፡ ሞትን ፡ ማየት ፡ እፈልጋለሁ ፡ ብለው ፡ ከይናቸው ፡ ፈተው ፡ ሲጥሉት ፡ ባየሁ ፡ ጊዜ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ፍርሃት ፡ ካይናቸው ፡ ላይ ፡ ፈተው ፡ የጣሉት ፡ መሰለኝ ።

ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ የኒህን ፡ ሰው ፡ የመንፈስ ፡ ብርታት ፡ ያየ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ምን ፡ በዚህ ፡ ከተማ ፡ ይቀመጣል ። ስለዚህ ፡ እኔ ፡ ዛሬውኑ ፡ አገሬ ፡ ጕዝም ፡ ሄጄ ፡ ስለ ፡ ሀገሬ ፡ በዱር ፡ በገደል ፡ የኢትዮጵያ ፡ ነፃነት ፡ እስክትመለስ ፡ አውሬ ፡ ሆኜ ፡ እቀመጣለሁ ።

በጌምድሬ ፡ ተማቹ ፤ ሰማኸ ፡ ወንድሜ ፡ በለው ፡ ጻድቃን ፡ ሳይቃጠሩ ፡ ይገናኛሉ ፡ እንደተባለው ፡ ሳንማከር ፡ በሐሳብ ፡ ተገናኘን ፡ እኔም ፡ ስላገሬና ፡ ስለ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቴ ፡ ክብር ፡ ባርማጭሆ ፡ በረሓ ፡ አውሬ ፡ ሆኜ ፡ እቀመጣለሁ ።

ጋላ ፡ ዋቅጅራ ፤ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ ዛሬ ፡ ባየሁት ፡ ታሪካዊ ፡ ነገር ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ ሲገርመኝ ፡ ዋልኩ ፡ ይልቁንም ፡ የሸዋን ፡ መንግሥት ፡ በክርስቲያን ፡ ሃይማኖትና ፡ ምግባር ፡ ተክሎ ፡ ኰትኵቶ ፡ ያሳደገኝን ፡ አመሰገንሁ ። አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ በመጨረሻ ፡ ሰዓታቸው ፡ ልጆቼ ፡ ስንኳን ፡ እናንተ ፡ መሬቷ ፡ ለጣልያን ፡ መንግሥት ፡ እንዳትገዛ ፡ ገዝቻለሁ ፡ ብለው ፡ የተቀደሰው ፡ ሰውነታቸው ፡ በመሬታቸው ፡ ላይ ፡ ሲወድቅ ፡ ባየሁ ፡ ጊዜ ፡ በማነበው ፡ መጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ ውስጥ ፤ ፀሓይን ፡ እንዳትጠልቅ ፡ በትእዛዝ ፡ ያቆሙ ፤ ዝናብ ፡ እንዳይዘንብ ፡ የከለከሉ ፡ አባቶቻችን ፡ ትዝ ፡ አሉኝ ።

አሁንም ፡ አምናለሁ ፡ ብፁዕ ፡ አባታችን ፡ በኢትዮጵያ ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ያደረጉት ፡ ርግማንና ፡ ግዝት ፡ የኢትዮጵያን ፡ መሬት ፡ ለጠላት ፡ እሾህ ፡ ሳያደርጋት ፡ አይቀርም ።

እስላም ፡ ፋጡማ ፤ በር ፡ ትመታለች ።
ሸዬ ፡ አደፍርሰው ፡ ማነው ፡ በር ፡ የሚመታ ፤
ፋጡማ ፤ -እኔ ፡ ፋጡማ ፡ ነኝ ።

ሸዬ ፡ አደፍርሰው ፤ ጉድ ፡ ፈላላችሁ ፡ ሁሉንም ፡ ማንሠራው ፡ እዚሁ ፡ ልንያዝ ፡ ነው ፤ ይህች ፡ እስላም ፡ ቅድም ፡ የተነጋገርነውን ፡ ወደ ፡ ቤታችን ፡ ተጠግታ ፡ ሰምታን ፡ ይሆን ።

እመዬቴ ፡ ይግቡ ፡ እንደምን ፡ አመሹ ።

ፋጡማ፤-ምን ፡ ደኅና ፡ አመሻለሁ ፡ የአቡነ ፡ ጴጥሮስን፡አሟሟት፡ ጧት ፡ ካየሁ ፡ ወዲህ ፡ እስላም ፡ መሆኔን ፤ አስጥላኝ ፤ ወንድሞቼ ፡ እኔ ፡ ያየሁትን ፡ ነገር ፡ እናንተ ፡ ያያችሁት ፡ አይመስለኝም ።

አቡነ ፡ ጴጥሮስ ፡ ጥቍሩን ፡ ጨርቅ ፡ ከይናቸው ፡ ላይ ፡ አንሥ ተው ፡ሲጥሉት ፡ በፊት ፡ ለፊታቸው ፡ ዘምባባ ፡ የሚመስል ፡ የብርሃን፡ አክሊል ፡ አየሁ

አቡነ ፡ ጴጥሮስም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ወዳጁ ፡ ሲመጣ ፡ ፈገግ ፡ ብሎ፡ ሥቆ ፡ እንደሚቀበለው ፡ ፈገግታ ፡ ሲያሳዩ ፡ ተኵስ ፡ ተተኰሰ ፤ ከዚያ፡ በኋላ ፡ መሬት ፡ ዘረጥኝና ፡ ቍጭ ፡ አልኩ ። ጥቂት ፡ ሲሻለኝ ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ ሄድኩ ። ወላሂ ፡ በዚህ ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ የፈሰሰው ፡ የዚህ ፡ የቅዱስ ፡ ደም ፡ በኢትዮጵያ ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ያሉ ፡ ጣልያኖች ፡ ይቅ ሩና ፡ በሮማ ፡ ያሉትንም ፡ ጀሃነም ፡ ሆኖ ፡ እንደሚፈጃቸው ፡ አይጠረ ጠርም ። ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ እኒህ ፡ መነኵሴ ፡ በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ አር በኝነት ፡ ጀሃድ ፡ ብለው ፡ ሲሞቱ ፡ ባየሁ ጊዜ ፡ የክርስቲያንን ፡ ሃይማ ኖት ፡ አከበርኩ ።

ፋጡማ ፡ በጕልበቷ ፡ ተንበርካ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ብርታት ፡ ነው ፤ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ዕድል ፡ ነው ፤ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ያገር ፡ ኵራት ፡ ነው ፤ ለሃይማኖቱና ፡ ላገሩ ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ክብር ፡ ጀሃድ ፡ ብሎ ፡ መሞት ፤ ጴጥሮስ ፡ ጴጥሮስ ፡ ጴጥሮስ ፡ አንተ ፡ ብትሞት ፡ ታሪክኽ ፡ ዘለዓለም ፡ አይሞትም ።

ፊቷን ፡ በሁለት ፡ እጅዋ ፡ ሸፍና ፡ ትቆማለች ።

## የሚያሳዝን ፡ ሙዚቃ ።

### መ ዝ ሙ ር ።

ላገራቸው ፡ የሚሞቱ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ክብራቸው ።
ጴጥሮስ ፡ ሐዋርያ ፡ ተፍጻሜተ ፡ ሰማዕት ፤
ደሙን ፡ አፈሰሰ ፡ ለናቱ ፡ ሞተላት ።

ምንኛ ፡ ያኰራል ፡ የወለዱት ፡ ከቶ ፤
ለናቱ ፡ ሞተላት ፡ ግንባሩን ፡ መክቶ ።

ሙሴ ፡ ዝማ ፡ ወርዶ ፡ ታሪክ ፡ ሲመለከት ፡
አንድ ፡ እሥራኤላዊ ፡ ለማጠብ ፡ አልባሳት ፡
እንዶድ ፡ በጠበጠ ፡ ልብሱን ፡ ሊነክርበት ።

የተዘጋጀውን ፡ ግብጻዊ ፡ አየና ፡
አትንከር ፡ ልብስኽን ፡ እኔ ፡ አጥባለሁና ፤
ብሎ ፡ ትእዛዝ ፡ ሲሰጥ ፡ ሙሴ ፡ ተመልክቶ ፤
በተሠራውም ፡ ግፍ ፡ በጣም ፡ ተጸጽቶ ፤

እሱ ፡ ባዘጋጀው ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ታጥብበት ፡
ብሎ ፡ ለግብጻዊ ፡ ሙሴ ፡ መለሰለት ፤
መልስ ፡ አረገና ፡ ፊቱን ፡ በትዕቢት ፤
እንኳን ፡ በንዶዱና ፡ በደሙስ ፡ ባጥብበት ፡
ማን ፡ ያስገድደኛል ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።

ይኸን ፡ ቃል ፡ በመስማት ፡ ሙሴ ፡ ተቆጥቶ ፤
ግብጻዊን ፡ ቀበረው ፡ በግዜር ፡ ኃይል ፡ መቶ ።

ሙሴ ፡ ለወገኑ ፡ ተቈርቋሪ ፡ ሆኖ ፡
ቀብሮት ፡ እንደ ፡ ሄደ ባሸዋ ፡ ሸፍኖ ።

ከወገናችንም ፡ የተቀበው ፡ ጳጳስ ፡
አሓሓቱ ፡ ሆነ ፡ ታሪኳን ፡ የሚያድስ ።

የበጎች ፡ እረኛ ፡ ጴጥሮስ ፡ ሐዋርያን ፡
ተኵላ ፡ ቢመጣበት ፡ ሊነጥቅ ፡ በጎቹን ፤
ተኵላ ፡ ሲፈጃቸው ፡ ዐይኔ ፡ አያይም ፡ ብሎ ፡
ከበጎቹ ፡ በፊት ፡ ሞተ ፡ ተከልሎ ።

የኢትዮጵያ ፡ ሰማዕት ፡ ጴጥሮስ ፡ በወህኒ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ሳለ ፡ የሞት ፡ ጥላ ፡ በወደቀችባት ፡ በዚያች ፡ በጭንቅ ፡ ሰዓት ፡ ለኢትዮጵያና ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ያደረገው ፡ ጸሎት ፡ ያፈሰሰው ፡ ዕንባ ፡ የፋሺስትን ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ተራራ ፡ ፈንቅሎ ፡ ጥሎ ፡ ተለያይተን ፡ የነበረውን ፡ አገናኘን ።

መድኃኒታችን ፡ የሰናፍጭ ፡ ቅንጣት ፡ የምታኽል ፡ ሃይማኖት ፡ ብትኖራችሁ ፡ ይኽንን ፡ ተራራ ፡ ከስፍራኽ ፡ ተነሥተኽ ፡ ሂድ ፡ ለማለት ፡ ትችላላችሁ ፡ ያለው ፡ ተፈጸመ ። በእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ነፃነታችን ፡ ከተመለሰ ፡ በኋላ ፡ ባ፲፱፻፴፫ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ ሐምሌ ፡ ፳፱ ፡ ቀን ፡ የሰማዕቱ ፡ የጴጥሮስ ፡ ደም ፡ ከፈሰሰበት ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ቆመው ፡ ጴጥሮስ አንተ ፡ ብትሞት ፡ ስምኽ ፡ ለዘለዓለም ፡ ሕያው ፡ ነው ብለው ፡ ተናገሩ ።

በፋሺስት ፡ እግር ፡ የተረገጠና ፡ የተናቀ ፡ ሥጋውም ፡ ለምድረ ፡ በዳ ፡ አራዊት ፡ የተሰጠ ፡ ጴጥሮስ ፡ የክብሩ ፡ ፋና ፡ በዓለም ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ አበራ ፤ በእግዚአብሔር ፡ መልክ ፡ የተፈጠረ ፡ ሰው ፡ ሰውነቱን ፡ በምን ፡ ስፍራ ፡ ማዋል እንደሚገባው ፡ አሳየ ። ከእግዚአብሔር ፡ ጋራ ፡ ሥራውን ፡ በቁም ፡ ነገር ፡ የሚዠምር ፡ እንደዚሁም ፡ ሥራውን ፡ በቁም ፡ ነገር ፡ ይጨርሳል ፡ እንደ ፡ ተባለው ። በደም ፡ የተነከረ ፡ የፋሺስት ፡ ፋስ ፡ ተሰባብሮ ፡ ሲወድቅ ፡ እነሆ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥታችን ፡ ተመልሰው ፡ መስቀሉን ፡ የተሸከመ ፡ መከራውን ፡ የታገሠ ፡ የጴጥሮስን ፡ ሐውልት ፡ ለማቆም ፡ ዕድለኛ ፡ ሆኑ ።

አትፍሩ ፡ ሥጋን ፡ ከሚገድሉ ፤ ነፍስን ፡ መግደል ፡ አይቻላቸውምና ።



# የድኾች ፡ ከተማ ፡፡

ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ።

ባ፲፱፻፵፩ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡

ክራስ ፡ ቢ ፡ መኰንን ፡ እንዳልካቸው ፡ ተጻፈ ።

ታርሞ ፡ አራተኛ ፡ ታተመ ።

---

# መግቢያ ።

ይህ ፡ የድሆች ፡ ከተማ ፡ ተብሎ ፡ የተሠየመ ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ ሁለት ፡ መሠረታውያን ፡ የሆኑ ፡ ነገሮችን ፡ ያሳስባል ።

፩ኛ ፤ ጌቶች ፡ በተሰጣቸው ፡ ብዙ ፡ ሀብት ፡ ላይ ፡ ሰፊ ፡ የሆነ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ አላፊነት ፡ እንዳለባቸው ፡ ያስታውሳል ፤ እንጀራህን ፡ በውሃ ፡ ውስጥ ፡ ጣል ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ሀብታምም ፡ ሀብቱን ፡ ለራሱና ፡ ለወዳጅ ፡ ለዘመድ ፡ ብቻ ፡ ሳይል ፡ የሰውን ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ መልካም ፡ መጋቢ ፡ እንዲያስተዳድርበት ፡ መሰጠቱን ፡ ያመለክታል ።

ደግሞም ፡ ይህ ፡ ጽሑፍ ፡ ገንዘባችሁ ፡ ባልሆነው ፡ ገንዘብ ፡ ወዳጅ ፡ ግዙበት ፡ እያለ ፡ ያስገነዝባል ።

፪ኛ ፤ ድኽነት ፡ ወዳጆችን ፡ ያርቃል ፤ ሀብት ፡ ግን ፡ ወዳጆችን ፡ ያቀርባል ፡ እንደተባለው ፡ ለድኾች ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ወዳጅና ፡ ባልንጀራ ፡ ለማግኘት ፡ ችግር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፤ ይህ ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ ለድኾች ፡ የታመነ ፡ ወዳጅና ፡ ጓደኛ ፡ እንዲሆናቸው ፡ የተሰጠ ፡ ነው ።

አንድ ፡ ድኻ ፤ ይህነን ፡ የድሆች ፡ ከተማ ፡ የተባለ ፡ መጽሐፍ ፡ የታመነ ፡ ጓደኛ ፡ አድርጎ ፡ በብብቱ ፡ ይዞ ፡ እዛፍ ፡ ሥር ፡ የለመለመ ፡ ሣር ፡ ካለበት ፡ ላይ ፡ ጋደም ፡ ብሎ ፡ ቢያጫውተውና ፡ ቢያነጋግረው ፡ ከሀብታምነት ፡ ድኽነትን ፤ ብዙ ፡ ከማግኘት ፡ በመጠን ፡ በመኖር ፡ የሚገኙትን ፡ ጥቅሞች ፡ ያስተምረዋል ።

ይልቁንም ፡ በሀብታምነት ፡ ምክንያት ፡ በሰው ፡ ልጆች ፡ ላይ ፡ የሚደርስባቸውን ፡ ጭንቅና ፡ ሐሳብ ፤ ደዌና ፡ ሕልም ፤ ቅዠትና ፡ የሐሳብ ፡ በሽታ ፡ ሌላውንም ፡ የጭንቅ ፡ ምሥጢር ፡ ገልጾ ፡ ያሳየዋል ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ይህ ፡ ድኻ ፡ ከታመነ ፡ ወዳጁ ፡ ይህነን ፡ ምሥጢር ፡ ከተነጋገረ ፡ ወዲህ ፡ በውነት ፡ በትልቅ ፡ ግንብ ፡ ውስጥ ፡ ተቀምጦ ፡ በጭንቅ ፡ ያገኘውን ፡ ገንዘብ ፡ የሚያስቀምጥበት ፡ የታመነ ፡ ቦታ ፡ ከሚፈልግ ፡ ሀብታም ፡ ይልቅ ፡ በርሻ ፡ ውስጥ ፡ የሚናፈስ ፡ ገበሬ ፡ እንደሚበልጥ ፡ ይረዳዋል ።

እንደዚህም ፡ ይላል ፤ ‹በዚህ ፡ ዓለም ፡ የከፋውም ፤ ደስ ፡ ያለውም ፡ የለም ፤ ከሁሉም ፡ ኑሮ ፡ የኔ ፡ የተሻለ ፡ ነው ፤ በግን ባሬ ፡ ወዝ ፡ ባገኘሁት ፡ ጥቂት ፡ ነገር ፡ ደስ ፡ ይበለኝ ።›

የሰው ፡ ልጆች ፡ ከክፉ ፡ ስሕተት ፡ ጉድጓድ ፡ የሚወድቁ ፡ የመንፈሳዊ ፡ ጓደኛ ፡ በማጣት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የታወቀ ፡ ነው ፤ ስለዚህ በችግር ፡ ጊዜ በድኽነት ፡ ምክንያት ፡ የሰው ፡ ወዳጆች ፡ ቢታጡ ፡ እንኳ ፡ ጊዜ ፡ አይቶ ፡ የማይወድ ፤ ጊዜ ፡ አይቶ ፡ የማይጠላ ፡ የታመነ ፡ ወዳጅኽ ፡ መጽሐፍን ፡ ከብብትኽ ፡ ውስጥ ፡ አትለየው ፤ ጠይቀው ፡ ተጨዋወተው ፡ ሁሉንም ፡ ይገልጥልኻል ።



## መ ቅ ድ ም ።

የዚህ ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ መነሻ ፡ የሆነውን ፡ ያቶ ፡ሀብ ትኽ ፡ ይመርን ፡ የሕይወት ፡ ታሪክ ፡ እናሳስባለን ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ያንድ ፡ ችጋረኛ ፡ ንፉግ ፡ ሥሥ ታም ፡ አቶ ፡ ንዋይ ፡ የሚባል ፡ ሰው ፡ ልጅ ፡ ነው ።

አቶ ፡ ንዋይም ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ከሚስቱና ፡ ከገልጋዮቹ ፡ ጋራ ፤ በውጭም ፡ ከጎረቤቶቹ ፡ ጋራ ፡ የሚጨቃጨቅና ፡ የሚነዛነዝ ፡ ጠባየ ፡ ክፉ ፤ ቢስ ፤ ጨቅ ፡ ሰው ፡ ነበረ ።

ይልቁንም ፡ ያፍ ፡ ክርስቲያን ፡ በመሆኑ ፡ ኀሊናውንና ፡ ክርስ ቲያንነቱን ፡ ለገንዘብ ፡ ሲሸጥ ፤ ሲለውጥ ፡ በመታየቱ ፡ የሚያው ቀው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በሱ ፡ ላይ ፡ እምነት ፡ የለውም ፤ ልጁም ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በሕፃንነቱ ፡ ያባቱን ፡ ባሕሪ ፡ እንደ ፡ መጽ ሐፍ ፡ እያጠና ፡ ያባቱን ፡ ፍለጋ ፡ ተከትሎ ፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ መን ገድ ፡ ይጓዛል ።

አቶ ፡ ንዋይ ፤ ትንሽ ፡ ገንዘብ ፡ እንኳ ፡ ቢያገኝ ፡ በመሠሠቱ ፡ ምክንያት ፡ ከሚስቱ ፡ ከወይዘሮ ፡ ይመኙሻል ፡ ለመሸሸግና ፡ በጓ ሮው ፡ ውስጥ ፡ ከመሬት ፡ ለመቅበር ፡ ሲሽሎከለክ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ያይ ፡ ነበር ።

ወይዘሮ ፡ ይመኙሻልም ፡ ሸሻጊ ፡ ባይኖር ፡ ሌባ ፡ አይገኝም ፡ ነበር ፡ እንደ ፡ ተባለው ፤ ባሏ ፡ በመሠሠት ፡ በሚያደርገው ፡ ስርቆት ፡ ምክንያት ፡ እሷም ፡ በመዘንጋት ፡ የሚጥለውን ፡ ገንዘብ ፡ ስትሸሽ ግና ፡ ስትደብቅ ፡ ይመለከታል ።

ሁለቱ ፡ ባልና ፡ ሚስት ፡ በችግርና ፡ በሥሥታምነት ፡ ምክን ያት ፡ የቤታቸው ፡ ሌቦች ፡ ሲሆኑ ፤ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርም ፡ በሕ ፃንነቱ ፡ የናቱንና ፡ ያባቱን ፡ ክፉ ፡ ጠባይ ፡ የሚያጠና ፡ ተማሪ ፡ ነበረ ።

አቶ ፡ ንዋይና ፡ ወይዘሮ ፡ ይመኙሻል ፡ እሑድና ፡ በያመት ፡ በዓሉ ፡ ልጃቸውን ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርን ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሲሄዱ ፡ ድኾች ፡ ወንድሞቻቸው ፤ አንካሶች ፤ ዕውሮች ፡ በሽተኞች ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ እየጠሩ ፡ ሲለምኑ ፡ የለማኝ ፡

ለማኝ ፡ ቊረንጮዬን ፡ ቀማኝ ፡ የሚባለውን ፡ አታውቅምን ፡ እኔ ፡ ራሴ ፡ ድኻ ፡ ምን ፡ እሰጥኻለሁ ፡ ከፊቴ ፡ ሂድ ፡ ብለው ፡ ሲያባር ሩት ፤ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርም ፡ ከናቱና ፡ ከባቱ ፡ ጭካኔን ፡ ስለ ፡ ተማረ ፡ በድኾች ፡ ላይ ፡ ድንጋይ ፡ ይወረውራል ።

አቶ ፡ ንዋይ ፤ በችግር ፡ የሚበልጠው ፡ ድኻ ፡ ሲለምነው ፡ አያዝንለትም ፡ አይራራለትም ።

ያገሩ ፡ ባላገሮች ፡ ድኾች ፡ ወንድሞቻቸውን ፡ እንዳቅማቸው ፡ በልብሳቸው ፡ ጥሬ ፡ ይዘው ፡ ያችኑ ፡ ንጹሕ ፡ መሥዋዕት ፡ ሲያካ ፍሉ ፤ አቶ ፡ ንዋይ ፡ ከነባለቤቱ ፡ እንደ ፡ ኀጢአት ፡ ይቈጥረው ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ንዋይ ፤ በመጠን ፡ በመኖር ፡ ያለን ፡ ዕረፍት ፤ በሀብታ ምነት ፡ ያለን ፡ ጭንቅ ፤ ባለማሰብና ፡ ባለማወቅ ፡ ሲጫወት ፡ የተለ መደ ፡ ተረቱ ፡ ገንዘብ ፡ ካለ ፡ በሰማይ ፡ መንገድ ፡ አለ ፡ ነው ።

እንዲያውም ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ሎነኔ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ነው ። ድኻ ፡ ሰው ፡ አሁኑኑ ፡ የተኰነነ ፡ ነው ፤ ሀብታም ፡ ሰው ፡ ግን ፡ የጸደቀ ፡ ነው ፡ እያለ ፡ ከጎረቤቶቹ ፡ ከሚስቱ ፡ ከልጁ ፡ ጋራ ፡ ሳያ ፍር ፡ ይከራከራል ።

ይህ ፡ ሁሉ ፡ ላቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ የክፉ ፡ ጠባይ ፡ መማ ሪያ ፡ ተማሪ ፡ ቤቱ ፡ ሆነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ሰው ፡ ያየውን ፡ ይመስላል ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ከባቱ ፡ ያየውን ፡ ለመሥራት ፡ በሕፃንነቱ ፡ ከልጆች ፡ ጋራ ፡ ሲጫወት ፡ ኳሱንም ፡ ጠጠሩንም ፡ ዶቃውንም ፡ ጥንጉንም ፡ ማንኛውንም ፡ የልጆች ፡ መጫወቻ ፡ እየሰረቀ ፡ ለራሱ ፡ ይወስድና ፡ ይደብቅ ፡ ነበር ፤ ብዙም ፡ ጠጠሮች ፡ እየለቀመ ፡ ገንዘ ቤን ፡ ሚስቴ ፡ እንዳታይብኝ ፡ እያለ ፡ ከመሬት ፡ ይቀብራል ።

ሰው ፡ የዋለበትን ፡ ይመስላል ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ አቶ ፡ ሀብ ትኽ ፡ ይመር ፡ በዝርዝር ፡ አባቱና ፡ እናቱ ፡ የሚሠሩትን ፡ ክፉ ፡ ጠባይ ፡ ከሕፃንነቱ ፡ ዠምሮ ፡ ለዐቅመ ፡ አዳም ፡ እስኪደርስ ፡ ድረስ ፡ አጠና ።

ወይዘሮ ፡ ይመኙሻልም ፡ ለምግባቸው ፡ ራሷ ፡ ፈልጋ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ አቶ ፡ ንዋይ ፡ በዝንጋታ ፡ የጣለውን ፡ ገንዘብ ፡

ሰርቃ ፡ ወይም ፡ በቤታቸው ፡ ጓሮ ፡ የተተከለውን ፡ ቃሪያ ፡ በር በሬ ፡ ቀጥፋ ፡ ሽንኩርት ፡ ነቅላ ፡ ሽጣ ፡ ምግባቸውን ፡ ታሰናዳ፡ ነበር ፡ እንጂ ፤ አቶ ፡ ንዋይ ፡ ስለ ፡ ቤት ፡ ወጪ ፡ ምንም ፡ አይሰ ጣትም ።

ስለዚህ ፡ ወይዘሮ ፡ ይመኙሻል ፡ ከባሏ ፡ ድኽነት ፡ ይልቅ ፡ የባሏ ፡ ሥሥትና ፡ ክፉ ፡ ምግባር ፡ ስላስቸገራት ፡ መፋታት ፡ ግድ ፡ ሆነባትና ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ የመንደር ፡ ዳኛ ፡ እንዲያፋታት፡ ይዛ ፡ መጣች ።

ዳኛውም ፡ አቶ ፡ ንዋይን ፡ አስጠርቶ ፡ ሚስትኽ ፡ ልፋታ ፡ ትላለች ፡ ስለዚህ ፡ አንተ ፡ ቄራቢ ፡ ነኝ ፡ አልፋታም ፡ ወይም ፡ ውል ፡ አለኝ ፡ የምትለው ፡ ነገር ፡ አለን ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ።

አቶ ፡ ንዋይም ፤ ከገንዘብ ፡ በቀር ፡ የሚወደው ፡ ስለሌለ ፡ ምንም ፡ ለመፋታት ፡ የሚያግድ ፡ ነገር ፡ በሁለታችን ፡ መከከል፡ የለም ፤ ከፈለጋት ፡ እፈታታለሁ ፡ ብሎ ፡ አስታወቀ ።

ዳኛውም ፤ እንግዲያስ ፡ ትዳራችሁ ፡ ትንሽ ፡ ስለሆነ ፡ ሰማኒያ ፡ ከመውረዱ ፡ በፊት ፡ ገንዘባችሁን ፡ ተካፈሉ አላቸው ።

አቶ ፡ ንዋይም ፤ እንደሚያውቁት ፡ እኛ ፡ ችግረኞች ፡ ዶኾች ፡ ስለሆን ፡ ከዚህ ፡ ከቤት ፡ ዕቃችን ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ ገንዘብ፡ የለንም ፡ ይህነኑ ፡ እንካፈል ፡ ብሎ ፡ ሲናገር ፡ ወይዘሮ ፡ ይመኙሻል ፡ ምንም ፡ ገንዘብ ፡ የለንም ፡ ብለኽ ፡ በእግዚአብ ሔርና ፡ በዳኛ ፡ ፊት ፡ አሰት ፡ መናገር ፡ ይገባኻልን ፤ ከኔ ፡ ሸሽ ገህ ፡ ከጓሮ ፡ የቀበርከውን ፡ ገንዘብ ፡ ያላየሁ ፡ ይመስልኻልን ፤ የተቀበረበትን ፡ ቦታ ዐውቀዋለሁና ፡ በዳኛ ፡ ይውጣልኝና ፡ ልካፈል ፡ ብላ ፡ አስታወቀች ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ንዋይ ፡ በድንጋጤ ፡ ዣርው ፡ ደም ፡ መስሎ ፡ የሚመልሰውን ፡ ነገር ፡ አጥቶ ፡ እየተርበደበደ ፡ ገንዘብ ፡ የለኝም ፡ እያለ ፡ ስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ እየጠራ ፡ ይምል ፡ ዠመር ።

ዳኛውም ፡ ከውጭ ፡ ሦስት ፡ እማኞች ፡ ያገር ፡ ጨዋዎች፡ አስጠርቶ ፡ ባልና ፡ ሚስቱን ፡ አስቀድሞ ፡ ወደ ፡ ጓሮ ፡ ሄደ ።

ዳኛውም ፡ እንግዴህ ፡ በቃውን ፡ አሳዩኝ ፡ አላት ፤ እሷም፡ በቃውን ፡ አሳየች ። ዳኛው ፡ በሉ ፡ ቄፍሩ ፡ ብሎ ፡ ቢያ ስቈፍረው ፡ አንድ ፡ ሺሕ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ብር ፡ ተገኘ ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ንዋይ ፡ ከዳኛው ፡ እግር ፡ ላይ ፡ ወድቆ፡ ከሚስቴ ፡ አስታርቁኝ ፤ እያለ ፡ ይለምን ፡ ዠመር ።

ወይዘሮ ፡ ይመኙሻልም ፡ አልታረቅም ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ኀዘ ንና ፡ ለቅሶ ፡ ከገንዘቡ ፡ ጋራ ፡ እንዳይፋታ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ለኔ ፡ መፋታት ፡ አዝኖ ፡ አይደለም ፡ ብላ ፡ እንቢ ፡ ስላለች ፡ ገንዘቡንም ፡ ለሁለት ፡ ዕቃቸውንም ፡ ለሁለት ፡ አካፍለው ፡ ለሁለቱም ፡ ድርሻቸውን ፡ ሰጥተው ፡ ዳኛውም ፡ እማኞቹም ፡ ወደየቤታቸው ፡ ሄዱ ።

አቶ ፡ ንዋይም ፤ ከዚያ ፡ ቀን ፡ ዠምሮ ፡ ምንም ፡ ጤናና፡ ሕይወት ፡ ሳያገኝ ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ ታሞ ፡ ሞተ ።

ልጁም ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ አባቱ ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ያባቱንና ፡ የናቱን ፡ ክፉ ፡ ጠባይ ፡ ከሕፃንነቱ ፡ ዠምሮ ፡ እንደ ፡ ተማሪ ፡ ቤት ፡ ካጠና ፡ ወዲያ ፡ ከዳግማዊ ፡ ምኒልክ፡ ትምህርት ፡ ቤት ፡ ገብቶ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ቋንቋና ፡ ጽሕ ፈት ፡ ሒሳብ ፡ ተማረ ።

ነገር ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አገር ፡ ሄዶ ፡ ትምህርቱን ፡ ለመቀጠል ፡ ገንዘብና ፡ የሚረዳው ፡ ዘመድ ፡ በማጣቱ ፡ ይል ቁንም ፡ በዕድሜው ፡ ምክንያት ፡ የትምህርቱ ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ ተላለፈበትና ፡ የማይችል ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ወደ ፡ ንግድ ፡ ሥራ ፡ አሳቡን ፡ ሁሉ ፡ አዘነበለ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ዕዉሪቱ ፡ ዕድል ፡ በዳበሳ ፡ አቶ ፡ ሀብ ትኽ ፡ ይመርን ፡ ስለ ፡ መረጠችው ፡ ባገሩም ፡ በውጭ ፡ አገ ርም ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ሀብታም ፡ ሆነ ።

ዳሩ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ሚሊዮኔር ፡ ቢሆን ፤ አባቱን ፡ የገደለ፡ ችግርና ፡ ሥሥት ፡ ሀብቱን ፡ ሁሉ ፡ ዘሎ ፡ ጕሮሮውን ፡ ያነቀው ፡ እየመሰለው ፡ ገንዘቡን ፡ ሲያወጣ ፡ ይንቀጠቀጥ ፡ ነበር ።

ይልቁንም ፡ አባታና ፡ እናቱ ፡ ቤት ፡ በሕፃንነቱ ፡ ያየውን ፡ የኑሮን ፡ ችግርና ፡ ያለመተማመን ፡ ቲያትር ፤ ዘወትር ፡ በፊቱ ፡

ሲያልፍ ፡ ከገንዘብ ፡ በቀር ፡ ዘመድ ፡ የለም ፡ የሚል ፡ አሳብን ፡ ያስታውሰዋል ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርም ፡ ከሕፃንነት ፡ ዝምሮ ፡ ለዐቅመ ፡ አዳም ፡ እስኪደርስ ፡ ድረስ ፡ ከባቱና ፡ ከናቱ ፡ ቤት ፡ ያጠናውን ፡ ክፉ ፡ ልምድ ፡ እንዳረጀ ፡ ልብስ ፡ አውልቆ ፡ ለመጣል ፡ ችግር ፡ ሆነበት ።

ልምድ ፡ ከሰይጣን ፡ ይከፋል ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ከልምድ ፡ ለመላቀቅ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ችግር ፡ ያለ ፡ ይመስልኻል ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ ልምድ ፡ እንደ ፡ ደዌ ፡ ሥጋ ፡ እንደ ፡ ቈዳ ፡ በሽታ ፡ አብሮ ፡ በመኖር ፡ የሚተላለፍ ፡ በሽታ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በዘር ፡ የሚተላለፍ ፡ ደዌ አይደለም ።

ለምሳሌ ፤ ብዙ ፕሮፌሰሮችና ፡ ሐኪሞች ፡ ደዌ ሥጋ ፡ ሌሎችም ፡ የቈዳ ፡ በሽታዎች ፡ አብሮ ፡ በመኖር ፡ በመቀራረብ ፡ የሚጋቡ ፡ መሆናቸውን ፡ በሲያንስ ፡ እንዳጠኑትና ፡ እንደ ፡ ተረዱት ፡ እንደዚሁም ፡ ሰው ፡ በሚያድግበት ፡ ቤት ፡ መጥፎ ፡ ልምድና ፡ ክፉ ፡ ጠባይ ፡ እንደ ፡ በሽታ ፡ እንደሚጋባበት ፡ ተረድተነዋል ።

የሰው ፡ ልጅ ፡ ከናቱ ፡ ማሕፀን ፡ ሲወጣ ፤ እንደ ፡ ሬት ፡ ከመረረችው ፡ ዓለም ፡ ውስጥ ፡ ሲጣል ፡ በሕሪው ፡ ንጹሕ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የመረረ ልቅሶ ፡ ያለቅሳል ፤ እኛ ፡ ግን ፡ ባለማወቅ ፡ በእልልታ ፡ በጭብጨባ ፡ በደስታ ፡ እንቀበለዋለን ።

በውነት ፡ አርቀን ፡ ስናስብ ፡ ሕፃናት ፡ በቤተ ፡ ዘመዶቻቸው ፡ የልምድ ፡ ደዌ ፡ ስላልታመሙ ፡ የሕፃናት ፡ አስተያየት ፡ ከኛ ፡ የተሻለ ፡ ነበረ ፡ ለማለት ፡ ያስደፍራል ።

ነገር ፡ ግን ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ጥቂት ፡ በጥቂት ፡ አብሮ ፡ በመኖርና ፡ በመላመድ ፡ እንደ ፡ ቤተ ፡ ሰቡ ፡ ምግባር ፡ ዐይነት ፡ ሕፃናት ፡ የልምድ ፡ በሽታ ፡ ስለሚተላለፍባቸው ፡ ንጹሕ ፡ ባሕሪያቸው ፡ በመጥፎ ፡ ጠባይ ፡ ይመረዛል ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሲወለድ ፡ ያጠለቀውን ፡ ሲሞት ፡ ያወልቀዋል ፡ እንደተባለው ፤ እስከ ፡ መቃብር ፡ ድረስ ፡ ለብሰውት ፡ ይኖራሉ ። የቤተ ፡ ዘመድን ፡ የመጥፎ ፡ ምግባርን ፡ ትምህርትና ፡ የልምድን ፡ ቀሚስ ፡ ማውለቅ ፡ ችግር ፡ ነው ።

ልምድ ፡ ከሰውነት ፡ በላይ ፡ ነው ። ልምድ ፡ የሚሠራውን ፡ ማንም ፡ አይሠራውም ፤ ልምድ ፡ ሦስት ፡ ዓይነት ፡ ጠባይ ፡ አለው ።

፩ኛው ፤ ደኅናው ፡ ጠባይ ፡ ሰውነትን ፡ ለመግታት ፡ ይህ ፡ በእጅ ፡ የሚዳሰሰው ፡ ዓለም ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በማወቅ ፡ ጠባዩም ፡ መጥፎ ፡ መሆኑን ፡ በመመልከት ፡ ሰውነታቸውን ፡ የገቱ ፤ በፈቃዳቸው ፡ ሥጋቸውን ፡ ችግርን ፡ በማስለመድ ፡ ያበ ረቱ ፡ ስለ ፡ ጽድቅ ፡ የተራቡና ፡ የተጠሙ ፡ የመንፈሳዊን ፡ ልምድ ፡ ያዘወተሩ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ አስተያየት ፡ ያላቸው ፡ ሰዎች ፡ በመንፈሳዊ ፡ ዕውቀት ፡ ከምን ፡ እንደ ፡ ደረሱ ፡ ብዙ ፡ መጻሕ ፍት ፡ አንበናል ።

፪ኛው ፤ ሰውነትን ፡ በጅምናስቲክ ፡ በማጠንከር ፡ ከሰው ፡ ልጅ ፡ ዐቅም ፡ በላይ ፡ የሆነውን ፡ ከባድ ፡ ነገር ፡ ማንሣት ፡ የቻሉ ፤ ሰው ፡ ሊሄድበት ፡ የማይችለውን ፡ በቀጭን ፡ ሽቦ ፡ ላይ ፡ በመሄድ ፤ ሌሎች ፡ እጅግ ፡ የሚገርሙ ፡ (በኤኬሊ.ቢ.ር) ፡ በሚ ዛን ፡ በቅልጥፍና ፡ ልምድ ፡ የሚሠሩ ፡ «እንዳክሮባሲ» ፡ ያሉ ፡ ነገሮች ፡ በማድረግ ፡ የቀለጠፉ ፡ በዝላይም ፡ በሩጫም ፡ ሌሎችም ፡ በልምድ ፡ ሥርን ፡ በሚያበረቱና ፡ ጡንቻን ፡ በሚያሳብጡ ፡ በጅምናስቲክ ፡ ልምዶች ፡ የሚሠሩ ፡ ናቸው ።

፫ኛ ፤ ክፉው ፡ ጠባይ ፤ የሰው ፡ ልጅ ፡ የሚፋጅ ፡ ሙብል ፡ ኀይሉ ፡ አለመጠን ፡ የበረታ ፡ መጠጥ ፡ አፉ ፡ የለመደ ፡ እንደ ሆን ፡ እሳት ፡ ለመጕረስ ፡ ይችላል ።

የሰው ፡ ልጅ ፡ አፍንጫው ፡ መጥፎ ፡ ሽታ ፡ የለመደ ፡ እንደሆን ፡ ከሽቱ ፡ ይበልጥ ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፤ ዐይኑ ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ ከለመደ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የተፈጠሩት ፡ ነገሮች ፡ አንሰ ውት ፡ ሌላ ፡ ፍጥረት ፡ ለማየት ፡ ይጥራል ።

ሰው ፡ የሰው ፡ ገንዘብ ፡ ከለመደ ፡ የዓለም ፡ ገንዘብ ፡ ሁሉ ፡ ለሱ ፡ ብቻ ፡ ቢሆን ፡ ይወዳል ፤ ዓለምን ፡ መውደድ ፡ ከለመደ ፡ ይህ ፡ የተፈጠረው ፡ ዓለም ፡ አንሶት ፡ ሌላ ፡ ዓለም ፡ እንዲፈ ጠር ፡ ያስባል ። ደስታን ፡ ከለመደ ፡ ይህ ፡ በዓለም ፡ ላይ ያለው ፡ ደስታ ፡ አልሰማ ፡ እያለው ፡ ሌላ ፡ ደስታ ፡ ይመኛል ።

ሰው ፣ የሰው ፣ ደም ፣ ማፍሰስ ፣ የለመደ ፣ እንደሆነ ፣ በግ ፣ እንደሚያርድ ፣ ሥጋ ፣ ቤት ፣ (በጋማችን) ፣ ምንም ፣ አያሰቅ ቀውም ።

አንባቢ ፣ ሆይ ፣ ስለዚህ ፣ ነው ፣ ሕፃናትን ፣ ከልዩ ፣ ልዩ ፣ ቤተ ፣ ዘመድ ፣ ክፉ ፣ ጠባይና ፣ ልምድ ፣ በሽታ ፣ በሕፃንነት ፣ ወራት ፣ እንዳይጋባባቸውና ፣ በልምድ ፣ እንዳይያዙ ፣ ወደ ፣ ተማሪ ፣ ቤት ፣ መውሰድ ፣ ዋና ፣ ጠቃሚ ፣ ነገር ፣ የሆነው ።

ምክንያቱም ፣ ተማሪ ፣ ቤት ፣ የብዙ ፣ ፈላስፎች ፣ የብዙ ፣ የምግባር ፣ ሮማንሴ ፣ የጻፉ ፣ ሊቆች ፤ ብዙ ፣ የምግባር ፣ ቅኔ ፣ የተቀኙ ፣ ዐዋቂዎች ፣ ብዙ ፣ የሃይማኖትንና ፣ የመንፈሳዊን ፣ ኑሮ ፣ ጠቃሚ ነት ፣ የሚያስረዱ ፣ መጻሕፍት ፣ የጻፉ ፣ ሊቆች ፤ አገርን ፣ የሚያበለ ጥግ ፣ ድኽነትን ፣ የሚያጠፉ ፣ የሕዝብን ፣ ሞራል ፣ ከፍ ፣ የሚያደ ርግ ፣ የኤኰኖሚ ፣ መጽሐፍ ፣ የጻፉ ፣ ሰዎች ፤ የሰውን ፣ ልጆች ፣ የሚመርዙ ፣ ሚክሮቦችን ፣ የሚገድል ፣ የመድኃኒት ፣ መጻሕፍት ፣ ያወጡ ፣ ጠቢባን ፣ ብዙም ፣ ለሰው ፣ ልጆች ፣ ጥቅምና ፣ ላገር ፣ ልማት ፣ የሚሆኑ ፣ የሲያንስ ፣ መጻሕፍት ፣ የጻፉ ፣ ከፍ ፣ ያሉ ፣ ያዋ ቂዎች ፣ መምህራን ፣ ቤት ፣ ስለ ፣ ሆነች ፣ ሕፃናት ፣ በትምህርት ፣ ቤት ፣ የነሱ ፣ ልጆች ፣ የነሱ ፣ ቤተ ፣ ሰቦች ፣ ሆነው ፣ ያደጉ ፣ እንደ ሆነ ፣ ላገር ፣ ክብር ፣ ለቤተ ፣ ዘመድ ፣ ኵራት ፣ እንዲያውም ፣ ለዓ ለም ፣ ሁሉ ፣ ጠቃሚ ፣ ይሆናሉ ።

አቶ ፣ ሀብትኽ ፣ ይመር ፣ ግን ፣ አንድ ፣ ሰው ፣ በጽኑ ፣ ደዌ ፣ ብዙ ዘመን ፣ ከታመመ ፣ በኋላ ፣ ወደ ፣ ሆስፒታል ፣ እንደሚሄድ ፣ በቤተ ፣ ዘመዶቹ ፣ ክፉ ፣ ጠባይ ፣ ከተመረዘና ፣ ከታመመ ፣ በኋላ ፣ ከዳግማዊ ፣ ምኒልክ ፣ ትምህርት ፣ ቤት ፣ ቢገባ ፣ ምንም ፣ አልጠቀመውም ፤ ጥቂ ትም ፣ አልተፈወሰም ።

ቢሆንም ፣ አቶ ፣ ሀብትኽ ፣ ይመር ፣ አንዳንድ ፣ ጊዜ ፣ በባልንጀ ራው ፣ መሞት ፣ በሌሎችም ፣ በሚያሳዝኑ ፣ ነገሮች ፣ በመነካት ፣ የዚህ ፣ ዓለም ፣ ከንቱነት ፣ ቢታሰበው ፣ እንኳ ፣ በመንገድ ፣ ላይ ፣ እንደ ፣ ተዘራ ፣ እኽል ፣ ወዲያው ፣ አብረው ፣ ያደጉት ፣ ክፉ ልም ዶች ፣ እንደ ፣ ወፍ ፣ ይለቅሙትና ፣ ሳይበቅል ፣ ይቀራል ።

ስለዚህ ፣ ያቶ ፣ ሀብትኽ ፣ ይመር ፣ የመዠመሪያው ፣ አስተዳደጉ ፣ ስላላማረ ፣ የመጨረሻውም ፣ ሞቱ ፣ ሳያምር ፣ ቀረ ።

◆ ◆ ◆

## የ ድ ኻ ች ፡ ከ ተ ማ ።

### ም ዕ ራ ፍ ፡ ፩ ።

በኢትዮጵያ ፡ ውስጥ ፡ አንድ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ የሚ ባል ፡ ነጋዴ ፡ ሰው ፡ ነበር ፤ ይህ ፡ ነጋዴ ፡ ጥቅም ፡ ለማግኘት ፡ በመ ጣሩና ፡ በትጋቱ ፡ በጥቂት ፡ ቀን ፡ ውስጥ ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ሀብታም ሆነ ፤ ይህ ፡ ሰው ፡ ምንም ፡ ቢከብር ፡ ይበቃኛል ፡ የሚባለውን ፡ ቋንቋ ፡ አያውቀውም ። ዘወትር ፡ የዓለምን ፡ ገበያ ፡ ወሬ ፡ በመ ጠየቅ ፡ የዕረፍቱ ፡ ሰዓት ፡ ጥቂት ፡ ነበር ፤ የየመንግሥቱን ፡ ገንዘብ መውጣትና ፡ መውረድ ፡ በራዲዮ ፡ በቴሌግራም ፡ በደብዳቤም ፡ በመጻጻፍ ፡ ሌትም ፡ ቀንም ፡ ዕረፍት ፡ የለውም ።

በውጭ ፡ አገሮች ፡ ውስጥ ፡ ብዙ ፤ አክሲዮን ፡ ኦብሊጋሲዮን ፡ ስላ ለው ፡ በቡርስ ፡ ላይ ፡ የሚደረገውን ፡ የገንዘብ ፡ ትግል ፡ ለማወቅ ፡ ይጥራል ፤ ገንዘብ ፡ የልብ ፡ ሥር ፡ ነው ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ ልቡ በገንዘብ ፡ ፍቅር ፡ ስለ ፡ ተተበተበ ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡ ለማ ሰብ ፡ ጊዜ ፡ የለውም ።

ይህነን ፡ ነጋዴ ፡ በውነት ፡ ለተመለከተው ፡ ሰው ፡ ከሕይወቱ ፡ በኋላ ፡ ገንዘቡን ፡ ሁሉ ፡ አስጭኖ ፡ የሚሄድ ፡ ይመስል ፡ ነበር ፡ እንጂ ፤ ፈንታውን ፡ በልቶ ፡ የተረፈውን ፡ ለሌላ ፡ ባለፈንታ ፡ ጥሎ ፡ የሚሄድ ፡ አይመስልም ።

ይልቁንም ፡ በጣም ፡ የሚያስገርመው ፡ ጥቅም ፡ ለማግኘት ፡ ማን ኛውንም ፡ ኃጢአት ፡ ለመሥራት ፡ አያሰቅቀውም ።

ስለ ፡ ገንዘብ ፡ ማግኘት ፡ መዋረድ ፡ መናቅ ፡ መሰደብ ፡ መታማት፡ ምንም ፡ አያሳፍሩትም ፤ ስለ ፡ ጥቅም ፡ ምግባርን ፡ ክብራትን ፡ ይሉ ኝታን ፡ አሽቀንጥሮ ፡ ጥሏቸዋል ።

ለምሳሌ ፤ ይህ ፡ ሰው ፡ በሩቁ ፡ ገንዘብ ፡ አይቶ ፡ ሲሮጥ ፡ እግዚ አብሔር ፡ በመንገድ ፡ አግኝቶት ፡ አትሩጥ ፡ ትወድቅና ፡ ትሰባበራ ለኽ ፡ እኔ ፡ ሁሉንም ፡ ነገር ፡ አደርግልኻለሁ ፡ ብሎ ፡ በምሕረት ፡ እጁ ፡ ቢይዘው ፡ እንኳ ፡ ነጥቆት ፡ ይሄዳል ፡ እንጂ ፤ ያሰበውንም ጥቅም ፡ ካላገኘ ፡ ማንም ፡ ሊያቆመው ፡ አይችልም ።

ይህ ፡ ሀብታም ፡ ሰው ፡ ራሱን ፡ ብቻ ፡ ስለሚወድ ፡ ጥቅምን ፡ በማነፍነፍ ፡ ሲሮጥ ፡ የሱን ፡ ምኞት ፡ የሚገቱ ፡ የሱን ፡ አሳብ ፡ የሚያቆሙ ፡ የፍልስፍናና ፡ የምግባር ፡ መጻሕፍት ፡ አይገኙም ።

ስለ ፡ ጥቅም ፡ በዓለም ፡ ቋንቋ ፡ ይናገራል ፤ ጥቅም ፡ ለማግ ኘት ፡ ይህ ፡ ዓለም ፡ አንሶት ፡ ሌላ ፡ ዓለም ፡ እንዲፈጠር ፡ ይፈልጋል።

ይህ ፡ ሀብታም ፡ በጥቅም ፡ ክንፍ ፡ ዓለምን ፡ በሙሉ ፡ ይዞራል ፤ ምኞት ፡ በሕልሙ ፤ ማግኘት ፡ በውኑ ፡ እጁን ፡ ይዘውት ፡ ያንከራ ትቱታል ። በዚህ ፡ ዓለም ፡ ላይ ፡ አንዲት ሰከንድ ፡ እንኳ ፡ ለልቡ፡ ዕረፍት ፡ የለውም ፤ ለሰው ፡ ልጆች ፡ አጥፊ ፡ የሆነው ፡ ነገር ፡ ለሱ ፡ ዕድሉና ፡ ሀብቱ ፡ ነው ።

ለምሳሌ ፤ ጦር ፡ የሰው ፡ ዘር ፡ መታረ ፡ መቅሠፍት ፡ የሆነው ፡ ለሱ ፡ ነግዶ ፡ ስለሚያተርፍበት ፡ዋና ፡ መጠቀሚያው ፡ ነው ።

ሰላምን ፡ ይወዳል ፤ ምክንያቱም ፡ የሰበሰበውን ፡ ገንዘብ ፡ ያለሥ ጋት ፡ ለመብላት ፡ ነው ።

በዓለም ፡ ላይ ፡ ላቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ የማይስማማ ፡ አየር ፡ አይገኝም ፤ ዐመሉ ፡ እንደ ፡ ቅቤ ፡ የለሰለሰና ፡ በማንኛውም ፡ ጠባብ ፡ መንገድ ፡ ለመሹለክ ፡ የሚችል ፡ ረቂቅ ፡ ነው ።

ስለዚህ ፡ በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ብልጠትና ፡ ዕውቀት ፡ የተመሠ ረተ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ባገሩም ፡ በውጭ ፡ አገርም ፡ የንግድ ፡ ሥራዎች ፡ ተከናውነውለት ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ሀብታም ፡ ሆነ ።

የሚበልጠውም ፡ ሀብቱና ፡ የሥራ ፡ ጉዳዩ ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ልቡ ፡ አገሩ ፡ ውስጥ ፡ በመሆን ፡ ፈንታ ፡ ከገንዘቡ ፡ ጋራ ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ ውስጥ ፡ ነበር ።

ይልቁንም ፡ በትልልቆች ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ ከተሞች ፡ ውስጥ ፡ በሚ ገኙት ፡ ባንኮች ፡ ብዙ ፡ ገንዘብ ፡ ስላስቀመጠ ፡ የዘወትር ፡ አሳብና ፡ ጭንቁ ፤ ሁለተኛ ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ የተነሣ ፡ እንደሆን ፡ በሀብቴ ፡ ላይ ፡ ምን ፡ አደጋ ፡ ይደርስበት ፡ ይሆን ፡ በማለት ፡ ሌትም ፡ ቀንም ፡ ዕረፍት ፡ የለውም ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሄዶ ፡ ጸሎት ፡ ማድረግ፡ ቅዳሴ ፡ መስማት ፡ ይወዳል ።

ነገር ፡ ግን ፡ የጸሎቱ ፡ መሠረት ፤ በውጭም ፡ በግቢም ፡ ባገሬም ፡ ውስጥ በሰው ፡ አገር፡ ያለውን፡ ሀብቴን ፡ ጠብቅልኝ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የሚለው ፤ ለመለመን ፡ የሚገባውን ፡ ነገር ፡ አያውቅም ።

እሑድ ፡ እሑድና ፡ በያመት ፡ በዓሉ ፡ ባጥቢያው ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ጴጥሮስ ፡ ጳውሎስ ፡ እየሄደ ፡ ተለመዱ ፡ ጸሎቱን ፡ ያደርጋል ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ከቅዱስ ፡ ጊዮርጊስና ፡ መንበረ ፡ ጸባኦት ፡ ቅድስት ፡ ሥላሴ ፡ ቤተ ክርስቲያን ፡ እያስቀደሰ ፡ ጉባኤም ፡ ይሰማል ።

ከዕለታት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ የዕርገትን ፡ በዓል ፡ ለማክበር ፡ ረጂ ፡ መድኃኔ ፡ ዓለም ፡ ሄዶ ፡ ቅዳሴ ፡ አስቀድሶ ጉባኤውን ፡ ለመስማት ፡ ተቀመጠ ፤ እንዳጋጣሚ ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ አለቃ ፡ በሰፊው ፡ የሰውን ፡ ከንቱነት ፡ ከተናገሩ ፡ በኋላ ፡ የያዕቆብ ፡ ሐዋርያውን ፡ መልእክት ፡ ጠቅሰው ፡ ሰው ፡ ሆይ ፡ የራስኽ ፡ ባልሆነ ፡ ቀን ፡ የምትመካ ፡ በእብሪትም ፡ እንደዚህ ፡ የምትል ፡ ዛሬ ፡ ወይም ፡ ነገ ፡ ወደዚያች ፡ አገር ፡ እንሄዳለን ፤ ከዚያም ፡ ዓመት ፡ እናደርጋለን ፤ እንነግድማለን ፡ እናተርፍማለን ።

እላንት ፡ ግብዞች ፡ አታውቁምን ፡ ነገ ፡ የናንተ ፡ ገንዘብ ፡ እንዳይደለች ፣ ሕይወታችን ፡ ምንድናት ፡ እንደ ፡ ጽጋግ ፡ አይደለችምን ጥቂት ፡ ታይታ ፡ የምትጠፋ ፤ አሁንም ፡ ሂዱ ፡ እላንት ፡ ባለጸጎች ፡ አልቅሱ ፡ ዋይም ፡ በሉ ፡ ባለጸግነታችሁ ፡ ጠፍቷልና ፡ ወርቃችሁም ብሬችሁም ፡ ዛገ ፤ ዝገቱም ፡ ምስክር ፡ ይሆንባችኋል ፤ ሥጋችሁንም ፡ ይበላዋል ፤ እንደ ፡ እሳት ፡ እያሉ ፡ አስፋፍተው ፡ ሲያስረዱ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ አቋርጦ ፡ ካጠገቡ ፡ ለተቀመጠው ፡ ጓደኛው ፡ ከገጠር ፡ ቤተ ክርስቲያን ፡ መምጣት ፡ የማልወደው ፡ ስለዚህ ፡ ነው ፤ ይህ ፡ ስብከት ፡ ሰው ፡ ሥራ ፡ እንዳይሠራና ፡ እንዳይከብር ፡ እጁን ፡ ማሰር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ደስ ፡ የሚል ፡ ስብከት ፡ ነውን ፡ ተነሥተን ፡ እንሂድ ፡ አለው ።

ባልጀራው ፡ ወንድሜ ፤ ይህ ፡ ስብከት ፡ እኔን ፡ በጣም ፡ ልቤን ነክቶኛል ፤ ስለዚህ ፡ እንቈይና ፡ እናስጨርስ ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ግን ፡ ይህነን ፡ የስንፍና ፡ ጉባኤ ፡ በመስማት ፡ ጊዜዬን ፡ አላጠፋም ፡ ብሎ ፡ ተቈጣኝ ፡ ተነሥቶ ፡ ሄደ።

## ምዕራፍ ፡ ፱ ።

እንዳጋጣሚ ፡ ሌሊቱኑ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በጠለቀ ፡ እንቅልፍ፤ ተውጠ ፡ ሳለ ፡ በሕልሙ ፡ የሱ ፡ ገንዘብ ፡ የተቀመጠ በት ፡ ትልቅ ፡ ከተማ ፡ በቦምብ ፡ ሲቃጠል ፡ አይቶ ፡ የሱ ፡ ሀብት ፡ ያለበትን ፡ ባንክ ፡ ለማዳን ፡ ሲሮጥ ፡ የልም ፡ ሩጫ ፡ እንደሚሉት አልጠራቀምልኽ ፡ ብሎት ፡ ሲወድቅ ፡ ሲነሣ ፡ በብዙ ፡ ድካም ፡ ከባንኩ ፡ አጠገብ ፡ ሲደርስ ፡ ባንኩ ፡ በእሳተ ፡ ገሞራ ፡ ተያ ይዞ ፡ ሲቃጠል ፡ የብሩና ፡ የወርቁ ፡ እሳት ፡ እንደ ፡ እሳተ ፡ ገሞራ ፡ እየተተፋ ፡ ቀልጦ ፡ የእሳት ፡ ባሕር ፡ ሆኖ ፡ ሲፍለቀለቅ፡ አይቶ ፡ እንግዴህ ፡ ከሀብቴ ፡ ጋራ ፡ አብሬ ፡ እጠፋለሁ ፡ እንጂ ፡ ምን ፡ ኑሮ ፡ አለኝ ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ እራት ፡ ዘሎ ፡ ከሚፍ ለቀለቀው ፡ የወርቅና ፡ የብር ፡ እሳት ፡ ባሕር ፡ ውስጥ ፡ ሲወድቅ በድንጋጤ ፡ ብንን ፡ አለ ።

ወዲያው ፡ ከልጋው ፡ ላይ ፡ ተነሥቶ ፡ ተቀምጦ ፡ እየተንቀጠ ቀጠ ፡ ከረቢ ፡ መድኃኔ ፡ ዓለም ፡ የሰማውን ፡ ስብከት ፡ እያሰበ ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ እንኳን ፡ ሕልም ፡ አደረግክልኽኝ ፡ እያለ ፡ እግ ዚአብሔርን ፡ ካመሰገነ ፡ በኋላ ፡ ልብሱን ፡ ለብሶ ፡ ቍርስ ፡ እን ኳን ፡ ሳያደርግ ፡ ካቅራቢያው ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሄዶ ፡ ጌታዬ አምላኬ ፡ ሆይ ፡ በሕልሜ ፡ እንዳየሁት ፡ ያለ ፡ ጥፋት ፡ በሀብቴና በንብረቴ ላይ ፡ አታድርስብኝ ፡ አንተ ፡ በቸርነትኽ ፡ በግቢም ፡ በው ጭም ፡ ያለውን ፡ ትዳሬን ፡ ሁሉ ፡ ጠብቅብኝ ፡ ብሎ ፡ በጠለቀ ፡ ኀዘን ፡ ጸሎት ፡ ካደረገ ፡ በኋላ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ አጠገብ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ሜትር ፡ ያህል ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ አንድ ፡ የመቃብር ቦታ ፡ ነበር ። ከዚያም ፡ ለመናፈሻ ፡ ከተሠራው ፡ ጠባብ ፡ መንገድ ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ብዙ ፡ ዐይነት ፡ የሚያማምሩ ፡ አበቦች ፡ ተተክለው በታል ፤ ያበቦቹን ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ቀለሞች ፡ በማየትና ፡ በዚያም፡ ውስጥ ፡ በመናፈስ ፡ የነፍስ ፡ ደስታ ፡ ይሰማል ።

ይልቁንም ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ አበቦች ፡ መካከል ፡ የተሠሩ ፡ መቃ ብሮች ፡ ለቦታው ፡ ጌጥ ፡ ሆነው ፡ ይታያሉ ።

ስለዚህ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ አታክልቱንና ፡ ሐውልቱን ፡ በማየት ፡ ሐሳቡ ፡ እንዲከፈልለት ፡ ምርኵዙን ፡ ይዞ ፡ በመንገዱ ፡ ውስጥ ፡ በኀዘንና ፡ በትካዜ ፡ እርምጃ ፡ ቀስ ፡ ብሎ ፡ ይናፈስ ፡ ነበር ።

አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ እየቆመ ፡ በጥበብ ፡ የተሠሩትን ፡ የዕብነ ፡ በረድና ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ድንጋይ ፡ የተቀረጹትን ፡ ሕንፃዎች ፡ በማየት ፡ ይደነቅ ፡ ነበር ።

ይልቁንም ፡ በሐውልቶቹ ፡ ላይ ፡ የተቀረጹትን ፡ የሙታን ፡ ስምና ፡ የተወለዱበትን ፡ ዓመተ ምሕረት ፡ የሞቱበትንም ፡ ቀን ፡ እያነበበ ፡ የሰው ፡ ዘመኑ ፡ ትንሽ ፡ በመሆኑ ፡ በጣም ፡ አዘነ ።

እንደዚሁ ፡ አንድ ፡ ሰዓት ፡ ያኽል ፡ ከሐሳቡ ፡ ጋር ፡ እየተሜወተ ። ኸር ፡ ኸር ፡ ካለ ፡ በኋላ ፡ ትንሽ ፡ ዕረፍት ፡ ለማድረግ ፡ ካንድ ፡ ድንጋይ ፡ ወንበር ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ በበትሩ ፡ መሬቱን ፡ እየቈረቈረ ፡ ዐንገቱን ፡ በእጁ ፡ ደግፎ ፡ በጠለቀ ፡ ኀዘን ፡ ተውጦ ፡ ሲያስብ ፡ ቀና ፤ ብሎ ፡ ወደ ፡ ፊቱ ፡ ቢመለከት ፡ ኃምሳ ፡ ሜትር ፡ ያኽል ፡ ራቅ ፡ ብሎ ፡ አንድ ፡ ያፈር ፡ መቃብር ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ የዕንጨት ፡ መስቀል ፡ ተተክሎበት ፡ በመስቀሉ ፡ ዐናት ፡ በጕልህ ፡ ጽፈት ፡ በጥቍር ፡ ቀለም ፡ ዋጋውን ፡ ያልከፈለ ፡ ሰው ፡ የሚል ፡ ጽሑፍ ፡ አየ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ይህንን ፡ መቃብር ፡ በነዚህ ፡ በጥበብ ፡ ሥራ ፡ በተቀረጹት ፡ ሐውልቶች ፡ መካከል ፡ በማየቱ ፡ በጣም ፡ ገረመው ።

ይልቁንም ፡ በመስቀሉ ፡ ዐናት ፡ የተጻፈውን ፡ የዕዳውን ፡ ደብዳቤ ፡ በማየት ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ምን ፡ ይሆን ፤ እያለ ፡ እጅግ ፡ አዘነ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ይህነኑ ፡ መቃብር ፡ በኀዘን ፡ ሲመለከት ፡ አንድ ፡ መንፈሳዊ ፡ ድኻ ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ የሚባሉ ፡ ጠጕራቸው ፡ አድጎ ፡ ከትከሻቸው ፡ ላይ ፡ የወደቀ ፡ የበግ ፡ ሌጦ ፡ ለብሰው ፡ አንዲት ፡ የዕንጨት ፡ ምርኵዝ ፡ በእጃቸው ፡ ይዘው ፡ ወደሱ ፡ ሲመጡ ፡ አየ ፤ ወዲያው ፡ ካጠገቡ ፡ ደርሰው ፡ ጌታው ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ውለዋል ፡ ብለው ፡ ሰላምታ ፡ ሰጡት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤–አባቴ ፡ ርስዎ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ውለ ዋል ።

መንፈሳዊ ፡ ድኻ ፤–ጌታው ፡ ከዚህ ፡ ከድኾች ፡ ከተማ ፡ ምን ፡ ያደርጋሉ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤–አባቴ ፡ የድኾች ፡ ከተማና ፡ የሀብታ ሞች ፡ ከተማ ፡ ተለይቷልን ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤–እንዴታ ፡ ይህን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ አያ ውቁምን ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤–አላውቅም ፡ እባክዎ ፡ የሀብታ ሞች ፡ ከተማ ፡ ማን ፡ ይባላል ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—የሀብታሞች ፡ ከተማማ ፡ ባንክ ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤-የድኾች ፡ ከተማስ፡ ማን ፡ ይባላል ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤--የድኾች ፡ ከተማ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ናት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤–የከተማው ፡ ገዢ ፡ ማነው ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤–የከተማው ፡ ገዢ ፡ ራሱን ፡ እንኳ ፡ የሚያስገባበት ፡ ጐጆ ፡ የሌለው ፡ ስለኛ ፡ ድኻ ፡ የሆነው ፡ የእ ግዚአብሔር ፡ ልጅ ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤–አባቴ ፡ እንደሚሉት ፡ ቤተ ፡ ክርስ ቲያን ፡ የድኾች ፡ ከተማ ፡ ናት ፡ አንበል ፤ እንሆ ፡ በዙሪያችን ፡ የከበቡን ፡ የሀብታሞች ፡ ሐውልትና ፡ መቃብሮች ፡ ናቸው ፤ ስለ ዚህ ፡ የሚሉኝ ፡ ነገር ፡ ምንም ፡ አይገባኝም ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤-እንግዲያስ ፡ ላስረዳዎ ፡ እነዚህ ፡ ዙሪ ያውን ፡ የከበቡን ፡ ሀብታሞች ፡ አይደሉም ፤ እንሆ ፡ ሀብታቸውን ፡ ሁሉ ፡ ተወርሰው ፡ ከናታቸው ፡ ማሕፀን ፡ ዕራቁታቸውን ፡ እንደ ፡ ወጡ ፡ እንደዚሁም ፡ ዕራቊታቸውን ፡ ድኻ ፡ መናጢ ፡ ሆነው ፡ እንደኔ ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ዜጋ ፡ የሆኑ ፡ ናቸው ፤ በዚህ ፡ መቃብር ፡ ከተማ ፡ ውስጥ ፡ ድኻና ፡ ሀብታም ፡ የለም ። ነገር ፡ ግን ፡ እነዚህ ፡ ገንዘባቸውን ፡ የተወረሱ ፡ ሀብታሞች ፡ ከድኾች ፡ ጥቂት፡ ብልጫ ፡ አላቸው ፤ ምክንያቱም ፡ በዕብነ ፡ በረድ ፡ የተሠራ ፡

በልዩ ፡ ልዩ ፡ ድንጋይ ፡ የተቀረጸ ፡ የመቃብር ፡ ርስት ፡ ስለሚ ኖራቸው ፡ ነው ።

ዳሩ ፡ ግን ፡ ይህ ፡ ለቆሙ ፡ ዘመዶቻቸው ፡ ማባበያ ፡ ማታ ለያ ፡ አሻንጉሊት ፡ ማለት ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ለነሱ ፡ የሚጠቅም ፡ ነገር ፡ አይደለም ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤–አባቴ ፡ በመቃብር ፡ ርስትና ፡ ጨሰኝነት ፡ አለን ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤–አዎን ፡ እንሆ ፡ ድኾች ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ርስተ ፡ ምድር ፡ ስለሌላቸው ፡ ከፊት ፡ ለፊትዎ ፡ የሚያ ዩት ፡ የድኻ ፡ መቃብር ፡ የጨሰኝነት ፡ ቦታ ፡ መሆኑን ፡ ያሳያል ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤–ቅድም ፡ ርስዎ ፡ ሳይመጡ ፡ ይህ ነን ፡ መቃብር ፡ በማየት ፡ ገርሞኝ ፡ ነበር ፤ እባክዎ ፡ አባቴ ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ የተተከለውን ፡ መስቀልና ፡ በመስቀሉ ፡ ዐናት ፡ የተ ጻፈውን ፡ ታሪክ ፡ ይንገሩኝ ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤–በላዩ ፡ የተተከለው ፡ መስቀል ፡ መከ ራውን ፡ ያሳስባል ፤ በመስቀሉም ፡ ዐናት ፡ የተጻፈውን ፡ ቃል ፡ የመቃብሩን ፡ ዋጋ ፡ ስላልከፈለ ፡ ባለርስት ፡ አለመሆኑን ፡ የሚያ መለክት ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤–ይህ ፡ ሰው ፡ ከሞተ ፡ ወዲህ ፡ መቃብሩን ፡ ለቆ ፡ ይሄዳልን ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤–አዎን ፡ እንደሱ ፡ ያለ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ርስት ፡ የሌለው ፡ ድኻ ፡ ሲመጣ ፡ ዐፅሙ ፡ ለቆ ፡ ይሄዳል ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—ወዴት ፡ ነው ፡ ለቆ ፡ የሚሄ ደው ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—ይህ ፡ ድኻ ፡ የመሬቱን ፡ ዋጋ ፡ ስላልከፈለ ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ብቻ ፡ በኪራይ ፡ መቃብር ፡ ተቀ ምጦ ፡ ለባለፈንታ ፡ ይለቃል ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤– ዐፅሙ ፡ ለቆ ፡ ወዴት ፡ ይሄዳል።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—አንድ ፡ የጠለቀ ፡ ጕድጓድ ፡ የድ ኾች ፡ ወንድሞቹ ፡ ዐፅም ፡ መከማቻ ፡ ስላለ ፡ ከዚያ ፡ ይጣላል።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—ወይ ፡ ግሩም ፡ እንግዴህ ፡ ለድኾች ፡ ርስተ ፡ ምድር ፤ ርስተ ፡ ሰማይ ፡ የላቸውም ፤ እጅግ ፡ ያሳዝናል ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—ርስዎ ፡ እንደሚሉት ፡ ርስተ ፡ ምድር፡ ድኾች ፡ እንደሌላቸው ፡ የታወቀ ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የማትሞተው ፡ ነፍሳቸው ፡ ርስተ ፡ ሰማይ ፡ ይቈያታል ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—እኔ ፡ ምንም ፡ ክርስቲያን ፡ ብሆን ፡ ነፍስ ፡ አለች ፡ ለማለት ፡ በጣም ፡ ያስቸግረኛል ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—እኔም ፡ እንደማያምኑ ፡ ዐውቃለሁ፤ ምክንያቱም ፡ ባለጸጎች ፡ ኀጢአትን ፡ ለመሥራት ፡ እንዲመቻችሁ ፡ ዕንቅፋትም ፡ እንዳይሆንባችሁ ፡ እግዚአብሔርንና ፡ ነፍስን፤ ሕግን ፡ ምግባርን ፡ ከመንገዳችሁ ፡ ላይ ፡ አንሥታችሁ ፡ ጥላችኋቸዋል ።

ስለዚህ ፡ በእጅ ፡ ከሚዳሰሰው ፡ ነገር ፡ በቀር ፤ ረቂቅ ፡ የሆኑትን ፡ ነገሮች ፡ አታምኑም ።

ነገር ፡ ግን ፡ ያች ፡ የምታስፈራዋ ፡ ቀን ፡ ድምፃችን ፡ እንደ ወፍ ፡ ድምፅ ፡ የምትሆንባት ፡ ሰዓት ፡ ስትደርስ ፡ ይታሰባል ፤ ምን ፡ ይሆናል ፡ ተመልሶ ፡ ከናት ፡ ማሕፀን ፡ መግባት ፡ አይቻል ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—አባቴ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ እንደዚህ ፡ ያስፈራሩኛል ፤ ባለጸጋ ፡ በቅጣት ፡ እንዲሣቀይ ፤ ድኻ ፡ በሰማያዊ ፡ ኑሮ ፡ ደስ ፡ እንደሚለው ፡ ማነው ፡ ለይቶ ፡ የሚያውቅ ፡ ሁሉስ ፡ በወሬ ፡ አይደለምን ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—ጌታው ፡ ይህ ፡ የማጫውትዎ ፡ ወሬ፡ አይደለም ፡ የድኾች ፡ ከተማ ፡ አስተዳዳሪ ፡ ራሱ ፡ ነዌ ፡ በሚባለው ፡ ሀብታምና ፡ አልዓዛር ፡ በሚባለው ፡ ድኻ ፡ ታሪክ ፡ ነግሮናል ።

ነዌ ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ በሥቃይ ፡ ሳለ ፡ የአልዓዛርን ፡ ነፍስ፡ በሩቁ ፡ አይቶ ፡ ይጠየፈው ፡ የነበረውን ፡ ድኻ ፡ በጣቱ ፡ ውሃ፡ ነክሮ ፡ ምላሱን ፡ እንዲያረጥብለት ፡ መለመኑን ፡ እምነናል ።

ይልቁንም ፡ ሀብታሙ ፡ ነዌ ፡ እንዳረጀ ፡ ልብስ ፡ ከመቃብር ፡ የጣለውን ፡ ሥጋውን ፡ ለብሶ ፡ ይህነን ፡ ሥቃይ ፡ ለዘመዶቹ ፡ ለመናገር ፡ ለምኖ ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ እናንተ ፡ ሀብታሞች ፡ መጻሕፍት ፡ የዓለም ፡ ምግባርና ፡ ፍልስፍና ፡ ያልመከሯችሁን ፡ ሞቶ ፡ የተነሣ ፡ ሰው ፡ ቢነግራችሁም ፡ ስለማታምኑ ፡ አሮጌ ፡ ልብሱን ፡ ሁለተኛ ፡ ለብሶ ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ ወህኒ ፡ ቤት ፡ እንዲመለስ ፡ የድኾች ፡ ከተማ ፡ ንጉሥ ፡ አልፈቀደለትም ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በዚህ ፡ በመነኵሴ ፡ ንግግር ፡ በጣም ፡ ተነካ ፤ ይልቁንም ፡ በሕልሙ ፡ የሚያሳዝን ፡ ሕልም ፡ በማየቱ ፡ ጸሎት ፡ ለማድረግ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ቢመጣ ፡ እኒህን ፡ መንፈሳዊ ፡ መነኵሴ ፡ አጋጥሞት ፡ ዐጥንት ፡ የሚሰብር ፡ መንፈሳዊ ፡ ጨዋታ ፡ በመስማቱ ፡ ተገረመ ።

ነገር ፡ ግን ፡ ከሌሊቱ ፡ አንሥቶ ፡ እስካሁን ፡ እስካለበት ፡ ሰዓት ፡ ድረስ ፡ የኀዘንና ፡ የትካዜ ፡ ቀን ፡ በመሆኑ ፡ አዝኖ ፡ ተክዞ ፡ ከቈየ ፡ በኋላ ፡ አባቴ ፡ እንግዴህ ፡ ቀጠሮ ፡ አለብኝና ፡ ልሂድ ፡ ቅድም ፡ ስለ ፡ ዠመርነው ፡ የነፍስን ፡ መኖርና ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ዕድሏ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለመረዳት ፡ ነገ ፡ ባሥር ፡ ሰዓት ፡ እዚሁ ፡ ስፍራ ፡ ድረስ ፡ እመጣለሁና ፡ እንዲጠብቁኝ ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፤ ነገ ፡ ከእኩለ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ባሥር ፡ ሰዓት ፡ እዚሁ ፡ እጠብቅዎታለሁ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—ደኅና ፤ ይደሩ ፡ አባቴ ።

አባ፡ሰው፡በከንቱ፤—አሜን፤ነገ፡እግዚአብሔር፡በሰላም፡ያገናኘን ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ የድኻው ፡ መቃብር ፡ ትዝ ፡ እያለው ፡ በኀዘን ፡ እርምጃ ፡ ቀስ ፡ ብሎ ፡ ምርኵዙን ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ተጓዘ ። አቶሞቢሉም ፡ በኋላ ፡ በኋላው ፡ ዝግ ፡ ብሎ ፡ ይከተለው ፡ ነበር ፤ ሩብ ፡ ሰዓት ፡ ያኽል ፡ በእግሩ ፡ ሄዶ ፡ ከዋናው ፡ ጐዳና ፡ ሲገባ ፡ አንድ ፡ የትልቅ ፡ ሰው ፡ ሬሳ ፡ በጕዞ ፡ ፍታት ፡ እየተ

ፈታ ፡ ባጌጠ ፡ የወርቅ ፡ ቀለም ፡ በተቀባ ፡ ሠረገላ ፡ ባበባ ፡ ተከቦ ፡ ቤተ ፡ ዘመዶቹና ፡ ባለቤቱ ፡ ሽልማቱንና ፡ ጌጡን ፡ ይዘው ፡ ሲያለቅሱ ፡ ብዙ ፡ መሳፍንትና ፡ መኳንንት ፡ ተከት ለውት ፡ ሲኀዙ ፡ አይቶ ፡ ደነገጠ ፡ ወዲያው ፡ ተጠግቶ ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ቢጠይቅ ፡ አንዱ ፡ የጥቅም ፡ ኀደኛው ፡ የሚያውቀው ፡ ወዳጁ ፡ መሆኑን ፡ ነገሩት ።

እሱም ፡ አልቅሶ ፡ በኦቶሞቢሉ ፡ ተቀመጠና ፡ ሬሳውን ፡ ያጅብ ፡ ዠመር ።

ሬሳውም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ እያረፈ ፡ የጕዞ ፍታት ፡ ከተፈታ ፡ በኋላ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ደረሰ ። መኳንንቱና ፡ መሳፍንቱ ፡ ስመ ፡ ጥሮች ፡ ነጋዴዎችም ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ወልወል ፡ ከፍተኛ ፡ ስፍራ ፡ ላይ ፡ ተቀምጠው ፡ ሲያለቅሱ ፡ ከቈዩ ፡ በኋላ ፡ የመጨረሻው ፡ ፍታት ፡ ሲያልቅ ፡ ሬሳውን ፡ አንሥተው ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ዙሪያ ፡ አዙረው ፡ ወደ ፡ ተዘጋጀው ፡ መቃብር ፡ አገቡት ።

ቄሱ ፡ ከመቃብሩ ፡ ዐፈር ፡ ላይ ፡ ቆመው ፡ ማዕጠንቱን ፡ ካጠኑ ፡ በኋላ ፡ እፍኝ ፡ ዐፈር ፡ ዘግነው ፡ አዳም ፡ ሆይ ፡ መሬት ፡ ነኽና ፡ ወደ ፡ መሬት ፡ ትመለሳለኽ ፡ ብለው ፡ ሲበትኑበት ፡ የመጣው ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ አንዳንድ ፡ እፍኝ ፡ ዐፈር ፡ በተነበት ። ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ዐፈሩንም ፡ ድንጋዩንም ፡ ከቆለሉበት ፡ ወዲያ ፡ የመጡት ፡ አዘነተኞች ፡ መሳፍንትና ፡ መኳንንት ፡ ስመ ፡ ጥሩ ዎች ፡ ነጋዴዎችም ፡ ተመልሰው ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ወልወል ፡ ላይ ፡ ተቀመጡ ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ የሚባሉ ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ አገ ልጋይ ፡ በጣም ፡ የተማሩ ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ትልቅ ፡ ሰው ፡ የመቃብር ፡ በዓል ፡ ጊዜ ፡ ለማሳረግ ፡ ይገባቸዋል ፡ ተብለው ፡ ተመርጠው ፡ መጡ ፡

ከተሰበሰበውም ፡ ሕዝብ ፡ መካከል ፡ ቆመው ፡ እንደዚህ ፡ ብለው ፡ ሰበኩ ፤ ሰው ፡ ሆይ ፡ ትላንት ፡ ትልቅ ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ሀብታም ፡ የነበርክ ፡ ዛሬ ፡ ማነኽ ፡ የተዋረድኽ ፡ ድኻ ፡ ዐፈር ፡ ትቢያ ፡ አይደለኽምን ።

እንሆ ፡ ድኻ ፡ መናጢ ፡ ሆነኽ ፡ ከድኾች ፡ ከተማ ፡ ለመኖር ፡ መጣኽ ፡ ዘመድ ፡ ወዳጅኽ ፡ ሸኝተውኽ ፡ ተመለሱ ።

ከሁሉም ፡ አብልጠኽ ፡ የምትወደው ፡ ወዳጅኽ ፡ እመቃብር ፡ ድረስ ፡ እንኳ ፡ አልሸኘኽም ።

ሚስትኽም ፡ ልጆችኽም ፡ ዘመዶችኽ ፡ ዐፈር ፡ ትቢያ ፡ ስለ ፡ ሆንኽ ፡ ከመቃብርህ ፡ ላይ ፡ እፍኝ ፡ ዐፈር ፡ በትነውብኽ ፡ ጌጥኽንና ፡ ውድ ፡ ዕቃኽን ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ቤትኽ ፡ ሊመለሱ ፡ ነው ።

ሰው ፡ ሆይ ፡ የመኖሪያ ፡ ቤትኽ ፡ ጠባብ ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ የመለወጫ ፡ ልብስ ፡ እንኳ ፡ ይዘኽ ፡ ለመግባት ፡ አትችልም ።

የቤተ ፡ ዘመድና ፡ የወዳጅ ፡ ውካታ ፡ ቀሩ ፤ አንተም ፡ በመቃብር ፡ ጨለማ ፡ ውስጥ ፡ ብቻኽን ፡ ተጣልኽ ።

እንግዲህ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ማነው ፡ የቀረ ፤ ያው ፡ የማትወደው ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ብቻ ፡ ነበር ፡ የሚከተልኽ ፡ አላስጠጋኸውም ።

እንግዲህ ፡ እነዚያ ፡ ሌትና ፡ ቀን ፡ የምታስብላቸው ፡ ሀብቶችኽ ፡ በባንክ ፡ የተቀመጡት ፡ ወርቅና ፡ ብር ፡ እየተፋጩ ፡ እሳት ፡ ሆነው ፡ ሥጋኽን ፡ በመቃብር ፡ ውስጥ ፡ ሊያቃጥሉት ፡ ነው ።

ሰው ፡ ሆይ ፤ የማትሞተው ፡ ነፍስኽ ፡ ሥጋዋን ፡ እንዳረጀ ፡ ልብስ ፡ በመቃብር ፡ ጥላ ፡ ካጠገብህ ፡ በጸጸት ፡ ትቃጠላለች ።

አንተ ፡ ብትሞት ፡ ነፍስኽና ፡ ጸጸት ፡ አይሞቱም ፤ በዓለምና ፡ በደስታ ፡ ምክንያት ፡ ጸጸት ፡ ተዳፍኖ ፡ ቢቀመጥ ፡ እንኳ ፡ ነፍስኽን ፡ ለማቃጠል ፡ ይነሣል ፡ ጸጸት ፡ ያንቀላፋል ፡ እንጂ ፡ አይሞትም ፡ ተብሏል ።

አንተ ፡ ሀብታም ፡ ሰው ፡ በባንክ ፡ ያለውን ፡ የወርቅ ፡ ጥጃ ፡ በማምለክ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የተጣላኽ ፡ ነፍስኽን ፡ ይማራት ፡ ብለው ፡ ሲጨርሱ ፤ ከዚያ ፡ የተሰበሰቡት ፡ ሀብታሞች ፡ በቍጣ ፡ ጥርሳቸውን ፡ ያፋጩ ፡ ጀመር ፤ ርስ ፡ በርሳቸውም ፡ እንዲህ ፡ ብለው ፡ ተማከሩ ።

እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ጥጋበኛ ፡ ድኻ ፡ ዓለሙን ፡ ሁሉ ፡ ሲያዋርድ ፡ ዝም ፡ ማለት ፡ የሚገባ ፡ አይደለምና ፡ አሁኑኑ ፡ ለከንቲባው ፡ አመልክተን ፡ እንዲታሰር ፡ ካልሆነ ፡ ትልልቅ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የማንም ፡ መጫወቻ ፡ መሆኑ ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ከመነኰሴው ፡ ጋራ ፡ የመንፈሳዊ ፡ ንግግር ፡ በመነጋገሩ ፡ ስለ ፡ ወደዳቸው ፡ ለሀብታሞቹ ፡ አይሆንም ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ድኻ ፡ ነገሩን ፡ አቅሎ ፡ መተው ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ መከታተል ፡ አያስፈልግም ፡ እያለ ፡ መከራቸው ።

ሀብታሞቹ ፡ ሁሉ ፤ ምንም ፡ ቢሆን ፡ አንተወውም ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ዐጥንት ፡ የሚሰብር ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ በሁላችንም ፡ ላይ ፡ ተናግሯል ።

ይልቁንም ፡ ይህ ፡ የሞተው ፡ ወንድማችን ፤ ምን ፡ አለው ፡ ሬሳውን ፡ እንደዚህ ፡ አድርጎ ፡ የሚወቅስ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—ክቡራን ፡ ወንድሞቼ ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ በድኽነቱ ፡ ተበሳጭቶ ፡ ይሆናል ፤ ስለዚህ ፡ እኛ ፡ ከድኾች ፡ የበለጠ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ መንፈስ ፡ እንዲኖረን ፡ ያስፈልጋል ፤ ይህነን ፡ የትንሽ ፡ ሰው ፡ ነገር ፡ መቈጣጠር ፡ አይገባንም ።

ሀብታሞቹ ፤—ምንም ፡ ቢሆን ፡ እንደዚህ ፡ አዋርዶን ፡ አንተወውም ፡ ብለው ፡ በቍጣ ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ ሚቱ ፡ ቤት ፡ ተጓዙ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ግን ፡ በሕልሙ ፡ ባየው ፡ ብርቱ ፡ ነገርና ፡ እንዳጋጣሚ ፡ ከመቃብር ፡ አትክልት ፡ ውስጥ ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱን ፡ አገናኝቶት ፡ የተነጋገሩትን ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ከዚያም ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሲመለስ ፡ የጥቅም ፡ ጓደኛው ፡ ሞቶ ፡ ከመንገድ ፡ ያጋጠመውን ፡ የመከራ ፡ ጊዜ ፡ በኅሊናው ፡ ሲያወጣ ፡ ሲያወርድ ፡ ዋለ ።

ይልቁንም ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ በጉባኤው ፡ መካከል ፡ ቆመው ፡ በድፍረት ፡ የሰውን ፡ ከንቱነት ፡ የሰበኩትን ፡ በማሰብ ፡ ሌሊት ፡ ምንም ፡ እንቅልፍ ፡ አልወሰደውም ፡ ነበር ።

ማለዳ ፡ ተነሥቶ ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ ቍርስ ፡ አደረገ ። በሦስት ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ሥራው ፡ ሄዶ ፡ እስከ ፡ ሰባት ፡ ሰዓት ፡ እሥራው ፡ ላይ ፡ ቈይቶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመለሰ ፤ ምሳውን ፡ በልቶ ፡ ከመኝታ ፡ ቤቱ ፡ ትንሽ ፤ ዕረፍት ፡ ካደረገ ፡ በኋላ ፡ በቀጠሮው ፡ አባ ሰው ፡ በከንቱ ፡ ዘንድ ፡ እዚያው ፡ ከመቃብር ፡ አትክልት ፡ ሄደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬ ።

አቶ ፡ ሀብት'ኸ ፡ ይመር ፤—አባቴ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ አደሩ ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤-ጌታው ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ፡ ርስዎ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ አደሩ ።

አቶ ፡ ሀብት'ኸ ፡ ይመር፤—አባቴ ፡ ትላንት ፡ በደረሱብኝ ፡ ነገሮች ፡ ሁሉ ፡ ሌሊቱን ፡ እንቅልፍ ፡ ሳይወስደኝ ፡ ሲገርመኝ ፡ አደርኩ ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—እኔ ፡ ይልቅ ፡ በጣም ፡ የሚገርም ፡ ነገር ፡ ስለ ፡ ገጠመኝ ፡ ብቻዬን ፡ ስሥቅ ፡ ነበር ።

ምክንያቱም ፤ እኔና ፡ ርስዎ ፡ በኑሮም ፡ በሐሳብም ፡ እንደ ፡ ሰማ ይና ፡ እንደ ፡ ምድር ፡ የተራራቅን ፡ ስንሆን ፡ ከድኻች ፡ ከተማ ፡ መጥተው ፡ ሁለታችንንም ፡ ጊዜና ፡ ሥፍራ ፡ ጓደኛ ፡ አድርጎን ፡ የመ ንፈሳዊ ፡ ጨዋታ ፡ ስንለዋወጥ ፡ በመዋላችን ፡ ነው ።

ደግሞ ፡ በጣም ፡ የገረመኝ ፡ ያንኑ ፡ የምንጫወተውን ፡ ሀብታሞች ፡ ሀብታቸውን ፡ ተወርሰው ፡ ዕራቍታቸውን ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ዜጋ ፡ ለመ ሆን ፡ ይመጣሉ ፡ ብዬ ፡ የነገርኩዎትን ፡ ወዲያው ፡ ባይንዎ ፡ ስላዩት ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብት'ኸ ፡ ይመር ፤—ይህ ፡ በጣም ፡ የሚገርም ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ አባቴ ፡ ትላንት ፡ ባደረጉት ፡ ብርቱ ፡ ስብከት ፡ ብዙ ፡ ሀብታ ሞች ፡ አዝነውብዎታል ፡ እኔም ፡ ጊዜ ፡ ያገናኘንን ፡ ወዳጄን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሲያዝንብዎ ፡ በመስማቴ ፡ አዘንኩ ። ቢሆንም ፡ እኔ ፡ ለማንኛ ውም ፡ ነገር ፡ ብርቱ ፡ ጠበቃዎ ፡ ነኝና ፡ አያስቡ ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—ጌታው ፡ አይጨነቁ ፡ ለርስዎም ፡ እግ ዚአብሔር ፡ ያስብልዎ ።

ነገር ፡ ግን ፡ እኛ ፡ ድኾች ፡ ዘወትር ፡ የምንሞተው ፡ በሀብታሞች ፡ እብሪት ፡ ነው ፤ ብሞትም ፡ ከመኖሬ ፡ የተሻለ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አላስብበትም ።

አቶ ፡ ሀብት'ኸ ፤ ይመር ፤—አባቴ ፡ ርስዎስ ፡ ምን ፡ ቸገረዎ ፡ ነበር ፡ እነዚህን ፡ የከበሩ ፡ ሀብታሞች ፡ ባያዋርዱ ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—ጌታው ፡ የድኾች ፡ ከተማ ፡ አስተዳዳሪ፤ ሰው ፡ ሀብቱ ፡ ቢበዛለትና ፡ ነፍሱ ፡ በጌትነት ፡ ደስ ፡ ቢላት ፡ አትፍ ራው ፤ ሰው ፡ መሆኑን ፡ እንዳይረሳ ፡ ምክረው ፡ ብሎናል ።

ስለዚህ ፡ እኛ ፡ የድኾች ፡ ከተማ ፡ ሰዎች ፡ እንደዚሁ ፡ እውነትን ተናግረን ፡ እንሞታለን ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—ይህ ፡ እንግዴህ ፡ አለፈ ፡ ምን ፡ ይደ ረግ ፤ ርስዎ ፡ ግን ፡ አይሥጉ ፡ እኔ ፡ ካለሁልዎ ፡ ምንም ፡ የለብዎ ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—እግዚአብሔር ፡ ይስጥልኝ ፡ እንግዴህ ፡ የተቃጠርንበትን ፡ ጒዳይ ፡ እንጫወት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—ትላንት ፡ የተቃጠርነው ፡ በልሳሳት ፡ ስለ፥ ነፍስ ፡ መኖርና ፡ ወደፊት ፡ ስለሚደርስባት ፡ ዕድል ፡ ነው ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤–ርግጥ ፡ ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—አባቴ ፡ ነፍስ ፡ ማለት ፡ ምንድናት ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤-ነፍስ ፡ ማለት ፡ የዕውቀታችንና ፡ የበጎ ፡ ኀሊናችን ፡ መገኛ ፡ የሕይወታችን ፡ ብርሃን ፡ ምድጃ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ስለዚህ ፡ አራቱ ፡ የሥጋ ፡ ባሕርይ ፡ ከነፍስ ፡ ጋራ ፡ በማ ይለያይ ፡ አንድነት ፡ ተሳስረው ፡ ተዋሕደው ፡ ሰው ፡ ያስኙናል ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—እነዚህን ፡ አራቱን ፡ ባሕርያተ ፡ ሥጋና ፡ ነፍስን ፡ በማይለያይ ፡ አንድነት ፡ የሚያስተሳስራቸው ፡ ማነው ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤–የሥጋንና ፡ የነፍስን ፡ ባሕርይ ፡ አንድ ፡ የሚያደርግና ፡ የሚያስተሳስር ፡ ማዕከላዊ ፡ ደመ ፡ ነፍስ ፡ አለ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ አራቱ ፡ የሥጋ ፡ ባሕርያት እነ ማናቸው ፤

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤-አራቱ ፡ ባሕርያተ ፡ ሥጋ ፡ መሬት ውሃ ፡ ነፋስ ፡ እሳት ፡ ናቸው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—ነፍስና ፡ ሥጋ ፡ እንደዚህ ፡ ተዋሕደው ሲኖሩ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይለያያሉ ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—የሰው ፡ ልጅ ፡ ብዙ ፡ ዘመንም ፡ በመቀመጥ ፡ በሕፃንነትም ፡ ቢሆን ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ በሚያስተኛ ፡ በሽታና ፡ ወይም ፡ በቶሎ ፡ በሚገድል ፡ መቅሠፍት ፡ ሥጋና ፡ ነፍስ ፡ በሞት ፡ ይለያያሉ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በመጨረሻ ፡ ደቂቃ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ ሥቃይና ፡ ጦር ፡ ለሁሉም ፡ አንድ ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር፤—እባክዎ ፡ ይህች ፡ የመጨረሻ ፡ ሰዓት ፡ እንደ ፡ ምንድናት ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—የሰው ፡ ልጅ ፡ ነፍሱ ፡ ከሥጋው ፡ ስትለይ ፡ በነፍስና ፡ በደመ ፡ ነፍስ ፡ መከከል ፡ ያለ ፡ ማሰሪያ ፡ ሲቈረጥ ፡እንዴት ፡ ያለ ፡ ጭንቅ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ አስተያየት ፡እንደ፡ ምን፡ያለ ፡ ድምፅ፡ይሰማ ፡ ይመስልዎታል፤ያንን ፡ ማየትና ፡ መስማት ፡ ሰው ፡ መሆንን ፡ ያስጠላል ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤–ነፍስና ፡ ሥጋ ፡ ከተለያዩ ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይሆናሉ ፤ ደስ ፡ ይላታልን ፡ ወይስ ፡ ታዝናለች ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—ነፍስ ፡ ሥጋዋን ፡ እንዳሮጌ ፡ ልብስ ፡ ከመቃብር ፡ ውስጥ ፡ ከጣለች ፡ በኋላ ፤ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ወህኒ ፡ ቤት ፡ በመውጣቷ ፡ ደስ ፡ ይላታል ።

ነገር ፡ ግን ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ጭጋግ ፡ ጥቂት ፡ በጥቂት ፡ እንደ ፡ ጉም ፡ እየበነነ ፡ ሲጠፋ ፡ አዲስ ፡ ዓለም ፡ አዲስ ፡ ፀሐይ ፡ ታያለች ።

ያን ፡ ጊዜም ፤ ነፍስ ፡ በጣም ፡ ትጨነቃለች ፤ ምክንያቱም ፡ በብርሃኑ ፡ ውስጥ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሳለች ፡ በእጅ ፡ የሚዳሰሱትን ፡ ነገሮች፡ በማሳደድ ፡ ያሳለፈችው ፡ ጊዜ ፡ በማስታወሻው ፡ ውስጥ ፡ ተጽፎ ፡ ስለሚታያት ፡ ነው ።

ይልቁንም ፡ ይህ ፡ አዲስ ፡ ሕይወት ፡ አዲስ ፡ ንብረት ፡ አዲስ ፡ ዓለም ፡ ለርሷ ፡ መሆኑንና ፡ አለመሆኑን ፡ በማመዛዘን ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ አባቴ ፡ ይህ ፡ ታሪክ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያሳዝናል ፡ ይህች ፡ ነፍስ ፡ ዕድሏን ፡ እስክታውቀው ፡ ድረስ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ጭንቅ ፡ አለባት ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤ በጣም ፡ ትልቅ ፡ ጭንቅ ፡ አለባት ፡ ከመ ቃብሯ ፡ ዐፈር ፡ ላይ ፡ ተቀምጣ ፡ ያንን ፡ ያረጀ ፡ ልብሷን ፡ ዘመድና ፡ ወዳጅ ፡ ተሰብስበው ፡ እንዳይሸት ፡ ዐፈር ፡ ድንጋይ ፡ ሲጨምሩበት ፡ በማየትና ፡ የሷም ፡ ዕድሏ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በማሰብ ፡ ትልቅ ፡ ኀዘን ፡ ይወድቅባታል ።

ይልቁንም ፡ ብርሃኑን ፡ በማየት ፡ ትፈራለች ፤ ምክንያቱም ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ከእንቅልፉ ፡ ሲነቃ ፡ ዐይኑም ፡ አእምሮውም ፡ አጣ ርቶ ፡ እንደማያይ ፡ ብዥ ፡ ብዥ ፡ ይልበታል ።

አቶ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ከዚያ ፡ በኋላስ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ትሆናለች ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤ ከዚያ ፡ በኋላማ ፡ የሷም ፡ ዐይን ፡ እየለመደ ፡ ብርሃኑም ፡ እየበዛ ፡ ይሄዳል ። ይህም ፡ ብርሃን ፡ የምልምት ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ዕቃ ፡ መፈለጊያ ፡ የዓለም ፡ ዓይን ፡ የለመደው ፡ አይደለም ፤ ይህ ፡ ብርሃን ፡ ቀለሙ ፡ የማይታወቅ ፡ ብርሃንነቱ ፡ የማይጠገብ ፡ ወደ ፡ አእምሮ ፡ ሠርፀ ፡ የሚገባ ፡ የዕውቀት ፡ ብርሃን ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ አባቴ ፡ ይህ ፡ ብርሃን ፡ ለነፍስ ፡ ምን ፡ ይረዳታል ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤–ይህ ፡ ብርሃን ፡ በዚች ፡ በተጨነቀች ፡ ነፍስ ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ መስኖ ፡ ውሃ ፡ ሲያጥለቀልቃት ፡ መጠራጠር ፡ መፍራት ፡ ከላይዋ ፡ ላይ ፡ ተገፎ ፡ ይወድቃል ።

ነቢዩ ፡ ዳዊትም ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ጭንቅ ፡ ወድቆበት ፡ ብር ሃንኽንና ፡ ጽድቅኽን ፡ ላክልኝ ፡ ብሎ ፡ ጮኋል ።

አቶ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ነፍስ ፡ ይህነን ፡ ብርሃን ፡ ከተቀበ ለች በኋላ ፡ ምን ፡ ስሜት ፡ ይሰማታል ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡–ብርሃኑን ፡ ከለመደችውና ፡ በትክክል ፡ ለማየት ፡ ከቻለች ፡ በኋላ ፤ የእግዚአብሔር ፡ ቤተ ፡ ሰብና ፡ የቅዱስ ፡ ኑሮን ፡ ተካፋይ ፡ የመድኃኒታችን ፡ ወዳጅ ፡ መሆኗን ፡ ታረጋግጣለች ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤— ነፍስ ፡ ይህነን ፡ ካረጋገጠች ፡ በኋላ ፡ ከመቃብር ፡ ዐፈሯ ፡ ትቈያለችን ፡ ወይስ ፡ ቶሎ ፡ ትሄዳለች ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—የሚቀበሏት ፡ ሰዎች ፡ እስኪመጡ ፡ ትቈያለች ፡

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—ያስ ፡ በመቃብር ፡ የጣለችው ፡ ሥጋ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይሆናል ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤ ጌታው ፡ የእሳት ፡ ባሕርይም ፡ ይቀዘቅዛል ፡ የነፋስም ፡ ባሕርይ ፡ ይበተናል ፤ የውሃም ፡ ባሕርይ ፡ ደምና ፡ እዥ ፡ ሆኖ ፡ ያልቃል ፡ ዐፈርም ፡ ወዳፈርነቱ ፡ ይመለሳል ።

ምዕራፍ ፡ ፳ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—ይህነን ፡ የሚያሳዝን ፡ የሰውን ፡ ተፈጥሮ ፡ ትተን ፡ ወደነፍስ ፡ እንመለስና ፡ ነፍስ ፡ የሚቀበሏት ፡ ሰዎች ፡ ይመጡላታልን ፡ ወይስ ፡ እሷ ፡ ዐውቃ ፡ ትሄዳለችን ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—ሊወስዷት ፡ ይመጣሉ ፡ እንጂ ፤ እሷ ፡ ዐውቃ ፡ አትሄድም ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—እነማናቸው ፡ መጥተው ፡ የሚወስዷት ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—ስለ ፡ ጽድቅና ፡ ስለእውነት ፡ የሞቱ ፡ ሰማዕታት ፡ ስለ ፡ ድኾች ፡ ከተማ ፡ አስተዳዳሪ ፡ ሲሉ ፡ ሁሉን ፡ ትተው ፡ የመነኑ ፡ እንደሎጥ ፡ ሚስት ፡ የተውትን ፡ ዓለም ፡ ዘወር ፡ ብለው ፡ ሳያዩ ፡ እንደ ፡ ጕድፍ ፡ የቈጠሩ ።

በዚህም ፡ ዓለም ፡ ተቀምጠው ፡ ድኾች ፡ ወንድሞቻቸውን ፡ ያልተጸየፉ ፡ ገንዘባቸው ፡ ባልሆነው ፡ ገንዘብ ፡ ወዳጅ ፡ የገዙ ፤ በባንክ ፡ ያለውን ፡ የወርቅ ፡ ጥጃ ፡ ያላመለኩ ፤ ሥሥትንና ራስ ፡ መውደድን ፡ እንደ ፡ ብርቱ ፡ ኀጢአት ፡ ስለቈጠሩት ፡ ማኅበራዊ ፡ ኑሮ ፡ ከወንድሞቻቸው ፡ ተካፍለው ፡ የሚኖሩ ፡ ቅዱሳንና ፡ መላእክትም ፡ ተቀላቅለው ፡ የምሥራች ፡ ዘንባባ ፡ ይዘው ፡ ይመጣሉ ፡

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ዓይታቸው ፡ የማታውቀውን ፡ ቅዱሳንና ፡ መላእክት ፡ ሲመጡባት ፡ አትፈራምን ።

አባ ፡ ስው ፡ በከንቱ ፤ አትፈራም ፤ ስለምን ፡ ቅድም ፡ እንደ ፡ ነገርኩዎ ፡ ነፍስ ፡ ሥጋዋን ፡ እንዳሮጌ ፡ ጨርቅ ፤ በመቃብር ፡ ጥላ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ወህኒ ፡ ቤት ፡ እንዳመለጠች ፡ የእግዚአብሔር ፡ ቤተ ሰብ ፡ መሆኗን ፡ ብርሃኑ ፡ ስለ ፡ ገለጠላት ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—እባክዎ ፡ ከሚቀበሏት ፡ ሰዎች ፡ ውስጥ ፡ የምታውቃቸው ፡ ሰዎች ታገኛለችን ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤ ሁሉንም ፡ ታውቃቸዋለች ። ስለ ፡ ምን ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሳለች ፡ መጻሕፍትን ፡ በማንበብ ፡ ታሪካቸውን ፡ በመ መልከት ፡ አስቀድማ ፡ የመንፈሳዊ ፡ ማኅበረተኛ ፡ ስለነበረች ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—አባቴ ፡ ይህች ፡ ነፍስ ፡ መዠመሪያ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ወህኒ ፡ ቤት ፡ አምልጣ ፡ ከመቃብር ፡ ዐፈር ፡ ላይ ፡ ተቀምጣ ፡ ለምን ፡ አዘነች ፤ ለምንስ ፡ ተጠራጠረች ፤ ለዚህ ፡ ክብር ፡ የሚበቃ ፡ ሥራ ፡ መሥራቷን ፡ አታውቅምን ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—ጌታው ፡ መልካም ፡ ጥያቄ ፡ ጠየቁኝ ፡ ጻድቅት ፡ ነፍስ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሳለች ፡ ምግባር ፡ ትሩፋት ፡ መሥራ ቷን ፡ አታውቅም ፤ ዘወትር፡ በዠሮዋ ፡ የሚሰማት፡ የድኾች ፡ ከተማ ፡ አስተዳዳሪ ፡ ሥራን ፡ ሁሉ ፡ በፈጸማችሁ ፡ ጊዜ ፡ እኛ ፡ ሥራ ፡ ፈት ፡ ባሮች ፡ ነን ፡ በሉ ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ ማሰብ ፡ ነው ።

እንደዚህ ፡ ያለች ፡ ነፍስ ፡ እኔ ፡ በምግባር ፡ አልጸድቅም ፡ በእ ግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ በማለቷ ፡ ሥራዋን ፡ ሁሉ ፡ ከሱ ፡ ቸርነት ፡ በታች ፡ ጥላዋለችና ፡ ምንም ፡ ምግባር ፡ እንዳልሠ ራች ፡ ስለ ፡ ቈጠረችው ፡ ነው ።

ነገር ፡ ግን ፡ ቅድም ፡ እንደ ፡ ነገርኩዎ ፡ ያ ፡ የጽድቅ ፡ ብርሃን ፡ ሥራዋንና ፡ ዋጋዋን ፡ በገለጠላት ፡ ጊዜ ፡ እውነቱን ፡ ታውቀዋለች ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡—በጣም ፡ የሚገርም ፡ ነው ። ርስዎን፡ ያገናኘኝን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግንኩ ፡ አባቴ ፡ ይህ ፡ ብርሃን ፡ የቅዱሳንን ፡ ዋጋ ፡ ብቻ ፡ ነውን ፡ የሚገልጥ ፡ ወይስ ፡ ክፉ ፡ የሠሩት ንም ፡ ኀጢአት ፡ እንደዚሁ ፡ ይገለጣል ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤-ጌታው ፡ ስለዚህ ፡ ጥያቄዎ ፡ በጣም ፡ አመስግኘዎታለሁ ፡ ምክንያቱም ፡ ጊዜያችንን ፡ ከማጥፋት ፡ ንግግራችንን ፡ ስላሳጠሩልኝ ፡ ነው ።

የኔ፡ ሐሳብ፡ በጎ፡ የሠራችውን፡ ነፍስ፡ ታሪክ፡ ስንጨርስ፤ እንደዚሁ ፡ በረዥሙ ፡ ክፉ፡ የሠራችውን፡ ነፍስ፡ ታሪክ፡ ላጫውትዎ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤-እባክዎ ፡ አባቴ ፡ ባጭሩ ፡ ማስረጃ ፡ የማያጠግብ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በዝርዝር ፡ በረዥሙ ፡ ያጫውቱኝ ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—ጌታው ፡ የዘር ፡ ብዛት ፡ ብዙ ፡ ምርት ፡ አይሰጥም ፡ ብዙ ፡ መከር ፡ የሚገኘው ፡ ከመሬቱ ፡ ባሕርይና ፡ ከገበሬው ፡ ባለሟያነት ፡ ነው ። ለፍሬ ፡ እስካሁን ፡ የተነጋገርነው ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ አሁንም ፡ የቀረንን ፡ ታሪክ ፡ ባጭሩ ፡ በጠቅላላው ፡ በተገለጠ ፡ አኳኋን ፡ ባጫውትዎ ፡ ይበቃዎታል ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ እሺ ፡ ያጫውቱኝ ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤-ጌታው ፡ በመዠመሪያ ፡ እንዳጫወትኩዎ ፡ ነፍስ ፡ የለበሰችውን ፡ ሥጋ ፡ እንዳሮጌ ፡ ጨርቅ ፡ በመቃብር ፡ ውስጥ ፡ ጥላ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ወህኒ ፡ ቤት ፡ በወጣች ፡ ጊዜ ፡ እንግዳ ፡ ነገር ፡ በማየት ፡ መደንገጥና ፡ መፍራት ፡ ለበጎም ፡ ነፍስ ፡ አንድ ፡ ነው ።

ነገር ፡ ግን ፡ ክፉ ፡ ነፍስ ፡ አዲስ ፡ ዓለምና ፡ የጽድቅ ፡ ብርሃን ፡ በማየቷ ፡ በጣም ፡ ትጨነቃለች ፡ ዐይኑ ፡ የታመመ ፡ ሰው ፡ ብርሃንን ፡ ትኩር ፡ ብሎ ፡ ለማየት ፡ እንደማይችል ፡ ክፉ ፡ ነፍስም ፡ የእግዚአብሔርን ፡ የጽድቅ ፡ ብርሃን ፡ ለማየት ፡ ትልቅ ፡ ሥቃይ ፡ ትልቅ ፡ ጭንቅ ፡ ይሆንበታል ።

ዳሩ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ብርሃኑ ፡ ላይኗ ፡ የማይስማማት ፡ ቢሆን ፡ በብርሃኑ ፡ ውጋጋን ፡ ውስጥ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሳለች ፡ የሠራቻቸው ፡ ክፉዎች ፡ ሥራዎች ፡ ሁሉ ፡ ከመዠመሪያ ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ሰዓቷ ፡ ተገልጠው ፡ ይታዩዋታል ።

ይልቁንም ፡ በጣም ፡ የሚያሳዝነው ፡ ዕድል ፡ ፈንታዋ ፡ በጥቍር ፡ ገበታ ፡ ላይ ፡ ስሟ ፡ ጭምር ፡ ተጽፎ ፡ ስለሚታያት ፡ ማፈሯ ፡ ነው ፤ ከስሟ ፡ በታችም ፡ ያለፉት ፡ መካን ፡ የሆኑት ፡ ቀኖች ፡ ሰዓቱም ፡ ደቂቃውም ፡ ሰከንዱም ፡ ሳይቀር ፡ በከንቱ ፡ ነገር ፡ ያሳለፈችው ፡ ዕዳዋ ፡ መሆን ፡ ያሳስባታል ።

እግዚአብሔር ፡ ወንድሞቻችንን ፡ ልንጠቅምበት ፡ የሰጠንን ፡ ቀን ፡ ያለፍሬ ፡ ስላስቀረች ፡ ዕዳዋን ፡ የምትከፍልበት ፡ ሰሌዳ ፡ ይቀርብላታል ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—እንደ ፡ ምን ፡ የሚያሳዝን ፡ ነገር ፡ ነው ፡ ይህች ፡ ነፍስ ፡ እንደዚሁ ፡ ብርሃን ፡ ማየት ፡ እንደ ፡ ፈራች ፡ ትቀራለችን ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—ጌታው ፡ ብርሃኑ ፡ ኃጢአቷን ፡ ለመግለጥ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከሷ ፡ ጋራ ፡ ለመኖር ፡ ስላይደለ ፡ ወዲያው ፡ ይጠፋል ።

ነፍስም ፡ በቀቢጸ ፡ ተስፋ ፡ በውድቅት ፡ ጨለማ ፡ ውስጥ ፡ ሆና ፡ እስከ ፡ የሌለውን ፡ የቅጣት ፡ ፍርድ ፡ በድንጋጤና ፡ በፍርሃት ፡ ትጠባበቃለች ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—ምን ፡ ዐጥንት ፡ የሚሰብር ፡ ታሪክ ፤ ነው ፤ እባክዎ ፡ በዚች ፡ በጭንቅ ፡ ሰዓት ፡ ውስጥ ፡ ምን ፡ ታስብ ፡ ይሆን ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ይህች ፡ ችጋረኛ ፡ ነፍስ ፡ ከመቃብሯ ፡ ዐፈር ፡ ላይ ፡ ተቀምጣ ፡ በእጅዋ ፡ አገጯን ፡ ይዛ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ የሚመጣባት ፡ ነገር ፡ የሚያስደነግጥ ፡ ልብን ፡ የሚሠነጥቅ ፡ መሆኑን ፡ ስለ ፡ ተረዳችው ፡ ዐይኗን ፡ አፍጣ ፡ በፍርሃት ፡ ትጠባበቃለች ።

ይልቁንም ፡ በሰሌዳ ፡ የተጻፈውን ፡ በከንቱ ፡ የባከነውን ፡ ጊዜ ፡ በማሰብ ፡ ጸጸት ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ያቃጥላታል ።

አቶ ፡ ሀብትህ ፡ ይመር ፤—እባክዎ ፡ አባቴ ፡ ይህች ፡ የተጨነቀች ፡ ነፍስ ፡ ወዴት ፡ ብትሸሽ ፡ ይሻላት ፡ ይሆን ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤—እባክዎ ፡ አያስቁኝ ፡ ምን ፡ መሸሻ ፡ አለ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሌለበት ፡ አገር ፡ ከወዴት ፡ ይገኛል ። ነገር ፡ ግን ፡ ርስዎም ፡ እንደሚሉት ፡ ያች ፡ ችጋረኛ ፡ ነፍስ ፡ ወደ ፡ መቃብሯ ፡ እየዞረች ፡ ያንን ፡ የጣለችውን ፡ አሮጌ ፡ ጨርቅ ፡ ደግሞ ፡ ለብሳ ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ ለመመለስም ፡ ታስብ ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ አውልቀው ፡ ከጣሉት ፡ ወዲህ ፡ ብል ፡ እንደበላው ፡ ልብስ ፡ ተበጫጭቆ ፡ ስለሚወድቅ ፤ ሁለተኛ ፡ የማይለበስ ፡ በመሆኑ ፡ ታዝናለች ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤—አባቴ ፡ እንግዴህ ፡ ይህች ፡ ነፍስ ፡ ምን ፡ ይሻላታል ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፤ ጌታው ፡ ምን ፡ የሚሻል ፡ ነገር ፡ አለ፤ ሰው ፡ ወደፊቱ ፡ ያርሳል ፡ እንጂ ፤ ወደኋላው ፡ አያርስም ። እንግዲህ ፡ ይህች ፡ ነፍስ ፡ የዘራችውን ፡ ልታጭድ ፡ እፍረትን ፡ ለብሳ ፡ እነዚያን ፡ በማየት ፡ የሚያስጨንቁ ፡ ተቀባዮቿን ፡ በኀዘንና ፡ በጭንቅ ትጠባበቃለች ።

እንግዴህ ፡ ጌታው ፤ ይህ ፡ በድኾች ፡ ከተማ ፡ የሚነገር ፡ ታሪክ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሬት ፡ የመረረና ፡ የማይጣፍጥ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ይብቃን፤ ነገር ፡ ግን ፡ በኋላ ፡ ከማር ፡ የጣፈጠ ፡ ሳይሆን ፡ አይቀርም ።

ጌታው ፤ ጊዜው ፡ ስለ ፡ መሸ ፡ እኔም ፡ የሠርክ ፡ ጸሎት ፡ አለብኝና ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ልሂድ ፤ ርስዎም ፡ ወደ ፡ ቤትዎ ፡ ይሂዱ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ አባቴ ፡ ጊዜዎን ፡ አጥፍተው ፡ እንደ ዚህ ፡ ያለ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ የቁም ፡ ነገር ፡ ታሪክ ፡ ስላጫወቱኝ ፡ በጣም ፡አመሰግንዎታለሁ ፤ እንግዴህ ፡ እኔም ፡ ልሂድ ፡ ደኅና ፡ ይደሩ።

አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱም ፤ ጌታው ፡ ደኅና ፡ ይደሩ ፡ ይህነን ፡ የተጫወትነውን ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ አይርሱት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ እስከ ፡ መቼም ፡ የምረሳው ፡ ነገር ፡ አይደለም ፡ ብሎ ፡ እያዘነና ፡ እየተከዘ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ።

## ምዕራፍ ፡ ፮ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ጥቂት ፡ ቀን ፡ ይህነን ፡ በማሰብ ፡ ማንኛውም ፡ ደስታ ፡ የከንቱ ፡ ከንቱ ፡ መሆኑ ፡ ስለሚታሰበው ፡ ፊቱ ጠቍሮ ፡ የኀዘን ፡ መልክ ፡ ይታይበት ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ባገሩም ፡ በብዙም ፡ የውጭ ፡ አገሮች ፡ ላይ ፡ በንግድና ፡ በኤኮኖሚ ፡ በእንዱስትሪ ፡ ጕዳይ ፡ የተተበተበ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ወዲያው ፡ የጥቅም ፡ አሳቦች ፡ ልቡን ፡ ሲይዙት ፡ ከፍ ፡ ያለው ፡ የዕውቀት ፡ አሳቡ ፡ በሸዋ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ጽሑፍ ፡ ተደመሰሰ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱን ፡ ባገኛቸው ፡ በምስተኛው ፡ ቀን ፡ ፌዲራል ፡ የሚባለው ፡ የስዊስ ፡ ባንክ ፡ ዲሬክተር ፡ ባንክ ፡ እንግላንድ ፡ የሚባለው ፡ የእንግሊዝ ፡ ባንክ ፡

ዲሬክተር ፡ ባንክ ፡ ደፍራንስ ፡ የሚባለው ፡ የፈረንሳዊ ፡ ባንክ ፡ ዲሬክተር ፡ ካቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ጋራ ፡ በጥቅም ፡ ስለ ፡ ተያያዙበት ፡ የሥራ ፡ ጕዳይ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ መጡ ፡ የሱ ፡ እንግዶች ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ አይሮፕላን ፡ ማረፊያ ፡ ሄዶ ፡ ተቀበለና ፡ ከራስ ፡ ሆቴል ፡ አስገባቸው ።

በማግስቱ ፡ ከሱው ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ ንግድና ፡ ስለ ፡ ኤኮኖሚ ፡ ስለ ፡ እንዱስትሪ ፡ ጕዳይ ፡ ስብሰባ ፡ ተደረገ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ከተነጋገሩ ፡ በኋላ ፡ ማታውኑ ፡ የሁለት ፡ ሰዓት ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ስለነሱ ፡ ክብር ፡ ግብዣ ፡ ስላደረገ ፡ መሰፍንቱ ፡ መኳንንቱ ፡ ሚኒስትሮች ፡ ዲሬክተሮች ፡ የየሥራው ፡ ክፍል ፡ ሹማምቶች ፡ ያገር ፡ ባላባቶች ፡ ተጠርተው ፡ ትልቅ ፡ በዓል ፡ ሷሬ ፡ (የማታ) ፡ ዳንስ ፡ ተደረገ ።

በማግቱ ፡ ጧት ፡ በምስት ፡ ሰዓት ፡ ሁለተኛ ፡ ካቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ቤት ፡ ተሰብስበው ፡ የዠመሩትን ፡ የሥራ ፡ ጕዳይ፡ ጨርሰው ፤ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ውስጥ ፡ ባሉት ፡ ነጋዴዎችና ፡ በራሱም ፡ ስም ፡ ሆኖ ፡ ስለ ፡ ንግድና ፡ ስለ ፡ እንዱስትሪ ፡ ስለ ፡ ኤኮኖሚ ፡ ጕዳይ ፡ ሲዋስ ፡ ሎንዶን ፡ ፓሪስ ፡ ኒዮርክ ፡ እንዲሄድ ፡ ተቈረጠ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ካባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ ተሰናብቶ ፡ እንደ ፡ ተለያዩ ፡ እነዚያ ፡ ሀብታሞች ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱን ፡ በሰበኩት ፡ ስብከት ፡ ምክንያት ፡ ለከንቲባው ፡ የክስ ፡ ራፖር ፡ ስላቀረቡ ፡ በፖሊስ ፡ ተይዘው ፡ ዓለም ፡ በቃኝ ፡ ከሚባለው ፡ ወህኒ ፡ ቤት ፡ ታሰሩ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ላባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ አይዞዎ ፡ እኔ ፡ ሁሉንም ፡ ነገር ፡ አበርድልዎታለሁ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ አይሥጉ ፡ ብሏቸው ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ እሳቸው ፡ የሰጣቸውን ፡ ተስፋ ፡ ለማስታወስ ፡ በግጥም ፡ አድርገው ፡ አንድ ፡ ብጣሽ ፡ ወረቀት ጽፈው ፡ ላኩለት ፡ ቃሉም ፡ እንደዚህ ፡ ነው ።

ዓለም ፡ በቃኝ ፡ ብዬ ፡ ሄድኩኝ ፡ ወደ ፡ ሞት ፤
ቃልኽን ፡ አትርሳ ፡ እንዳይጐድል ፡ እምነት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ይህች ፡ በብጣሽ ፡ ወረቀት

የተጻፈች ፡ ቃል ፡ በደረሰችው ፡ ጊዜ ፡ ከገንዘብ ፡ ማስቀመጫ ፡ ኰረጆ ፡ ውስጥ ፡ ጨምሮ ፡ የመንንዱን ፡ ጉዳይ ፡ ያዘጋጅ ፡ ዠመር ፤ በሦስተኛውም ፡ ቀን ፡ ኀሙስ ፡ ጧት ፡ ከባንክ ፡ ዲሬክተሮች ፡ ጋራ ፡ ባይሮፕላን ፡ ወደ ፡ ስዊስ ፡ አገር ፡ ሄደ ። ከዚያም ፡ ጄኔብ ፡ ከተማ ፡ ሆቴል ፡ ደሩሲ ፡ ከሚባለው ፡ ገባ ፡ ብዙ ፡ ሁብታሞችም ፡ የጥቅም ፡ ጓደኞቹ ፡ እየመጡ ፡ ተገናኙት ።

ማታውኑ ፡ ከዚያው ፡ ካለበት ፡ ሆቴል ፡ የእራት ፡ ግብዣ ፡ አድርገውለት ፡ በማግስቱ ፡ ማለዳ ፡ ከዋናው ፡ ከተማ ፡ ቢርን ፡ ከሚባለው ፡ በምድር ፡ ባቡር ፡ ሄደ ፤ ብዙ ፡ ካፒታሊስቶች ፡ የጥቅም ፡ ጓደኞቹ ፡ እላጋር ፡ ድረስ ፡ ሄደው ፡ ተቀበሉት ፡ በፍጥነት ፡ ስብሰባ ፡ አድርገው ፡ ስለ ፡ ጥቅምና ፡ ስለ ፡ ኤኮኖሚ ፡ ጉዳይ ፡ ከተነጋገሩ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ጄኔብ ፡ ተመለሰ ። አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ገንዘብኽ ፡ ወዳለበት ፡ ልብኽ ፡ ከዚያው ፡ ይሆናል ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ዘወትር ፡ አሳቡ ፡ ስዊስ ፡ አገር ፡ ለመኖር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አንዲት ፡ ቤት ፡ ለመግዛት ፡ አሳብ ፡ ነበረው ፤ ስለዚህ ፡ ከስዊስ ፡ አገር ፡ ውስጥ ፡ ሞንትሬ ፡ ከሚባ ለው ፡ ወይም ፡ ዙሪክ ፡ ውስጥ ፡ ለመግዛት ፡ አስቦ ፡ ነበርና ፡ ቅዳሜና ፡ እሑድ ፡ ሥራ ፡ ስለሌለበት ፡ መዠመሪያ ፡ ሞንትሬ ፡ ሄዶ ፡ ስለ ፡ ቤት ፡ ግዥ ፡ ተጠያይቆ ፡ ማታውኑ ፡ ወደ ፡ ዙሪክ ፡ ሄደ ፤ ከብዙ ፡ ሰዎችም ፡ ጋራ ፡ ቤት ፡ ለመግዛት ፡ ንግግር ፡ አድርጎ ፡ ከዚያው ፡ አደረ ።

በማግስቱ ፡ ማለዳ ፡ ካቅራቢያው ፡ አንድ ፡ ጥንታዊ ፡ ያሮጌ ፡ ገዳም ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ስለነበረ ፡ ገብቶ ፡ ጸሎት ፡ አደረገ ።

ከዚያ ፡ በኋላ ፡ የቀድሞ ፡ ጊዜ ፡ በጣም ፡ አሮጌ ፡ የነበረ ፡ ጋለሪ ፡ ስላየ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ እየተመላለሰ ፡ ከተመለ ከተ በኋላ ፡ ሊማን ፡ ወደሚባል ፡ ቦታ ፡ ሄደ ፤ ከዚያም ፡ ዱሮ ፡ በፌዎዳል ፡ ጊዜ የሰቧይ ፡ የነበረ ፡ ግንብ ፡ በሐይቅ ፡ ዳር ፡ ተሠርቶ በማየቱ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለውና ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ከባሕሩ ፡ ዳር ፡ ተቀምጦ ፡ ገንዘቡን ፡ ሁሉ ፡ ከዚሁ ፡ አገር ፡ ባንክ ፡ አኑሮ ፡ ከዚሁ ፡ የተቀመጠ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ዕድለኛ ፡ ነው ፡ እያለ ፡ ተመኘ ።

ወዲያው ፡ በአቶሞቢል ፡ ራቅ ፡ ብሎ ፡ ለመናፈስ ፡ ሄደ ፡ ከአ ቶሞቢል ፡ ወርዶ ፡ በእግሩ ፡ ሲናፈስ ፡ ድንገት ፡ አንዲት ፡ በጣም ፡ የምታምር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አየ ፡ ደስ ፡ ስላለችው ፡ ተጠግቶ ፡



ሲመለከት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያኒቱን ፡ ሬፎርም ፡ ያደረገውን ፡ ዝቬንግሊ ፡ የሚባለውን ፡ ሰውዬ ፡ ሐውልት ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ቆሞ ፡ አየ ። ከሐ ውልቱ ፡ አጠገብ ፡ ተጠግቶ ፡ ሲመለከት ፡ ሰውዬው ፡ የተወለደበ ትን ፡ ቀንና ፡ የሞተበትን ፡ ዘመን ፡ አንብቦ ፡ ሰው ፡ ከቤቱና ፡ ከሐ

ውልቱ ፡ ያነሰ ፡ እከ ፡ ነው ፤ የሠራው ፡ ሥራ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ሲቀመጥ ፡ ሠሪው ፡ በጥቂት ፡ ዘመን ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ይጠፋል ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ እንደ ፡ ነገሩኝ ፡ ከማትሞተው ፡ ነፍስ ፡ በቀር ፡ ከመቃብር ፡ እንዳሮጌ ፡ ልብስ ፡ የምንጥለው ፡ ሥጋችን ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ እያለ ፡ በጠለቀ ፡ ኀዘንና ፡ በትካዜ ፡ ወደ ፡ ሆቴሉ ፡ ተመለሰ ።

ከእኩለ ፡ ቀንም ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ጀኔብ ፡ በአቶሞቢሉ ፡ ተመልሶ ፡ ከባለጥቅሞቹ ፡ ጋራ ፡ ጕዳዩን ፡ ከጨረሰ ፡ በኋላ ፡ ማታውኑ ፡ ወደ ፡ ፓሪስ ፡ ባይሮፕላን ፡ ሄዶ ፡ ቡርጀ ፡ ከሚባለው ፡ አይሮፕላን ፡ ማረፊያ ፡ ወዳጆቹና ፡ የጥቅም ፡ ጓደኞቹ ፡ ተቀበሉትና ፡ ሆቴል ፡ ክሬዮ ፡ ገባ ።

በማግስቱ ፡ ትልቅ ፡ ስብሰባ ፡ ተደርጎ ፡ ስለ ፡ ንግድና ፡ ስለ ፡ ኤኮኖሚ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ጕዳይ ፡ ከተነጋገሩ ፡ በኋላ ፡ ጓደኞቹ ፡ ብዙ ፡ ሀብታሞች ፡ ሮችልዶች ፡ የመንግሥትም ፡ ሠራተኞች ፡ ጨምረው ፡ አምባሳደር ፡ ከሚባለው ፡ ሬስቶራ ፡ ከማታው ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ ግብዣ ፡ አደረጉለት ።

ያም ፡ አምባሳደር ፡ የሚባለው ፡ ቲያትርም ፡ ዳንስም ፡ ምግብም ፡ የሚደረግበት ፡ ሞዲሪን ፡ የሆነ ፡ ሬስቶራ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ በደስታ ፡ አሳለፈው ።

በሁለተኛው ፡ ቀን ፡ ማለዳ ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ ኖትርዳም ፡ ከምትባለው ፡ ከእመቤታችን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሄደ ፤ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ የዱሮ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ስለሚወድ ፡ ኖትርዳም ፡ ስቲል ፡ ጎቲክ ፡ በሚባለው ፡ ቅርጽ ፡ በመሠራቷ ፡ ደስ ፡ እያለው ፡ ፓሪስ ፡ በመጣ ፡ ቍጥር ፡ ከእመቤታችን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሳይደርስ ፡ አይቀርም ፡ ነበር ።

ከዚያ ፡ ሲወጣ ፡ የመድኃኒታችንን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሳክሬከር ፡ የሚባለውን ፡ ለመሳም ፡ ወደ ፡ ሞማርት ፡ ሄደ ።

ይህ ፡ ሳክሬከር ፡ የሚባለው ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ከተራራ ፡ ጫፍ ፡ በመሠራቱ ፡ ከሱ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ ፓሪስ ፡ በሙሉ ፡ ስለሚታይ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ተደስቶ ፡ ሩብ ፡ ሰዓት ፡ የሚያኽል ፡ በደረጃው ፡ ላይ ፡ ቆመና ፡ ከተመለከተ ፡ በኋላ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፡ የተለመደ ፡ ጸሎቱን ፡ አድርጎ ፡ ወጣ ።

ሆቴል ፡ ክሬዎ ፡ ተመልሶ ፡ ምሳውን ፡ ከተጋበዘ ፡ በኋላ ፡ ከመኝታ ፡ ቤቱ ፡ ገብቶ ፡ ትንሽ ፡ ዕረፍት ፡ አደረገና ፡ ከእኩለ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ፲፩ ፡ ሰዓት ፡ በእግሩ ፡ በሻንዚሊዚ ፡ ጕዳና ፡ እስከ ፡

አርክ ፡ ዳትርዮንፍ ፡ ድረስ ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ በቪትር ፡ ውስጥ ፡ የሚታዩትን ፡ ዕቃዎች ፡ በማየት ፡ እየተጓዘ ፡ ሳይደክመው ፡ ደረሰ ።



ኦፔራ ፡

ፕላስ፡ ዴላኮንኮርድ

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አንድ ፡ አቶሞቢል ፡ ይዞ ፡ በትሮ ፡ ካዲሮ ፡ በኩል፡ አድርጎ ፡ ቱርኤፌልን ፡ አይቶ ፡ ፓዳሌክሳንድሬ ፡ በሚባለው ፡ ድልድይ፡ አቋርጦ ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ከሬዎ ፡ ተመለሰ ።

ማታውኑ ፤ የጥቅም፡ጓደኞቹ ፡ ጋብዘውት ፡ በ፪ ሰዓት ፡ ኦፔራ፡ ሂዶ ፡ ታይስ ፡ የሚባለውን ፡ ቲያትር ፡ በማየት ፡ አመሸ ።




አቶ ፡ ሀብትኽ፡ ይመር ፡ ክላሲክ ፡ የሆነውን ፡ ሙዚቃና ፡ የአርቲስ ቶችን ፡ ጨዋታ ፡ በማየቱ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ አለው ።

ይልቁንም ፡ ብዙ ፡ ደስታና ፡ ዓለም ፡ በሚደረግበት ፡ በፓ ሪስ ፡ ከተማ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ መንፈሳዊ ፡ ቲያትር ፡ በመታየቱ፡ ተገረመ ።

ባራተኛው ፡ ቀን ፡ ሎንዶን ፡ በምድር ፡ ባቡር ፡ ከእኩለ ፡ ቀን በኋላ ፡ ሄደ ።

ቢክቶርያ ፡ ስታሽን ፡ ከሚባለው ፡ ላጋር ፡ የጥቅም ፡ ጓደኞቹ፡ መጥተው ፡ ተቀበሉትና ፡ ሳባይ ከሚባለው ሆቴል ፡ ገባ ።

በማግስቱ ፡ ትልቅ ፡ ስብሰባ ፡ ተደርጎ ፡ ከፍ ፡ ላለ ፡ ጥቅም፡ ጉዳይ ፡ ከተነጋገሩ ፡ በኋላ ፡ ማታ ፡ ፪ ፡ ሰዓት ፡ ግሮብነር ፡ ሐውስ ፡ ከሚባለው ፡ ሆቴል ፡ ትልቅ ፡ ግብዣ ፡ አደረጉለት ።

በማግስቱም ፡ ጧት ፡ ከቅዱስ ፡ ጳውሎስ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን፡ ገብቶ ፡ ጸሎት ፡ አደረገ ።

ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ዊስት ፡ ሚኒስቴር ፡ አቢ ፡ ከምትባለው ፡ ቤተ፡ ክርስቲያን ፡ ሄዶ ፡ ጐብኝቶ ፡ ወዲያው ፡ ፒኪጋሐም ፡ ፖሊስ ፡ በሚባለው ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ቆሞ ፡ የክብር ፡ ዘበኞች ፡ ሲለዋወጡ ፡ የሚደረገውን ፡ ሰልፍ ፡ በማየት ፡ ደስ ፡ ብሎት፡ወደ ሳባይ ፡ ሆቴል ፡ በፒካደሊ ፡ ሰርኩስ ፡ በኩል ፡ በእ ግሩ ፡ ቀስ ፡ ብሎ ፡ በቪትር ፡ ያለውን ፡ ዕቃ ፡ እያየ ፡ ሄደ ።

ማታ ፡ ከራት ፡ በፊት ፡ ትራፋልጋር ፡ አደባባይ ፡ ድረስ ፡ በእ ግሩ ፡ ሄዶ ፡ የኒልሶን ፡ ኩለምን ፡ መታሰቢያ ፡ ቆሞ ፡ ሲመለከት፡ ከቆየ ፡ በኋላ ፡ በ፱ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ሆቴል ፡ ሳባይ ፡ ተመለሰ።

በማግሥቱ ፡ ማለዳ ፡ ወደ ፡ አክስፎርድ ፡ ሄዶ ፡ ዩንቬርሲ ቲውን ፡ ጐብኝቶ ፡ ወዲያው ፡ የክርስቶስን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ለማየት ፡ ገብቶ ፡ የኀሊና ፡ ጸሎት ፡ አድርጎ ፡ ወጣ ።

አክስፎርድን ፡ ጐብኝቶ ፡ ወደ ፡ ሎንዶን ፡ ሲመለስ ፡ አድሚ ራሊቲ ፡ አርክ ፡ የሚባለውን ፡ ቅስት ፡ አይቶት ፡ አያውቅም ፡ ነበ ርና ፡ በዚያ ፡ በኩል ፡ አልፎ ፡ ከአቶሞቢሉ ፡ ወርዶ ፡ እየተመለ ከተ ፡ በጣም ፡ ከተደነቀ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሆቴሉ ፡ ተመለሰ ።

ከእኩለ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ታዎር ፡ አፍ ፡ ሎንዶን ፡ የተባለውን ከፍተኛ ፡ ሥፍራ ፡ ጐበኘ ።



ቅዱስ ጳውሎስ



የታወር ድልድይ

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ባንድ ፡ ታክሲ ፡ ሆኖ ፡ ፓርላማውን ፡ በውጭ ፡ አይቶ ፡ በዚያው ፡ በኩል ፡ ታዎር ፡ በርድጅ ፡ የሚባለውን ፡ ድል

ድይ ፣ ከጐበኘ ፣ በኋላ ፣ ከወንዙ ፣ ዳር ፣ ከዕንጨት፣ ወንበር ፣ ላይ፣ ተቀምጦ ፣ ስለ ፣ ገንዘቡና ፣ ስለ ፣ ሀብቱ ፣ አገሩ ፣ ሳለ ፣ ስላየው ፣ ሕልም ፣ እያስታወሰ ፣ በጣም ፣ ተጨነቀ ፤ በምን ፣ ምክንያት ፣



ዌስትሚኒስቴር ፡ አቢ



የአድሚራሊቲ ፡ ቅሥት

ይሆን ፣ እንደዚህ ፣ ያለ ፣ ሕልም ፣ የደረሰብኝ ፣ እያለ ፣ ጥልቅ ፣ ኀዘን ፣ ካዘነ ፣ በኋላ ፣ ወደ ፣ ሆቴሉ ፣ ተመለሰ ።

ሎንዶን ፡ ሦስት ፡ ቀን ፡ ከዋለ ፡ በኋላ፡በማለዳ ፡ ባይሮፕላን፡ ኒዮርክ ፡ ሄደ ።




ሌሊቱኑ ፡ ከዋናው ፡ ከተማ ፡ ደርሶ ፡ ብዙ ፡ የሥራ ፡ ጓደኞቹና ፡ የጥቅም ፡ ተካፋዮቹ ፡ ተቀበሉትና ፡ አልዶፍ ፡ አስቶሪያ ፡ ከሚባለው ፡ ሆቴል ፡ ገባ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ አሜሪካንን ፡ መዠመሪያ ፡ ማየቱ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሥራ ፡ ከመዠመር ፡ በፊት ፡ መታሰቢያ ፡ የሆኑትን ፡ ነገሮች ፡ ሁሉ እንዲያይ ፡ ተቈረጠ ።

መዠመሪያ ፡ ሰማይ ፡ ጠቀስ ፡ የሆነውን ፡ ኤምፓየር ፡ የሚባለውን ፡ ባለብዙ ፡ ደርብ ፡ አየ ።

ሁለተኛ ፡ ሊቢርቴ ፡ የምትባለውን ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ አንደኛ ፡ የሆነችውን ፡ የነፃነት ፡ ሐውልት ፡ አየ ።

ሦስተኛ ፡ ትልልቆችን ፡ ዩኒቨርስቲና ፡ ሆስፒታሎችን ፡ አየ። አራተኛ ፡ ብዙዎች ፡ አሮጌ ፡ ዕቃዎች ፡ የሚገኙበትን ፡ ሙዜና ፡ የጥበብ ፡ ሥራ ፡ ሥዕል ፡ የሚታይበትን ፡ ጋለሬ ፡ አየ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በማለዳ ፡ በፈጣን ፡ ባቡር ፡ ወደ ፡ ዋሽንግቶን ሄዶ ፡ ከዚያም ፡ ዋሽንግቶን ፡ ከሚባል ፡ ሆቴል ፡ ጥቂት ፡ ዐረፈ ።

ከእኩል ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ዋሽንግቶንን ፡ እየዞረ ፡ ጐበኘ ፤ ከነዚህ ፡ ውስጥ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ ያለው ።

አንደኛ ፡ የስመ ፡ ጥሩው ፡ የአብርሃም ፡ ሊንከል ፡ ሐውልትና ፡ የዋሽንግቶን ፡ መታሰቢያ ነው ።

ሁለተኛ ፡ ኒዮርክን ፡ በትልቅነቱና ፡ በስፋቱ ፡ በቤቶቹ ፡ ርዝመት ፡ ቢገረም ፡ እንኳ ፡ በዋሽንግቶን ከተማ ፡ በስቲልና ፡ በሚያምሩ ፡ ቅርጾች ፡ የተሠሩ ፡ ቤቶችና ፡ መንገዶች ፡ አታክልቶች ፡ በማየቱ ፡ በጣም ፡ ተደነቀ ።

እነዚህም ፡ ቤቶች ፡ ከብዙ ፡ በጥቂቱ ፡ ነጭ ፡ ቤት ፡ የተባለው ፡ የፕሬዚዴንቶች ፡ መኖሪያና ፡ የውጭ ፡ ጉዳይ ፡ ሚኒስቴር ፡ የጦር ፡ ሚኒስቴር ፡ ሌሎችም ፡ ብዙ ፡ የሚያምሩ ፡ ቤቶች ፡ ናቸው ።

ይልቁንም ፡ የከተማው ፡ ጽዳትና ፡ የቤቱ ፡ ንጣት ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ ያሰኝ ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ አሜሪካንን ፡ ለማየት ፡ የተቈረጠለት ፡ ጊዜ ፡ አጭር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሳያድር ፡ ከእኩለ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ባ፲፪ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ኒዮርክ ፡ ተመለሰ ።

ማታውኑ ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ የጥቅም ፡ ጓደኞቹ ፡ ግብዣ ፡ አድርገውለት ፤

ራዲዮን ፡ ሲቲ ፡ ከሚባለው ፡ ቲያትርና ፡ ሲኒማ ፤ እሚታዩ በት ፤ ሄዶ ፡ አመሸ ።




የዚህ ፡ ቲያትር ፡ ቤት ፡ ትልቅነትና ፡ የሕዝቡ ፡ ብዛት ፡ በጣም ፡ አስደነቀው ።

በማግሥቱ ፡ ማለዳ ፡ ባ፩ ፡ ሰዓት ፡ ባይሮፕላን ፡ በሮ ፡ ሺካጎ ፡ ዐርፎ ፤ ሁለት ፡ ሰዓት ፡ ያኽል ፡ ከተማውን ፡ እየዞረ ፡ ካየ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሳንፍራንሲስኮ ፡ ባይሮፕላን ፡ በረረ ።




ከዚያም ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ተቀብለውት ፡ ሆቴል ፡ ፍራንሲስ ፡ ከሚባለው ፡ ገባ ።

ሳንፍራንሲስኮም ፡ በጣም ፡ የተዋበች ፡ ከተማ ፡ ስለ ፡ ሆነች፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ጥቂቶች ፡ ቀኖች ፡ ቢቀመጥ ፡ ወዶ ፡ ነበር፡

ነገር ፡ ግን ፡ ሥራው ፡ ለመቈየት ፡ ጊዜ ፡ የማይሰጠው ፡ ስለ ሆነ ፡ ወደ ፡ ኒዮርክ ፡ ከመመለሱ ፡ በፊት ፡ ከተማውን ፡ እየዞረ፡ ያይ ፡ ዠመር ።

ይልቁንም ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ መዠመሪያ ፡ የሆኑትን ፡ ትልልቅ ፡ ድልድዮችና ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ የተሠሩትን ፡ የሚያምሩ ፡ ቤቶች፡ በማየት ፡ መጠን ፡ የሌለው ፡ ደስታ ፡ ተሰማው ።

ከፋፍ ፡ ላይ ፡ ሆነው ፡ ከተማውን ፡ ሲመለከቱት ፡ ከዓለም፡ ከተሞች ፡ የተለየ ፡ ውበት ፡ ይታይበት ፡ ነበር ።

የከተማውን ፡ ጽዳት ፡ በሮፓ ፡ ውስጥ ፡ ካሉት ፡ ትልል ቆች ፡ ከተሞች ፡ ለማመዛዘን ፡ አይቻልም ።

በየትንንሾች ፡ ቤቶች ፡ ግንባር ፡ የተተከሉት ፡ አበቦች ፡ በጉል ህነታቸውና ፡ በቀለማቸው ፡ ማማር ፡ በመዐዛቸውም ፡ ከሌላው ፡ ዓለም ፡ የተለዩ ፡ ነበሩ ።

ይልቁንም ፤ አቶ ፡ ሀብት'ኽ ፡ ይመር ፡ የካሊፉርኒ ፡ አየር ፡ እንደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ያለ ፡ በመሆኑ ፡ አየሩ ፡ ስለ ፡ ተስማማው ፡ ከዚያ ፡ ለመ ኖር ፡ ይመኝ ፡ ነበር ።

ካሊፉርኒ ፡ በጣም ፡ ሀብታም ፡ አገር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከከተማ ፡ ወጥቶ ፡ ሲናፈሱ ፡ በመንገዱ ፡ ግራ ፡ ቀኝ ፡ የኰኰና ፡ የፖም ፡ የጥ ዋር ፡ ዛፎች ፡ በሚያስገርም ፡ አኳኋን ፡ ይታዩ ፡ ነበር ።

ከዚያም ፡ ጋራ ፡ የቀንድ ፡ ከብቶችና ፡ በጎች ፤ አሣሞች ፡ ዶሮ ችና ፡ ዝዮች ፡ በሜዳ ፡ ፈሰው ፡ ሲታዩ ፡ ያገሩን ፡ ሀብት ፡ ይገልጣሉ ።

አልፎ ፡ አልፎ ፡ በየመንደሩ ፡ የቤንዚን ፡ ማጣሪያ ፡ መኪናዎች ፡ ሲጨሱ ፡ በማየት ፡ ያገሩ ፡ ሀብት ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ይገመት ፡ ነበር ።

ከሳንፍራንሲስኮ ፡ ስምንት ፡ መቶ ፡ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ያኽል ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ ዮሲሚቲ ፡ በሚባል ፡ የደን ፡ ቦታ ፡ ለመናፈስ ፡ ሂዶ ፡ በብዙ ፡ ሺህ ፡ ዘመን ፡ የሚቈጠሩ ፡ ዛፎች ፡ በማየት ፡ ተገረመ ።

እነዚህም ፡ ዛፎች ፡ በቁመት ፡ በውፍረትም ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ ካሉት ፡ ዛፎች ፡ የሚበልጡ ፡ ነበሩ ፡ ዕድሜያቸውም ፡ ፫ ፡ ፬ ፡ ሺሕ ፡ ዓመት ፡ ይገመታል ።

ከዮሲሚቲ ፡ ራቅ ፡ ብሎ ፡ ሰኳያ ፡ የሚባል ፡ ፓርክ ፡ ናሲዮና ልን ፡ ለመጐብኘት ፡ ሄዶ ፡ አንዱን ፡ ወፍራም ፡ ዛፍ ፡ ግንዱን ፡ እንደ ፡ ዋሻ ፡ ፈልፍለውት ፡ በውስጡ ፡ በአቶሞቢል ፡ በማለፉ ፡ አቶ ፡ ሀብ ትኽ ፡ ይመር ፡ በጣም ፡ ተደነቀ ።

ይልቁንም ፡ ዛፎች ፡ ይህን ፡ ያኽል ፡ ሲኖሩ ፡ ሰው ፡ በጥቂት ፡ ዘመን ፡ መታሰቢያው ፡ ሲጠፋ ፡ በጣም ፡ ያሳዝናል ፡ በማለት ፡ ተከዘ ። ዮሲሚቲ ፡ ፓርክ ፡ ናሲዮናል ፡ ከሚባለው ፡ ሥፍራ ፡ በደኑ ፡ ውስ ጥም ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ ሆቴል ፡ ተሠርቶ ፡ ነበር ።

የዚህ ፡ ሆቴል ፡ አሠራር ፡ በጣም ፡ አስደነቀው ፡ ምክንያቱም ፡ የግንቡ ፡ አገነባብና የዕንጨቱ ፡ አቋቋም ፡ ከየው ፡ ሥራ ፡ ሁሉ ፡ ልዩ ፡ ነበር ። ቅርጹ ፡ እስቲሉ ፡ ሩስቲክ ፡ በሚባለው ፡ በጥበብ ፡ ሥራ ፡ የተ ሠራ ፡ ነው ፤ የተሠራበትም ፡ ሸለቆ ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ ፏፏቴ ፡ ከሚ ወርድበት ፡ አጠገብ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ከበቀሉ ፡ ትልልቆች ፡ የጥድ ፡ ዛፎች ፡ ጋራ ፡ ሲታይ ፡ በውነት ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ የተሰጠ ፡ ደስታ ፡ አይመስልም ።

ይልቁንም ፡ ከተራራውና ፡ ከመሬቱ ፡ ልዩ ፡ ቀለም ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ከፈይ ፡ ምንጣፍ ፡ ሣሩ ፡ አረንጓዴ ፡ ሆኖ ፡ በሜዳው ፡ ሲታይ ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ አበቦቹ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ቀለም ፡ አጊጠው ፡ አልፎ ፡ አልፎ ፡ ሲታዩ ፡ በመካከሉ ፡ የሚፈሰው ፡ ወንዝ ፡ በሹክሹክታ ፡ ድምፅ ፡ ሲሰጥ ፡ የቦታው ፡ መልክ ፡ ከመሬቱ ፡ ልዩነት ፡ ጋራ ፡ የፀሐይ ፡ ውጋ ጋን ፡ ሲገባበት ፡ በውነት ፡ ሌላ ፡ ብርሃን ፤ ሌላ ፡ መልክ ፡ ሌላ ፡ ደስታ ፡ ይታይበት ነበር ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ ስለ ፡ ቅድስት ፡ ነፍስ ፡ ያጫወቱት ፡ ትዝ ፡ ብሎት ፡ አዘነ ፡ በልቡም ፡ ለሚሞት ፡ ሥጋ ፡ ይህን ፡ ያኽል ፡ ደስ ፡ የሚል ፡ ነገር ፡ ሲሰጥ ፡ በው ነት ፡ አባ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ እንዳሉት ፡ እንደሆን ፡ ለማትሞተው ፡ ነፍ ስማ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ደስታ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ቦታ ፡ ይሰጣት ፡ ይሆን ፡ በማለት ፡ ነው ።

ምዕራፍ ፡ ፳ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ምንም ፡ ከልክ ፡ ያለፈ ፡ ደስታ ፡ ደስ ፡ ቢለው ፡ ወደ ፡ ሥራው ፡ በቶሎ ፡ ለመመለስ ፡ ግዴታ ፡ ስለ ፡ ሆነበት ፡ ከደኑ ፡ ውስጥ ፡ ካለው ፡ ሆቴል ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ እንኳ ፡ ሳያድር፡ ወደ ፡ ሳንፍራንሲስኮ ፡ ተመለሰ ።

ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ማለዳ፡ ባንድ ፡ ሰዓት ፡ ባይሮፕላን ፡ አልውድ ፡ የሚባለውን ፡ የአርቲስቶች ፡ ቦታ ለማየት ፡ ሄደ ፤ ጊዜ ፡ ስለሌለው ፡ ወዲያው ፡ ካይሮፕላን ፡ እንደ ፡ ወረደ ፡ ሲኒማ ፡ የሚደራጅበትን ፡ ቦታ፡ ለማየት ፡ ሄዶ ፤ ከዚያም ፡ ብዙ ፡ አርቲስቶችና ፡ በጥበብ ፡ የተሠሩትን፡ ቦታዎች ፡ በማየት ፡ ተደነቀ ።

የከተማውን ፡ ጽዳትና ፡ የሕዝቡን ፡ መደርጀት ፡ በማየት ፡ ገረ መው ። ከእኩለ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ኒዮርክ ፡ በረረ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ኒዮርክ ፡ እንደ ፡ ደረሰ ፡ የእንግሊዝ ፡ መንግሥት ፡ ደቫሉያሲዮን ፡ ማድረጉን ፡ ሰማ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በእስተርሊን ፡ ብዙ ፡ ንግድና ፡ ብዙ ፡ ሥራ ፡ ብዙ ፡ የተቀመጠም ፡ ገንዘብ ፡ ስላለው ፡ በጣም ፡ አዘነ ።

ይልቁንም ፡ ካይሮና ፡ ፍልስጥኤም ፡ ከይሁዲ ፡ ነጋዴዎችና ፡ ከግ ብፅ ፡ ፓሻዎች ፡ ጋራ ፡ የተያያዘ ፡ የእስተርሊን ፡ ጥቅም ፡ ስላለው ፡ ከካይሮ ፡ የሚያሳዝን ፡ ቴሌግራም ፡ ደረሰው ፤ ስለዚህ ፡ በቶሎ ፡ ካይ ሮና ፡ ፍልስጥኤም ፡ ሄዶ ፡ ስለ ፡ እስተርሊን ፡ ጉዳይ ፡ ከጥቅም ፡ ጓደ ኞቹ ፡ ጋራ ፡ መነጋገር ፡ ግዴታ ፡ ሆነበት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ነገ ፡ ጧት ፡ በሚሄደው ፡ አይሮፕላን ፡ ከይሮ ፡ ሄዶ ፡ ወዲያው ፡ ፍልስጥኤም ፡ ደርሶ ፡ ወደ ፡ ኒዮርክ ፡ ለመ መለስ ፡ ቈረጠ ።

ማለዳ ፡ በ፲፪ ፡ ሰዓት ፡ ከኒዮርክ ፡ ባይሮፕላን ፡ በሮ ፡ በሁለት ፡ ቀን ፡ ካይሮ ፡ ገባ ።

ከዚያም ፡ ብዙ ፡ ነጋዴዎችና ፡ ፓሻዎች ፡ ተቀበሉትና ፡ ሚኒ ፡ ሐውስ ፡ ከሚባል ፡ ሆቴል ፡ ገባ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ሥራ ፡ ከመዠመሩ ፡ በፊት ፡ ከእኩለ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ካይሮን ፡ እየዞረ ፡ ጐበኘ ፤ ሲታዴል ፡ ከሚባለው ፡ ሥፍራ ፡ ወጥቶ ፡ ካይሮን ፡ በሙሉ ፡ አይቶ ፡ በያመቱ ፡ ከተማው ፡ ስለ ፡ ሚጨምርና ፡ ስለሚያድግ ፡ በጣም ፡ ገረመው ።

ከእኩለ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ከሆቴሉ ፡ አጠገብ ፡ ፕራሚድናስ ፡ ፊንክስ ፡ የቀድሞ ፡ ፈርዖኖች ፡ መታሰቢያዎች ፡ ስላሉ ፡ በእግሩ ፡ ቀስ ፡ ብሎ ፡ እየተናፈሰ ፡ ዙሪያውን ፡ ዞሮ ፡ ከተመለከተ ፡ በኋላ ፡ ማታ ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ ለራቱ ፡ ከሆቴሉ ፡ ተመለሰ ።

በማግሥቱ ፡ ስለ ፡ እስተርሊን ፡ መውደቅ ፡ ትልቅ ፡ ስብሰባ ፡ ከጋሻዎችና ፡ ከትልልቆች ፡ ነጋዴዎች ፡ ጋራ ፡ ተደረገ ።

ስብሰባውም ፡ ከሦስት ፡ ሰዓት ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ ሰባት ፡ ሰዓት ፡ ቈየ ፤ ጕዳዩ ፡ ብርቱ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለነገ ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ ቀጠሮ ፡ ተደርጎ ፡ ተለያዩ ።

ማታውኑ ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ የጥቅም ፡ ጓደኞቹና ፡ ጋሻዎች ፡ ከመሐመድ ፡ ዐሊ ፡ ክለብ ፡ ግብዣ ፡ አደረጉለት ።

በማግሥቱ ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ ጉባኤው ፡ ተዠመረ ። እንደ ፡ ትላንትናው ፡ ሰባት ፡ ሰዓት ፡ ድረስ ፡ ቈይተው ፡ ተለያዩ ፤ ደግሞ ፡ ከእኩለ ፡ ቀን ፡ በኋላ ። እንደዚሁ ፡ ስብሰባ ፡ አድርገው ፡ እስከ ፡ ምሽቱ ፡ ሁለት ፡ ሰዓት ፡ ድረስ ፡ ጕዳያቸውን ፡ ጨረሱ ።

ማለዳ ፡ ባሥራ ፡ ሁለት ፡ ሰዓት ፡ አልማዛ ፡ ከሚባለው ፡ አይሮፕላን ፡ ማረፊያ ፡ በምስር ፡ አይሮፕላን ፡ ወደ ፡ ፍልስጥኤም ፡ በሮ ፡ ልዳ ፡ ላይ ፡ ዐረፈ ።

ከዚያም ፡ የጥቅም ፡ ጓደኞቹ ፡ ብዙዎች ፡ ይሁዲዎች ፡ ዐረቦችም ፡ መጥተው ፡ ተቀበሉትና ፡ ሆቴል ፡ ዒድን ፡ ገባ ።

ከእኩለ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ባሥር ፡ ሰዓት ፡ ቅድስት ፡ አገርን ፡ ለመጐብኘት ፡ ስላሰበ ፡ መዠመሪያ ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፡ ሄዶ ፡ መድኃኒታችን ፡ የተወለደበትን ፡ ቦታ ፡ ተሳልሞ ፡ ጸሎት ፡ ካደረገ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ጎልጎታ ፡ ሄዶ ፡ ከጌታችን ፡ መቃብር ፡ ተንበርክኮ ፡ ስለ ፡ ጥቅሙና ፡ ስለ ፡ ገንዘቡ ፡ ጸሎት ፡ አድርጎ ፡ ወደ ፡ ቀራንዮ ፡ ወጥቶ ፡ ሰገደ ።

ወዲያው ፡ የግሪኮችን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንና ፡ የካቶሊኮችን ፡ ቤተ፡ ክርስቲያን ፡ ከጐበኘ ፡ በኋላ ፡ ዴር ፡ ሡልጣን ፡ የተባለውን ፡ የኢት ዮጵያን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያንና ፡ መነኮሳት ፡ ጐበኘ ።




አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ያገሮቹን ፡ መነኮሳት ፡ በማየቱ ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱን ፡ አስቦ ፡ ዕንባው ፡ አቀረረ ።

አምሳ ፡ ፓውንድ ፡ ላገሩ ፡ መነከሳት ፡ ርዳታ ፡ ሰጠና ፡ ወደ ፡ ጌቴ ሴማኒ ፡ ወርዶ ፡ ከእመቤታችን ፡ መቃብር ፡ ውስጥ ፡ ተንበርክኮ ፡ ጸሎት ፡ አደረገ ።

ከዚያ ፡ ወጥቶ ፡ ዐፀደ ፡ ሐምል ፡ ከሚባለው ፡ መድኃኒታችን ፡ የደም ፡ ወዝ ፡ እስኪ ፡ ወዛ ፡ ድረስ ፡ የጸለየበትን ፡ በማየቱ ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ የድኾች፡ ከተማ ፡ አስተዳዳሪ ፡ በበረት ፡ የተወለ ደው ፡ ራሱን ፡ የሚያስገባበት ፡ ጐጆ ፡ እንኳ ፡ የሌለው ፡ አምላክ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ የነገሩትን ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፤ ዐፀደ ፡ ሐምልን ፡ በማ የቱ ፡ ትዝ ፡ ብሎት ፡ እንባው ፡ ፈሰሰ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ያገሩ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ለመ ጐብኘት ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ገነት ፡ ወጣ ፤ ብዙዎች ፡ ያገሩ ፡ መነከሳት ፡ ወንድም ፡ ሴትም ፡ በማየቱ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ አምሳ ፡ ፓውንድ ፡ ሰጥቶ ፡ ባገሩ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ዐይነት ፡ የተሠራችውን ፡ ሕንፃ ፡ ገብቶ ፡ ከየና ፡ ጸሎት ፡ ካደረገ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሆቴሉ ፡ ተመለሰ ።

በማግሥቱ ፡ ማለዳ ፡ ወደ ፡ ቴል ፡ አቢብ ፡ ሄዶ ፡ ከባለጥቅሞቹ ፡ ይሁዳዎች ፡ ጋራ ፡ ጉባኤ ፡ አድርጎ ፡ ምሳውን ፡ ከዚያው ፡ ተጋብዞ ፡ ወደ ፡ ሐይፋ ፡ ሄዶ ፤ ከዚያም ፡ ኤልያስ ፡ የነበረበትን ፡ የቀርሜሎ ስን ፡ ዋሻ ፡ ጐብኝቶ ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ታቦር ፡ ወጣ ። ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ናዝሬት ፡ ደርሶ ፡ መድኃኒታችን ፡ ብዙ ፡ ተአምራት ፡ ያደረገበትን ፡ የጥብርያዶስን ፡ ባሕር ፡ ካየ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተመለሰ ። ማታውኑ ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ ተክል ፡ ከንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ሆቴል ፡ አይሁድ ፡ ግብዣ ፡ ስላደረጉለት ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ አመሸ ።

ብዙዎች ፡ የመንግሥት ፡ ሠራተኞች ፡ ሀብታሞች ፡ ተጠርተው ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ እስቲነጋ ፡ ድረስ ፡ ዳንስ ፡ ተደርጎ ፡ ከሌሊቱ ፡ በዘጠኝ ፡ ሰዓት ፡ ወደ ፡ ሆቴሉ ፡ ተመለሰ ።

በማግስቱ ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ ቍርሱን ፡ አድርጎ ፡ ወደ ፡ ኢያሪኮ ፡ ወረደ ፡ የኤልሳዕን ፡ ምንጭ ፡ አይቶ ፡ አንድ ፡ ብርጭቆ ፡ ውሃ ፡ ጠጥቶ ፡ ወደ ፡ ገዳመ ፡ ቆሮንቶስ ፡ ወጣ ፤ ከዚያው ፡ የግሪኮችን ፡ ገዳምና ፡ ቤተ ፡ ክርስ ቲያን አይቶ ፡ በጣም ፡ አደነቀ ። ወዲያው ፡ ከተራራው ፡ ጫፍ ፡ ወጥቶ ፡ የዓለም ፡ መድኃኒት ፡ የተፈተነበትን ፡ በማየት ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ኀዘን ፡ አዝኖ ፡ ትንሽ ፡ ጸሎት ፡ አድርጎ ፡ ከተራራው ፡ ጫፍ ፡ ወረደ ።

ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ሄደና ፡ ጠበል ፡ ተነክሮ ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ገዳም ፡ ገብቶ ፡ ያገሮቹን ፡ ልጆች ፡ ጐበኘ ፡ የዮርዳኖስምን ፡ ገዳም ፡ በማየት ፡ ልቡ ፡ በኀዘን ፡ ተነካ ።




ምክንያቱም ፡ በበረሓ ፡ የወደቁትን ፡ መነኰሳት ፡ ሲያይ ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱን ፡ ስለ ፡ መሰሉት ፡ ነው ።

ይልቁንም ፡ በዮርዳኖስ ፡ በረሓ ፡ በሞቱ ፡ መነኮሳት ፡ መቃብር ፡ ላይ ፡ የዕንጨት ፡ መስቀል ፡ ተተክሎ ፡ በማየቱ ፡ ታብ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ ጋራ ፡ የተነጋገራቸው ፡ ቁም ነገሮች ትዝ ስላሉት ፡ ነው ።

ብዙ ፡ ጊዜ ፡ አዝኖ ፡ ከቈየ ፡ በኋላ ፡ ሠላሳ ፡ ፓውንድ ፡ ለመነኮሳቱ ፡ ሰጥቶ ፡ ጸሎት ፡ አድርገውለት ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ወጣ ።



ምዕራፍ ፡ ፳ ።

በማግሥቱ ፡ ማልዳ ፡ ተነሥቶ ፡ ወደ ፡ ካይሮ ፡ ባይሮፕላን ፡ በረረ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በካይሮና ፡ በፍልስጥኤም ፡ ያለውን ፡ ጕዳይ ፡ ከጨረሰ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ አሜሪካን ፡ አገር ፡

ባይሮፕላን ፡ በረረ ። ከካይሮ ፡ ተነሥቶ ፡ ትሪፖሊ ፡ ዐረፈ ። ከትሪፖሊ ፡ ተነሥቶ ፡ ከዛ ፡ ፕላንካ ፡ ከሚባለው ፡ ከተማ ፡ አደረ ፤ ከዚያም ፡ ማለዳ ፡ በሮ ፡ አዞር ፡ ከሚባለው ፡ ደሴት ፡ ዐረፈ ።

ከዚያ ፡ ምሳውን ፡ በልቶ ፡ ወዳሥሩ ፡ ሰዓት ፡ ላይ ፡ ተነሥቶ ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ በሮ ፡ ከሌሊቱ ፡ በ፱ ሰዓት ፡ ቤርሙዳ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ለመድረስ ፡ መቶ ፡ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ያኽል ፡ ሲቀረው ፡ ካፒቴኑ ፡ አይሮፕላኑ ፡ መበላሸቱን ፡ አስታወቀ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ እንዳበደ ፡ ሰው ፡ ዘሎ ፡ ለመውደቅ ፡ መስኮቱን ፡ ሁሉ ሲቧጥጥ ፡ በማየታቸው ፡ የተሳፈሩት ፡ መንገዶኞች ፡ ከራሳቸው ፡ ይልቅ ፡ ለሱ ፡ ስላዘኑ ፡ ቶሎ ፡ ብለው ፡ ላስቲኩን ፡ ከወገቡ ፡ አስረው ፡ ከምሱሩን ፡ አፈንድተው ፡ ሲነፉ ፡ ፒስቶሊውን ፡ በገመድ ፡ ከንገቱ ፡ ላይ ፡ አስረው ፡ ፈላጊ ፡ ሲመጣ ፡ እንዲያገኝኽ ፡ ይህነን ፡ እንድትተኵስ ፡ ብለው ፡ አውጥተው ፡ ከባሕሩ ፡ ላይ ጣሉት ።

እነሱም ፡ ቶሎ ፡ ብለው ፡ ላስቲካቸውን ፡ ታጥቀው ፡ ፒስቶሊያቸውን ፡ አንገታቸው ፡ አግብተው ፡ ከባሕሩ ላይ ፡ ወደቁ ።

አይሮፕላኑም ፡ ወዲያው ፡ ተከታትሎ ፡ ከባሕሩ ፡ ውስጥ ፡ ወድቆ ፡ ሰጠመ ፡ ዐሥራ ፡ ሁለት ፡ የሚሆኑ ፡ መንገደኞች ፡ ካቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ጋራ ፡ በባሕሩ ፡ ላይ ፡ በውድቅት ፡ ጨለማ ፡ እየተንሳፈፉ ፡ ረዳት ፡ ይጠብቁ ፡ ነበር ።

ቤርሙዳ ፡ አይሮፕላኑ ፡ ከወደቀበት ፡ ሥፍራ ፡ በጣም ፡ ቅርብ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ረዳት ፡ መርከቦች ፡ በሩቅ ፡ ሲመጡ ፡ አዩ ፡ እነዚያ ፡ መንገደኞች ፡ ያሉበትን ፡ ሥፍራ ፡ ለመርከቡ ፡ አዛዥ ፡ ለማሳየት ፡ ምልክት ፡ የሚሰጠውን ፡ ፓስቶሊ ፡ ይተኵሱ ፡ ገሥር ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ግን ፡ በውነት ፡ ሕልም ፡ መስሎት ከእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ጭንቅና ፡ ክፉ ፡ ቅገርት ፡ መቼ ፡ እነቃ ፡ ይሆን ፡ እያለ ፡ ይጠባበቅ ፡ ነበር ። ከወገቡ ፡ በላይ ፡ ከባሕር ፡ ውጭ ፡ ከወገቡ ፡ በታች ፡ ከባሕር ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ ዓሦችና ፡ የባሕር ፡ አውሬዎች ፡ በተላለፉ ፡ ቍጥር ፡ እያንገላቱት ፡ በድንጋጤ ፡ እንደ ፡ በድን ፡ ሆኖ ፡ በዋና ፡ ለማምለጥ ፡ ይፍጨረጨር ፡ ነበር ።

አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ይጮኽ ፡ ይጨነቅ ፡ ነበር ፤ እነዚያ ፡ መንገደኞች ፡ ግን ፡ በፒስቶሊው ፡ ተኵሰው ፡ በማሳየት ፡ መርከቡ ፡ እየተጠጋ ፡ ከጠገባቸው ፡ ደርሶ ፡ ለቀማቸውና ፡ ወጡ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ግን ፡ ብቻውን ፡ ቀረ ፤ የመርከብ ፡ ሹማምት ፡ ሰዎቹን ፡ አውጥተው ፡ ከቈጠሯቸው ፡ በኋላ ፡ አንዱ ፡ የመርከብ ፡ ሹም ፡ እናንተ ፡ ብቻ ፡ ናችሁ ፡ ወይስ ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ አለ ፡ ብሎ ፡ ጠየቃቸው ።

እነሱም ፡ አንድ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰው ፤ የህንድ ፡ አገር ፡ ይሁን ፡ የግብጽ ፡ አናውቅም ፡ እሱ ፡ ብቻ ፡ ቀርቷል ፡ አሉት ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ የመርከቡ ፡ አዛዥ ፡ ትእዛዝ ፡ አሳልፎ፡የመርከቦቹን ፡ ሁሉ ፡ መብራት ፡ አስበርቶ ፡ ያስፈልገው ፡ ገ፫መር ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ያንን ፡ ግሩም ፡ የሆነ ፡ መብራት ፡ በማየቱ ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በክንቱ ፡ ያጫወቱት ፡ ነገር ፡ ትዝ ፡ ብሎት ፡ ሞቻለሁ ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ ያጫወቱኝ ፡ የጽድቅ ፡ ብርሃን ፡ ይህ ፡ ነው ፡ በማለት ፡ እስቦ ፡ ይፈራ ፡ ይንቀጠቀጥ ፡ ገ፫መር ።

ባሕሩ ፡ ከመብራቱ ፡ የተነሣ ፡ ወለል ፡ ብሎ ፤ እንደ ፡ ቀን ፡ በማታየቱ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርን ፡ በሩቁ ፡ አዩት ።

ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ተጠግተው ፡ ገመድ ፡ቢሰዱለት ፡ በድንጋጤ ፡ ምክንያት ፡ የማይዝ ፡ ሆነ ፤ ስለዚህ ፡ የዕቃ ፡ ማውጫ ፡ ሚንጠ ፡ ሰደው ፡ እንደ ፡ ዓሣ ፡ ጐትተው ፡ አወጡት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርንና ፡ የቀሩትን ፡ ካደጋ ፡ የዳኑትን ፡ ሰዎች ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ ቤርሙዳ ፡ ተጓዙ ፤ ሌሊቱ ፡ እስኪነጋ ፡ ከዚያው ፡ ከመርከብ ፡ ውስጥ ፡ ልብሳቸውን ፡ አስወልቀው ፡ የሚሞቅ ፡ ልብስ ፡ አልብሰው ፡ የሚሞቅ ፡ ነገር ፡ አጠጥተው ፡ አስተኙዋቸው ።

ማለዳ ፡ በዓለም ፡ ራዲዮ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ የሚባለው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ነጋዴ ፡ ያለበት ፡ አይሮፕላን ፡ ቤርሙዳ ፡ አጠገብ ፡ ወደቀ ፡ ተብሎ ፡ ቃል ፡ ተላለፈ ።

የመርከቡ ፡ ሹም ፡ ይህነኑ ፡ ወሬ ፡ በራዲዮ ፡ ስለ ፡ ሰማ ፡ ካደጋ ፡ የዳኑትን ፡ ሰዎች ፡ ስማቸውን ፡ ለመጠየቅ ፡ አስነሣቸው ፤ ሁሉንም ፡ በየስማቸው ፡ በያገራቸው ፡ ከጠየቀ ፡ በኋላ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርንም ፡ አገርዎ ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ፤ አገሬ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ነው ፤ የመርከቡ ፡ ከማንዳ ፡

ስምዎ ፡ ማነው ፡ ስሜ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ይባላል ፡ ካለው ፡ በኋላ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ የሚባለው ፡ ኢትዮጵያዊ ፡ ካይሮፕላን ፡ አደጋ ፡ መዳኑን ፡ በራዲዮ ፡ ለዓለም ፡ አስተላለፈ ።

ወሬውን ፡ ከሰሙ ፡ በኋላ ፡ ከኒዮርክ ፡ ብዙ ፡ የሥራ ፡ ጓደኞቹ ፡ መጥተው ፡ እንኳን ፡ እግዚአብሔር ፡ አተረፈኽ ፡ ብለው ፡ ደስታቸውን ፡ ከገለጡ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ኒዮርክ ፡ ይዘውት ፡ ሄዱ ፤ ወዲያው ፡ ከተሰናዳለት ፡ ሆቴል ፡ አልዶርፍ ፡ አስቶሪያ ፡ አስገቡት ።

ጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ቈይቶ ፡ ካዲስ ፡ አበባ ፡ ከካይሮ ፡ ከኢየሩሳሌም ፡ ከበርሊን ፡ ከፓሪስ ፡ ከሎንዶን ፡ ከሌሎችም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ከተሞች ፡ የጥቅም ፡ ጓደኞቹ ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ነጋዴዎች ፡ እንኳን ፡ እግዚአብሔር ፡ አተረፈኽ ፡ የሚል ፡ ቴሌግራም ፡ ሳያቋርጥ ፡ ቀኑን ፡ ሁሉ ፡ አለፈለት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በደረሰበት ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ምን ፡ ይሆን ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ የሚያደርስብኝ ፡ አሁንም ፡ ከሞት ፡ አፋፍ ፡ ተመለስኩ ፤ በእስተርሊን ፡ የነበረውም ፡ ገንዘቤ ፡ በዲቫሉያሲዮን ፡ ምክንያት ፡ ጐደለ ፡ እንዲያውም ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ የተነሣ ፡ እንደሆን ፡ በያለበት ፡ የተበተነውን ፡ ገንዘቤን ፡ ለመሰብሰብ ፡ አልችልም ፤ በውጭ ፡ መንግሥት ፡ ያለ ገንዘቤን ፡ ሁሉ ፡ በጦር ፡ ጊዜ ፡ ሊለቁልኝ ፡ አይችሉም ፡ ይሆናል ፡ ድካሜ ፡ ሁሉ ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ ሊቀር ፡ ነው ፡ በማለት ፡ ተጨነቀ ።

ይልቁንም ፡ በጣም ፡ የሚያሳዝነኝ ፡ ብዙው ፡ ገንዘቤ ፡ በአክሲዮንና ፡ በኦብሊጋሲዮን ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ የተነሣ ፡ እንደሆን ፡ ጨርሶ ፡ ይጠፋብኛል ፡ እያለ ፡ አሳቡ ፡ ሁሉ ፡ ጠቈረ ።

ማታውኑ ፡ እራቱን ፡ አልዶርፍ ፡ አስቶርያ ፡ በልቶ ፡ ሲያበቃ ፡ የጥቅም ፡ ጓደኞቹ ፡ መጥተው ፡ ከቲያትር ፡ ወይም ፡ ከሲኒማ ፡ ቤት ፡ እናምሽ ፡ ብለው ፡ ቢጠይቁት ፡ በጣም ፡ ደክሞኛል ፡ ዛሬ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ አልሄድም ፡ ብሎ ፡ ቀረ ።

ነገር ፡ ግን ፡ ከመጽሐፍ ፡ ቤቱ ፡ ውስጥ ፡ መጽሐፍ ፡ ሲመለከት ፡ አምሽቶ ፡ ወደ ፡ መኝታ ፡ ቤቱ ፡ ሄዶ ፡ ተኛ ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

የሰው ፡ ልጅ ፡ በሐሳብ ፡ ማዕበል ፡ ሲማታ ፡ ሐሳቡ ፡ ሲጠቍር ፡ የሚታየው ፡ ክፉ ፡ ቅዠት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሌሊት ፡ በሕልሙ ፡ መጥፎ ፡ ቅዠት ፡ ወደቀበት ።

ሕልሙም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ካንድ ፡ ረዥም ፡ ተራራ ፡ ላይ ፡ በግድ ፡ በጭንቅ ፡ እየቧጠጠ ፡ ወጥቶ ፡ ከተራራው ፡ ጫፍ ፡ ሲደርስ ፡ ብርቱ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ ተነሥቶ ፡ አንሥቶ ፡ ሊጥለው ፡ ሲል ፡ ከዛፍ ፡ ላይ ፡ ተንጠልጥሎ ፡ ዛፉን ፡ ይዞ ፡ ሲታገል ፡ ነፋሱ ፡ ኀይለኛ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ዛፉን ፡ ነቅሎ ፡ እሱንም ፡ ዛፉንም ፡ እንዳሞራ ፡ በሰማይ ፡ ይዞ ፡ ሄዶ ፡ ካንድ ፡ እጅግ ፡ የሚያስፈራ ፡ ቦታ ፡ የውስጡ ፡ መሬት ፡ በእሳተ ፡ ገሞራ ፡ ተገልብጦ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ከሆነ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ላይ ፡ ጣለው ።

ይህ ፡ ሥፍራ ፡ ተራሮቹም ፡ ሁሉ ፡ ተገለባብጠው ፡ የወደቁበት ፡ ያገር ፡ መልክ ፡ የሌለው ፡ የሚያስፈራ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ነው ።

በዚያም ፡ በሚገርምና ፡ በሚያስፈራ ፡ አገር ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ያሉ ፡ የሚያስፈሩ ፡ መልክ ፡ ያላቸው ፡ ምትሀቶች ፡ ይመላለሱበታል ።

አቶ ፡ ሀብተ ኹ ፡ ይመር ፡ ከእንደዚህ ፡ ያለ ፡ እግዚአብሔር ከተቈጣው ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ በመድረሱ ፡ ደንግጦ ፡ እየተንቀጠቀጠ ፡ ሲመለከት ፡ አንዱ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ የሚመስል ፡ መልኩ ፡ በጣም ፡ የሚያስፈራ ፡ ወደሱ ፡ ሲመጣ ፡ አየ ።

በዚያም ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ሀብተ ኹ ፡ ይመር ፡ መሬት ፡ ተከፍታ ፡ ብትውጠው ፡ ወደደ ።

ያም ፡ የሚያስፈራ ፡ ምትሀት ፡ ተጠግቶ ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ ከዚህ ፡ ምን ፡ አመጣህ ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርም ፡ ከተራራ ፡ ጫፍ ፡ ወጥቼ ፡ ስመለከት ፡ ብርቱ ፡ ዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ አንሥቶ ፡ እነሆ ፡ አሁን ፡ ከቆምኩበት ፡ ቦታ ፡ ጣለኝ ፤ እባክዎ ፡ ጌታው ፡ ይህ ፡ አገር ፡ ማን ፡ ይባላል ፡ ብሎ መለሰለት ።

ምትሀቱም ፡ (ፋንቶም) ፡ ይህ ፡ አገር ፡ ሺሮሺማ ፡ የሚባል ፡ ነው ። ይኸሁልህ ፡ ይህ ፡ ቦታ ፡ ነው ፡ ለዓለም ፡ ጥፋት ፡ የተደራጀው ፡ መሣሪያ ፡ የተፈተነበት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ እባክዎ ፡ በዚህ ፡ ከተማ ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ አልቋልን ፡ የብዙ ፡ ሰው ፡ ንብረት ፡ ጠፍቷልን ።

ምትሀቱም ፡ አዎን ፡ ካምስት ፡ መቶ ፡ ሺሕ ፡ የሚበልጥ ፡ ሕዝብ ፡ አልቋል ፤ በብዙ ፡ ሚሊዮንም ፡ የሚቈጠር ፡ የሕዝብ ፡ ንብረት ፡ ጠፍቷል ፤ ብዙዎችም ፡ ባንኮችና ፡ በዙዎችም ፡ የንግድ ፡ ጕዳዮች ፡ ተቃጥለዋል ፤ በብዙ ፡ ሺሕ ፡ የሚቈጠሩ ፡ ሀብታሞችና ፡ ነጋዴዎች ፡ አንደኛ ፡ ምትሀት ፡ (ፋንቶም) ፡ የከንቱ ፡ ከንቱ ፡ ሆነው ፡ ቀርተዋል ፡ ብሎ ፡ እጁን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ዘርግቶ ፡ አቤቱ ፡ አቤቱ ፡ የዓለም ፡ ፈጣሪ ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ መዓት ፡ ሁለተኛ ፡ በሰው ፡ ልጆችና ፡ ባገር ፡ ላይ ፡ አታድርስባቸው ፡ እያለ ፡ በሚያሳዝንና ፡ በሚያስጨንቅ ፡ ቃል ፡ ይጮኽ ፡ ዠመር ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ በጣም ፡ ደነገጠና ፡ ዕንባው ፡ ባይኑ ፡ ሞልቶ ፡ ለምትሀቱ ፡ እባክዎ ፡ መቅሠፍት ፡ ሁለተኛ ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ የደረሰ ፡ እንደሆን ፡ በኔ ፡ ንብረትና ፡ በኔ ፡ ባንክ ፡ ይደርስ ፡ ይመስልዎታልን ።

ምትሀቱ ፡ ዐይኑን ፡ ወደሱ ፡ አፍጦ ፡ አንተ ፡ ርጉም ፡ ራስኽን ፡ ብቻ ፡ ወዳጅ ፤ በናንተ ፡ በቃኝ ፡ አለማለት ፡ ምክንያት ፡ ነው ፡ ይህ ፡ መቅሠፍት ፡ የተፈጠረ ፤ የዓለም ፡ ጥፋት ፡ ሳያሳዝንህ ለራስህ ፡ ሀብት ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ የምታዝን ፡ ብሎ ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡ በጥፍሩ ፡ ጕሮሮውን ፡ ሊያንቀው ፡ ወደሱ ፡ ሲመጣ ፡ በድንጋጤ ፡ ብንን ፡ አለ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ከንቅልፉ ፡ ባኖ ፡ ሰውነቱ ፡ ሳይመለስ ፡ ሩብ ፡ ሰዓት ፡ ያኽል ፡ አእምሮውን ፡ ሳያውቅ ፡ ከቈየ ፡ በኋላ ፡ ጥቂት ፡ ሰውነቱ ፡ ሲመለስ ፡ ያለቅስ ፡ ይንቀጠቀጥ ፡ ዠመር ፤ ወዲያው ፡ መብራቱን ፡ አብርቶ ፡ ልብሱን ፡ ለብሶ ፡ በአንሳሰር ፡ መውረጃው ፡ በር ፡ አጠገብ ፡ ቆሞ ፡ ይደውል ፡ ዠመር ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ያለበት ፡ አፓርተማ ፡ ዐሥራ ፡ ስድስተኛው ፡ ደርብ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አንሳሰሩ ፡ እስኪ መጣለት ፡ ድረስ ፡ ከወደ ፡ ኋላው ፡ ምትሀቱ ፡ (ፋንቶም) ፡ የመጣበት ፡ እየመሰለው ፡ ይገላመጥ ፡ ነበር ። አንሳሰሩ ፡ እንደ ፡ ደረሰ ፡ ወርዶ ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ ተከፍቶ ፡ ከሚያድር ፡ ቡና ፡ ቤት ፡ ሄዶ ፡ ያንን ፡ የጭንቅ ፡ ሌሊት ፡ አሳለፈው ፡ ሲነጋጋም ፡ ከሆቴሉ ፡ ተመልሶ ፡ ጥቂት ፡ እንቅልፍ ፡ አሸለበው ።

ከጧቱ ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ ከእንቅልፉ ፡ ተነሥቶ ፡ ገላውን ፡ ታጥቦ ፡ ልብሱን ፡ ለብሶ ፡ በሦስት ፡ ሰዓት ፡ ቍርሱን ፡ አድርጎ ፡ ባራት ፡ ሰዓት ፡ ከትልቆች ፡ ባንኮች ፡ ዲሬክተሮችና ፡ ከጥቅም ፡ ጓደኞቹ ፡ ጋራ ፡ ስለ ፡ ጥቅምና ፡ ስለ ፡ እንዱስትሪ ፡ ስለ ፡ ኤኮኖሚ ፡ ጕዳይ ፡ ስብሰባ ፡ ስላለበት ፡ በቀጠሮው ፡ ሄደ ።

ነገር ፡ ግን ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ሌሊት ፡ በሕልሙ ፡ ስለ ፡ ተመታው ፡ በትር ፡ ደንዝዞ ፡ የሚናገረውን ፡ አያውቀውም ፡ ነበር ።

የተሰበሰቡትም ፡ የገንዘብ ፡ ሰዎች ፡ ስለ ፡ ዓለም ፡ አኳኋን ፡ ስለ ፡ እስተርሊን ፡ መውደቅ ፡ ስለ ፡ ሠራተኞች ፡ ግሬቭ ፡ ማድረግ ፡ ይልቁንም ፡ ሁለተኛ ፡ የዓለም ፡ ጦርነት ፡ የተነሣ ፡ እንደ ሆን ፡ በካፒታሊስቶች ፡ ላይ ፡ ምን ፡ ችግር ፡ እንደሚደርስባቸው ፡ ሲያወጡ ፡ ሲያወርዱ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ከጠረጴዛው ፡ ላይ ፡ ራሱን ፡ በእጁ ፡ ደግፎ ፡ አዝኖ ፡ ተክዞ ፡ ይታይ ፡ ነበር ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እነዚያ ፡ የባንክ ፡ ሰዎችና ፡ ባለገንዘቦች ፡ በዛሬው ፡ ስብሰባ ፡ ከሱ ፡ ምንም ፡ ነገር ፡ ስላላገኙ ፡ ባይሮፕላኑ ፡ መውደቅ ፡ ምክናያት ፡ የደነገጠው ፡ ብርቱ ፡ ድንጋጤ ፡ አሁንም ፡ ከራሱ ፡ ውስጥ ፡ ያልወጣለት ፡ ስለ ፡ መሰላቸው ፡ ቀጠሮውን ፡ ለሳምንቱ ፡ ቅዳሜ ፡ እንዲሆን ፡ ተስማምተው ፡ ጉባኤው ፡ ተዘጋ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርም ፡ አስቶርያ ፡ ሆቴል ፡ ተመልሶ ፡ ምሳውን ፡ ከበላ ፡ በኋላ ፡ ከመጻሕፍት ፡ ቤት ፡ ገብቶ ፡ ሲመለከት ፡ መጻሕፍትን ፡ እያለዋወጠ ፡ ሲያነብ ፡ ዐሥር ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ሆነ ።

አሳቡን ፡ ለማሳረፍ ፡ አንድ ፡ አቶሞቢል ፡ ተከራይቶ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ውጭ ፡ ሄዶ ፡ ግራና ፡ ቀኙ ፡ የባላገሩን ፡ ውበት ፤ በሜዳ ፡ ላይ ፡ የሚግጡትን ፡ የቀንድ ፡ ከብቶችና ፡ ዶሮዎች ፤ ዝዮች ፡ እየተመለከተ ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ምን ፡ ያኽል ፡ ዕድል ፡ ተሰጥቷቸዋል ፡ እያለ ፡ እየተደነቀ ፡ ሲሄድ ፡ ሳያው ቀው ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ኪሎ ፡ ሜትር ፡ ያኽል ፡ ተጓዘ ።

ወዲያው ፡ አንዲት ፡ የተዋበች ፡ ትንሽ ፡ መንደር ፡ አየ ፤ ከመን ደሯም ፡ ራቅ ፡ ብሎ ፡ በዙሪያዋ ፡ ብዙ ፡ መቃብር ፡ ያለባት ፡ በሐውልቶችና ፡ ባበባ ፡ ያጌጠች ፡ በውስጧም ፡ የመናፈሻ ፡ መንገዶች ፡ የተሠሩባት ፡ አንዲት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ተመ ለከተ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ይህንን ፡ ቦታ ፡ በማየት ፡ ልቡ ፡ ተነካ ፤ ይልቁንም ፡ አንዲት ፡ የባላገር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በማ የቱ ፡ ሌሊት ፡ በሕልሙ ፡ ያየውን ፡ የሚያስደነግጥ ፡ ቅዠት ፡ እግ ዚአብሔር ፡ በሰው ፡ ልጆችና ፡ በራሱም ፡ እንዳያደርስበት ፡ ጥቂት ፡ ጸሎት ፡ ለማድረግ ፡ አስቦ ፡ ወዲያው ፡ ነጂውን ፡ አቁም ፡ ብሎ ፡ ከአቶሞቢሉ ፡ ወጥቶ ፡ እቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ቅጽር ፡ ውስጥ ፡ ገባ ፡ ነጂው ፡ ግን ፡ ከቅጽሩ ፡ ውጭ ፡ ሆኖ ፡ ይጠብቀው ፡ ነበር ።

## ምዕራፍ ፡ ፲ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርም ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ተጠ ግቶ ፡ ሌሊት ፤ ስላየው ፡ ሕልም ፡ በጠለቀ ፡ ኀዘን ፡ ጸሎት ፡ ካደ ረገ ፡ በኋላ ፡ ከመቃብሩ ፡ አትክልት ፡ ውስጥ ባለው ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ በትካዜ ፡ እርምጃ ፡ እየተናፈሰ ፡ ለሙታን ፡ መታሰቢያ ፡ የተቀረጹትን ፡ ሐውልቶች ፡ እያደነቀ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ ሲመላ ለስ ፡ በድንገት ፡ አንድ ፡ ድምፅ ፡ ሰማ ።

እሱም ፡ ደንግጦ ፡ እየዞረ ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ሲመለከት ፡ ፀሐይ፡ ስለ ፡ ጠለቀች ፡ በሩቁ ፡ ለማየት ፡ አልቻለም ፤ ቢሆንም ፡ የሰማ ውን ፡ ድምፅ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለማወቅ ፡ እየዞረ ፡ ሲመለከት ፡ አንዲት ፡ ረቂቅ ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ንድፍ ፡ የነጣች ፡ የማትዳሰስ ፡ መልኳ ፡ ሕፃን ፡ ልጅ ፡ የመሰለች ፡ ባንድ ፡ ሐውልት ፡ አጠገብ ፡

ቆማ ፡ አየ ፤ ላቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ለማየት ፡ የረዳው ፡ የንጣቷ ፡ ብዛት ፡ በመሬቱ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ጮራ ፡ ሆኖ ፡ ይታይ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ነው ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ብቻውን ፡ በመቃ ብር ፡ ቦታ ፡ ጊዜው ፡ ጨልሞ ፡ አይቶት ፡ የማያውቀውን ፡ እንደ ዚህ ፡ ያለ ፡ ተአምር ፡ የሆነ ፡ ነገር ፡ በማየቱ ፡ በድንጋጤ ፡ ከራሱ እስከ ፡ እግሩ ፡ ድረስ ፡ ተንዘፈዘፈ ፤ ትኵር ፡ ብሎ ፡ እያየ ፡ በፍ ርሃት ፡ ወደሷ ፡ እየቀረበ ፡ አንቺ ፡ ምንድነሽ ፡ ብሎ ፡ ጠየቃት ።

ያችም ፡ ረቂቅ ፡ የሆነች ፡ ፍጥረት ፡ እኔ ፡ ነፍስ ፡ ነኝ ፡ ብላ ፡ መለሰችለት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ እባክሽ ፡ የማን ፡ ነፍስ ፡ ነሽ ፡ ብሎ ፡ ጠየቃት ።

እሷም ፡ ያባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ ነፍስ ፡ ነኝ ፡ ብላ ፡ መለሰችለት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ከድኾች ፡ ከተማ ፡ ተገናኝተን ፡ ብዙ ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ የተጫወትነው ፡ የመንፈሳዊ ፡ ድኻ ፡ ነፍስ ፡ ነሽን ።

እሷም ፡ አዎን ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ አለችው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በኀዘን ፡ በደስታ ፡ በፍርሃት ፡ የተቀላቀለ ፡ ዕንባውን ፡ እያፈሰሰ ፡ ወደሷ ፡ ቢቀርብ ፡ የመንፈሳዊ ፡ ድኻ ፡ ነፍስ ፡ ከመቃብሬ ፡ የጣልኩትን ፡ ያረጀ ፡ ልብስ ፡ ለብ ሰኽ ፡ ወደኔ ፡ መቅረብ ፡ አትችልም ፡ ብላ ፡ እንደ ፡ ጉም ፡ ሥፍራ ዋን ፡ ለቀቀችና ፡ እልፍ ፡ ብላ ፡ ቆማ ፡ አትቅረበኝ ፡ ከዚሁ ፡ ሆነኽ ፡ አነጋግረኝ ፡ አለችው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ የመንፈሳዊ ፡ ድኻ ፡ ነፍስ ፡ ከዚህ ፡ ምን ፡ አመጣሽ ፡ አገርሽ ፡ ኢትዮጵያ ፡ አይደለምን ።

የመንፈሳዊ ፡ ድኻ ፡ ነፍስ ፡ ርግጥ ፡ አገሬ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ያንን ፡ ያረጀ ፡ ልብሴን ፡ በመቃብር ፡ ጥዬ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ወህኒ ፡ ቤት ፡ ከመለጥኩ ፡ ወዲህ ፡ ወገን ፡ ዘመድ ፡ አጋር ፡ የለኝም ፡ ዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ የኔ ፡ አገር ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ምነው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ነፍስ ፡ ለኢ ትዮጵያ ፡ የሮፓ ፡ ነፍስ ፡ ለሮፓ ፤ የአሜሪካን ፡ ነፍስ ፡ ለአሜሪካን አይደለችምን ።

መንፈሳዊት ፡ ነፍስ ፤ አይደለም ፡ ይህ ፡ ከረጀው ፡ ልብስ ፡ ጋራ ፡ ከመቃብር ፡ ውስጥ ፡ ቀርቷል ፤ አምላካችን ፡ መንፈስ ፡ ነው ፤ እኛም ፡ መንፈስ ፡ ነን ፤ የምናመልከውም ፡ በመንፈስ ፡ ነው ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ በሥጋ ፡ በተወሰንን ፡ ጊዜ ፡ የተወሰነ ፡ አገር ፡ ነበረን ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ በሥጋ ፡ የተወሰነ ፡ ገዥ ፡ ብሚገዛን ፡ ጊዜ ፡ ዕውቀታችን ፡ አገራችን ፡ የተወሰነ ፡ ነበር ።

ዛሬ ፡ ግን ፡ ዓለም ፡ የማይወስነው ፡ ገዥ ፡ ስላለን ፡ ዕውቀት ፡ አይቈጠብብንም ፤ ዓለምም ፡ አይወሰንብንም ። ሁሉን ፡ እናውቃ ለን ፤ በሁሉም ፡ ሥፍራ ፡ እንገኛለን ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ እባክሽ ፡ መቼ ፡ ነው ፡ ከሥጋሽ ፡ የተለየሽው ።

መንፈሳዊት ፡ ነፍስ ፤ መጽሐፍ ፡ ሥጋን ፡ ክንዱ ፡ የሚያደርግ ፡ የተረ ገመ ፡ ነው ፡ ያለውን ፡ በመዘንጋት ፡ አንተን ፡ ያመንኩ ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ምን ፡ ጊዜ ፡ ነው ፡ አንቺ ፡ ስታም ኚኝ ፡ እኔ ፡ የካድኩሽ ።

መንፈሳዊት ፡ ነፍስ ፡ የክሕደትኽን ፡ ምስክር ፡ ከገንዘብ ፡ መያዣኽ ፡ ውስጥ ፡ አንዲት ፡ ብጣሽ ፡ ወረቀት ፡ አለችና ፡ ፈል ጋት ፡ አለችው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ የገንዘቡን ፡ ኰረጆ ፡ አውጥቶ ፡ ቢዳብስ ፡ ያችን ፡ ብጣሽ ፡ ወረቀት ፡ አገኛት ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ጨለማ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለማንበብ ፡ ባይችል ፡ እንኳ ፡ ዓለም ፡ ብቃኝ ፡ ውህኒ ፡ ቤት ፡ ሆነው ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ የጻፉ ለት ፡ መሆኗ ፡ ትዝ ፡ አለውና ፡ አዘነ ።

ይልቁንም ፡ ይህች ፡ ደብዳቤ ፡ ሳትጠፋ ፡ እስካሁን ፡ መቈ የቷ ፡ በጣም ፡ ገረመውና ፡ በኀዘንና ፡ በጸጸት ፡ ወይኔ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ ሥራ ፡ በዝቶብኝ ፡ እኮ ፡ ነው ፡ ወዳጄን ፡ የረሳሁት ፡ እምነቴን ፡ ያጐደልኩት ፡ ብሎ ፡ አለቀሰ ።

ያባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ ነፍስ ፡ አንተ ፡ ሀብታም ፡ አትዘን አታልቅስ ፡ እናንተ ፡ ዘወትር ፡ በዓለም ፡ ሁከትና ፡ ሽብር ፡ ጥቅምን ፡ በመዛረፍ ፡ ስትጯጯኹ ፡ እምነትን ፡ ለመስማት ፡ ገሮ ፡ እንደሌላችሁ ፡ የታወቀ ፡ ነው ፤ እንግዲህ ፡ በድኅና ፡ ያገናኘን ፡ ብላው ፡ ጥቂት ፡ በጥቂት ፡ እንደ ፡ ጉም ፡ እየረቀ ቀች ፡ ጠፋችበት ፤ (ተሰወረችው) ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ምነው ፡ ጥቂት ፡ ሳንነጋገር ፡ ሄድሽብኝ ፡ እያለ ፡ እጁን ፡ ዘርግቶ ፡ ሲጮኽ ፡ ቀኑ ፡ በጣም ፡ ጨልሞ ፡ ስለ ፡ ነበር ፡ ይልቁንም ፡ የፀ ፡ ብርሃን ፡ ሲጠፋ ፡ ፍጹም ፡ ውድቅት ፡ ስለ ፡ ሆነበት ፡ ተጨንቆ ፡ ሳለ ፡ ከመቃብሩ ፡ ውስጥ ፡ ከዚህ ፡ ቀደም ፡ ሰምቶት ፡ የማያውቅ ፡ የጭንቅና ፡ የመከራ ፡ ድምፅ ፡ ቢሰማ ፡ በፍርሃት ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ሲመለከት ፡ በመቃብሩ ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ ሲተላለፉ ፡ ያየ ፡ መስሎት ፡ ለመሸሽ ፡ ሲሞክር ፡ ራሱ ፡ ዞሮ ፡ እመቃብር ፡ ላይ ፡ ወደቀ ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ነጂውም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ በመቈየቱ ፡ ይልቁ ንም ፡ የጩኸት ፡ ድምፅ ፡ በመስማቱ ፡ ባትሪውን ፡ አብርቶ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ ቅጽር ፡ ውስጥ ፡ ቢገባ ፡ ካንድ ፡ መቃብር ፡ ሥር ፡ ወድቆ ፡ አየው ።

ነጂውም ፡ በጣም ፡ ደንግጦ ፡ ምናልባት ፡ ሽፍታ ፡ (ጋን ጊስተር) ፡ ለገንዘብ ፡ ሲል ፡ ገድሎት ፡ ሄዶ ፡ ይሆን ፡ በማለት ፡ በባትሪ ፡ ሰውነቱን ፡ ሁሉ ፡ ቢመለከት ፡ ምንም ፡ ደምና ፡ ቊስል ፡ አላገኘም ፤ ብቻ ፡ ባጠገቡ ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ ፊደል ፡ የተጻፈች ፡ ብጣሽ ፡ ወረቀት ፡ አግኝቶ ፡ ምን ፡ ይሆን ፡ በማለት ፡ ከኪሱ ፤ አኖራትና ፡ ቶሎ ፡ በአቶሞቢል ፡ ሄደና ፡ ዘበኞች ፡ አመጣ ።

የዘበኛውም ፡ አለቃ ፡ መጥቶ ፡ አወዳደቁን ፡ አይቶ ፡ ምናልባት ፡ ሰው ፡ ደብድቦት ፡ እንደሆን ፡ በማለት ፡ በፍጥነት ፡ በአቶሞቢል ፡ ሄዶ ፡ አንድ ፡ ሐኪምና ፡ አንድ ፡ የዘበኛ አለቃ ፡ ይዞ ፡ መጣ ፡ የወደቀበትን ፡ ቦታ ፡ በሜትር ፡ ከለኩ ፡ በኋላ ፡ ቦታውንና ፡ ሰው ዬውን ፡ ፎቶግራፍ ፡ አንሥተው ፡ ለዘበኛ ፡ የሚገባውን ፡ ምር መራ ፡ ሁሉ ፡ ከጨረሱ ፡ በኋላ ፡ ሐኪሙ ፡ ልቡን ፡ እንዲ

መረምረው ፡ ስለ ፡ ጠየቁት ፡ ሐኪሙም ፡ በጣም ፡ መርም"ሮ ፡ አልሞተም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ድካም ፡ አለው ፡ ስለዚህ ፡ ሙሉ ፡ ምርመራ ፡ እንዲደረግለት ፡ ወደ ፡ ሐኪም ፡ ቤት ፡ ብንወስደው ፡ ይሻላል ፡ ብሎ ፡ ካስታወቀ ፡ በኋላ ፡ ዘበኞቹ ፡ ተሸ ክመው ፡ ከአቶሞቢል ፡ ውስጥ ፡ አገቡትና ፡ ወደ ፡ ሐኪም ፡ ቤት ፡ ይዘውት ፡ ሄዱ ።

## ምዕራፍ ፲፩ ።

የሆስፒታሉ ፡ ዲሬክተር ፡ መጥቶ ፡ ምርመራ ፡ ካደረገለት ፡ በኋላ ፡ ሐኪሙ ፡ የሰው ፡ በትር ፡ አለመሆኑን ፡ አረጋግጦ ፡ እንደኔ ፡ ሐሳብ ፡ የሚሻለው ፡ ፕሮፌሰሮችና ፡ ሐኪሞች ፡ ስብሰባ፡ አድርገው ፡ ሙሉ ፡ ምርመራ ፡ እንዲደረግለት ፡ ወደ ፡ ኒዮርክ፡ በፍጥነት ፡ ቢሄድ የተሻለ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ አስታወቀ ።

ወደ ፡ ኒዮርክ ፡ ለመውሰድ ፡ የመጣበትን ፡ አገርና ፡ የተቀ መጠበትን ፡ ሆቴል ፡ ማወቅ ፡ አስፈላጊ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የዘበኛው፡ አለቃ ፤ ይለፉንና ፡ በገንዘብ ፡ ኰረጆው ፡ ውስጥ ፡ የሚገኙትን፡ ካርትቪዚት ፡ ሌሎችንም፡ ማስረጃዎች ፡ ለመፈለግ ፡ ኪሱን ፡ ይበረብር ፡ ዝመር ፤ ከይለፉ ፡ ውስጥ ፡ የተገኘው ፡ ምርመራ፡ አገሩ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ሥራው ፡ ንግድ ፡ የሚሄድባቸው ፡ አገሮች፡ ስዊስ ፡ እንግልጣር ፡ ፍራንስ ፡ አሜሪክ ፡ የሚል ፡ ነው ።

በገንዘብ ፡ማስቀመጫው ፡ ኰረጆ ፡ ጓዳ ፡ የተገኙ ፡ ካርትቪ ዚቶች ፡ የትልልቅ ፡ ካፒታሊስቶችና ፡ የሮችልድ ፡ ቤተ ፡ ሰቦች፡ ብቻ ፡ ናቸው ።

በኮቱ ፡ ውስጥ ፡ አልዶርፍ ፡ አስቶርያ ፡ የሚል ፡ አርእስት፡ ያለው ፡ የተከፈለ ፡ የሆቴል ፡ ሒሳብ ፡ ማስታወቂያ ፡ ተገኘ ።
ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሁሉም ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ ትልቅ ፡ ሰው ፡ ሳይሆን ፡ አይቀርምና ፡ ብለው ፡ ወደ ፡ ኒዮሮክ ፡ ለመውሰድ ፡ ከቈረጡ ፡ በኋላ ፡ ኒዮርክ ፡ ሆስፒታል ፡ ድረስ ፡ የሚሸኘው ፡ አንድ ፡ ሐኪም ፡ ጨምረው ፡ በአንቡላንስ ፡ ወደ ፡ ኒዮርክ ፡ ሰደዱት ።

ኒዮርክ ፡ እንደ ፡ ደረሱ ፡ አስቀድመው ፡ የሚያስፈልገውን ፡ ማስ ረጃ ፡ ለማግኘትና ፡ የሚኖርበትንም ፡ ሆቴል ፡ አስቶርያ ፡ መሆኑን ፡ ለማረጋገጥ ፡ ወደ ፡ አልዶርፍ ፡ አስቶርያ ፡ ሆቴል ፡ ይዘውት ፡ ሄዱ።

ነገር ፡ ግን ፡ እንቡላሱ ፡ ውስጥ ፡ እንዳለ ፡ የሆቴሉን ፡ ሹም ፡ ጠርተው ፡ ይለፉን ፡ አሳይተው ፡ ከዚህ ፡ ሆቴል ፡ መሆኑን ፡ ጠየ ቁት ፤ ሹሙም ፡ በጣም ፡ ደንግጦ ፡ ርግጥ ፡ ነው ፡ በዚሁ ፡ ሆቴል ፡ ነው ፡ የሚኖረው ፡ ብሎ ፡ በፍጥነት ፡ ወደ ፡ ሆቴሉ ፡ ገብቶ ፡ ለጥ ቅም ፡ ጓደኞቹ ፡ በስልክ ፡ አስታወቃቸው ።

ከጥቂት ፡ ደቂቃ ፡ በኋላ ፡ ሦስት ፡ አራት ፡ የሚሆኑ ፡ የጥቅም ፡ ጓደኞቹ ፡ ሀብታሞች ፡ መጥተው ፡ ሮዝቤልት ፡ ሆስፒታል ፡ አስ ገቡት ።

በማግስቱ ፡ ማለዳ ፡ በሦስት ፡ ሰዓት ፡ ብዙ ፡ ፕሮፌሰሮች ፡ ተሰ ብስበው ፡ ምርመራ ፡ አደረጉለት ፤ በዝርዝር ፡ ሰውነቱ ፡ ሁሉ ፡ በራዲዮ ፡ ፎቶግራፍ ፡ ተነሣ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ምንም ፡ የሕመም ፡ ምልክት ፡ አልተገኘበትም ፤ ቢሆንም ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በጣም ፡ ደኅና ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ድንጋጤውም ፡ ስላለፈለት ፡ ከፕሮፌ ሰሮቹ ፡ አንደኛውን ፡ «የማንታል ፡ ኤስፒስያል» ፡ የራስ ፡ መዘር ፡ ልዩ ፡ ፕሮፌሰር ፡ ጥያቄ ፡ እንዲያደርግለት ፡ ተስማምተው ፡ ጥያ ቄና ፡ ምርመራ ፡ ተዠመረ ።

ፕሮፌሰር ፡ ይህ ፡ በሽታ ፡ እንደምን ፡ ዠመረዎ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ከትላንት ፡ ወዲያ ፡ ሌሊቱን ፡ መጥፎ ፡ ቅዠት ፡ አቃዥቶኝ ፡ በጣም ፡ አዝኜ ፡ ነበር ፤ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ እንቅልፍ ፡ አልወስድ ፡ ስላለኝ ፡ ይልቁንም ፡ በሕልሜ ፡ ያየሁት ፡ የሚያስፈራ ፡ ነገር ፡ ከመኝታዬ ፡ ቤት ፡ የሚመጣብኝ ፡ ስለ ፡ መሰለኝ ፡ ልብሴን ፡ ለብሼ ፡ ከሌሊቱ ፡ በስምንት ፡ ሰዓት ፡ ያችን ፡ የምታስ ደነግጥ ፡ ሌሊት ፡ ለማሳለፍ ፡ ካንዲት ፡ የሌሊት ፡ ቡና ፡ ቤት ፡ ሄጄ ፡ አነጋሁ ።

ፕሮፌሰር ፤ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ነውን ፡ ከኒዮርክ ፡ ውጭ ፡ ሄደው ፡ የታመሙት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ አይደለም ፡ ማለዳ ፡ ከሆቴል ፡ ተመልሼ ፡ ትንሽ ፡ ተኝቼ ፡ በሦስት ፡ ሰዓት ፡ ዋና ፡ ስብሰባ ፡ ስለ ፡ ነበረኝ ፡

ሄጀ ፡ በጉባኤው ፡ ውስጥ ፡ ነበርኩ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ኅሊናዬ ፡ ያንን ፡ ያየውን ፡ የሚያስደነግጥ ፡ ሕልም ፡ በማሰብ ፡ የተሰበሰብ ንበትን ፡ ጉዳይ ፡ ምንም ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሳይሰማኝ ፡ ተክዤ ፡ አዝኜ ፡ የጉባኤው ፡ ሰዎች ፡ ስላዩኝ ፡ ቀጠሮውን ፡ ለቅዳሜ ፡ አስተላል ፈውት ፡ ጉባኤው ፡ ተዘጋ ።

ፕሮፌሰሩ ፤ እንግዲያው ፡ ከጉባኤው ፡ በኋላ ፡ ነዋ ፡ የሄዱት ።
አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ እርግጥ ፡ ከጉባኤው ፡ በኋላ ፡ ምሳዬን ፡ በልቼ ፡ ትንሽ ፡ መጽሐፍ ፡ ተመልክቼ ፡ ነው ፡ የሄድኩት ።

ፕሮፌሰሩ ፡ ስንት ፡ ሰዓት ፡ ይመስልዎታል ፡ ከሆቴል ፡ ወጥ ተው ፡ ከኒዮርክ ፡ ውጭ ፡ ሲሄዱ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ባልሳሳት ፡ ዐሥር ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ይመስለኛል ።

ፕሮፌሰሩ ፤ ከከተማ ፡ ውጭ ፡ ከሄዱ ፡ በኋላ ፤ ምን ፡ አደረጉ ።
አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ከአቶሞቢል ፡ ወርጄ ፡ አንዲት ፡ የባ ላገር ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ስላየሁ ፡ ትንሽ ፡ ጸሎት ፡ ለማድረግ ፡ ገባሁ ።

ፕሮፌሰሩ ፤ ከዚያ ፡ በኋላስ ፡ ወዴት ፡ ሄዱ ።
አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ አጠገብ ፡ ብዙ ፡ አበቦችና ፡ በጥበብ ፡ የተሠሩ ፡ የመቃብር ፡ ሐውልቶች ፡ ስላየሁ ደስ ፡ ብሎኝ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ እየተመላለስኩ ፡ እናፈስ ፡ ነበር ።

ፕሮፌሰሩ ፤ ከመቃብሩ ፡ ውስጥ ፡ ሲናፈሱ ፡ ስንት ፡ ሰዓት ፡ ይሆን ፡ ነበር ።
አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ምናልባት ፡ ባልሳሳት ፡ ላንድ ፡ ሰዓት ፡ ሩብ ፡ ጉዳይ ፡ ይሆን ፡ ይመስለኛል ።

ፕሮፌሰሩ ፤ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ምን ፡ ሆኑና ፡ ወደቁ ።
አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ካታክልት ፡ ውስጥ ፡ ከተናፈስኩ ፡ በኋላ ፡ ጥቂት ፡ ስለ ፡ ደከመኝ ፡ ቆሜ ፡ በጥበብ ፡ የተቀረጸውን ፡ አንድ ፡ ሐውልት ፡ ስመለከት ፡ ከሐውልቱ ፡ ዐሥር ፡ ሜትር ፡ ያኽል ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ አንዲት ፡ የረቀቀች ፡ እንደ ፡ ባዘቶ ፡ የነ ጣች ፡ የምታምር ፡ የሰው ፡ መልክ ፡ ቅርጽ ፡ ያላት ፡ ነፍስ ፡ አየሁ ።

ፕሮፌሰሩና ፣ የቀሩትም ፣ ሐኪሞች ፣ ርስ ፣ በርሳቸው ፣ ከተ ያዩ ፣ በኋላ ፣ ፕሮፌሰሩ ፣ ነፍስ ፣ መሆኗን ፣ በምን ፣ ዐወቋት ።

አቶ ፣ ሀብትኽ ፣ ይመር ፤ ይህን ፣ የሚገርም ፣ ነገር ፣ በማየቴ፣ ደንግጬ ፣ እየተንቀጠቀጥኩ ፣ ስፈራ ፣ ስቸር ፣ አንቺ ፣ ምንድነሽ፣ ብዬ ፣ ጠየቅኋት ።

እሷም ፣ የምታውቀኝ ፣ የመንፈሳዊ ፣ ድኻ ፣ ነፍስ፣ነኝ፣አለችኝ ።

ፕሮፌሰሩ ፤ ርስዎስ ፣ ምን ፣ ብለው ፣ መለሱላት ።

አቶ ፣ ሀብትኽ ፣ ይመር ፤ ከሥጋሽ ፣ ጋራ ፣ መቼ ፣ ተለያየሽና፣ ወደዚህ ፣ መጣሽ ፣ ብዬ ፣ ጠየቅኋት ።

እሷም ፣ አንተ ፣ የካድኸኝ ፣ ጊዜ ፣ ነው ፣ አለችኝ ። እኔም ፣ መቼ ፣ ነው ፣ የካድኩሽ ፣ ብዬ ፣ መለስኩላት ፣ እሷም፣የክ ሕደትኽን ፣ ምስክር ፣ የሚገልጥ ፣ ከገንዘብ ፣ ኰረጆኽ ፣ ውስጥ ፣ ይገኛል ፣ ፈልገው ፣ አለችኝ ።

ፕሮፌሰሩ ፤ ታዲያስ ፣ ወረቀት ፣ አገኙ ፤ እንደምን ፣ ሆነ ።

አቶ ፣ ሀብትኽ ፣ ይመር ፤ አዎን ፣ ከገንዘብ ፣ ኰረጆዬ ፣ ውስጥ፣ ስፈልግ ፣ አንዲት ፣ ብጣሽ ፣ ወረቀት ፣ አገኘሁ ፤ ባነበው ፣ መንፈ ሳዊ ፣ ድኻው ፣ ዓለም ፣ በቃኝ ፣ ወህኒ ፣ ቤት ፣ ታስረው ፣ የጻፉ ልኝ ፣ ደብዳቤ ፣ መሆኑን ፣ ተረዳሁት ፣ እነሆ ፣ ይህ ፣ ወረቀት ፣ በዘ በኛው ፣ ሹም ፣ እጅ ፣ ይገኛል ።

ፕሮፌሰሩ ፤ በዚህ ፣ ምክንያት ፣ እንደምን ፣ አእምሮዎን ፣ አጥ ተው ፣ ወደቁ ።

አቶ ፣ ሀብትኽ ፣ ይመር ፤ በዚህ ፣ አልወደቅሁም ፣ የወደቅ ሁበት ፣ ምክንያት ፣ የላኩብኝን ፣ ወረቀት ፣ በማየቴ ፣ በጣም ፣ ተክ ዤና ፣ አዝኜ ፣ ሳለሁ ፣ ያባ ፣ ሰው ፣ በከንቱ ፣ ነፍስ ፣ አትዘን ፣ በዓ ለም ፣ ላይ ፣ ያለውን ፣ ሀብት ፣ በመዛረፍ ፣ በመቃማት ፣ ሽብርና፣ ሁከት ፣ በማድረግ ፣ እናንተ ፣ ሀብታሞች ፣ ቁም ፣ ነገርን ፣ ለመስ ማት ፣ ዡሮ ፣ እንደሌላችሁ ፣ ዐውቃለሁና ፣ አላዝንም ፣ ደኅና ፣ ያገናኘን ፣ ብላ ፣ ተሰወረችኝ ።

ከዚህ ፣ በኋላ ፣ ከመቃብሩ ፣ ካትክልቱ ፣ ውስጥ ፣ ስምቼው ፣ የማላውቅ ፣ የሚያሳዝንና ፣ የሚያስደነግጥ ፣ የጭንቅ ፣ ድምፅ ፣ በያ ለበት ፣ ብሰማ ፣ ፈርቼ ፣ ግራና ፣ ቀኝ ፣ ስመለከት፣እንደ ፣ ጥላ ፣ የሚ

መስሉ   የሚያስፈሩ ፡ ነገሮች ፡ ሲመላለሱ ፡ አይቼ ፡ በድንጋጤ፡ ራሴ ፡ ዞሮ ፡ ወደቅሁ ፤ ከዚያ ፡ ከኋላ ፡ ምን ፡ እንደ ሆንኩ ፡ አላውቀውም ።

ፕሮፌሰሩ ፤ ይህነን ፡ ጥያቄ ፡ ከሰማ ፡ በኋላ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይስጥልኝ ፡ በጣም ፡ አመሰግንዎታለሁ ፡ ብሎ ፡ ፕሮፌሰሩ ፡ ሐኪሞቹም ፡ ሁሉ ፡ ካቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ዘንድ ፡ ወጥተው ፡ ካንድ ፡ ስብሰባ ፡ ከሚያደርጉበት ፡ አዳራሽ ፡ ገብተው ፡ ስለዚህ ፡ ጉዳይ ፡ ለመመካከር ፡ ተቀምጠው ፡ ብዙ ፡ ክርክር ከተደረገ ፡ በኋላ ፡ የሚበልጡት ፡ ፕሮፌሰሮች ፡ ራሱ ፡ ዞሯልና ፡ ለብቻው ፡ በመገለል ። በተለየ ፡ ለዚህ ፡ በሽታ ፡ ኤስፒሲያል ፡ በሆነ ፡ ሐኪም ፡ ካልታከመ፡ በጣም ፡ ያሠጋል ፡ አሉ ።

ሌሎቹ ፤ ፕሮፌሰሮች ፡ ግን ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ ምንም ፡ የመታመም ፡ ምልክት ፡ አይታይበትም ፡ በምርመራ ፡ ረገድና ፡ በራዲዮም ፡ የተነሣውን ፡ ስንመለከተው ፡ አንድም ፡ የበሽታ ፡ ምልክት፡ ሰጥቶም ፡ አይሰጥ ፡ ስለዚህ ፡ የራስ ፡ መዞር ፡ ሕመም ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ማከም ፡ ከጥቅሙ ፡ ጉድለቱ ፡ ይበልጣልና ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ አንስማማም ፡ ብለው ፡ ተለያዩ ።

ነገር ፡ ግን ፡ በሚበልጡት ፡ ፕሮፌሰሮች ፡ ቃል ፡ ተቈርጦ፡ ከዚያው ፡ ሮዝቤልት ፡ ከሚባለው ፡ ሐኪም ፡ ቤት ፡ ሰው ፡ ከማይደርስበት ፡ ብዙ ፡ ድምፅ ፡ ከማይሰማበት ፡ ከጸጥታ ፡ ቦታ ፡ ተኝቶ፡ እንዲታከም ፡ ተደረገ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፪ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ሳይታመም ፡ ነፍስን ፡ አየሁ ፡ ቤማለቱ ፡ እንደ ፡ በሽተኛ ፡ ተቈጥሮ ፡ ከሆስፒታል ፡ ብቻውን ፡ በጸጥታ ፡ ሥፍራ ፡ ይታከም ፡ ዠመር ።

ነገር ፡ ግን ፡ ሳይታመም ፡ ታሟል ፡ ተብሎ ፡ የሚታከም ፡ አቶ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ እየከሳ ፡ ሰውነቱ ፡ እየደከመ ፡ እየገረጣ ፡ የውነተኛ ፡ በሽተኛ ፡ ሆነ ፤ ምክንያቱም ፡ በሁለት ፡ ነገሮች ፡ ነው ።

፩ኛው ፡ እሱ ፡ ያየውን ፡ ረቂቅ ፡ ነገር ፡ እነሱ ፡ ባለማየታቸው፡ ታሟል ፡ ብለው ፡ ፈርደውበት ፡ ያለፈቃዱ ፡ በሚያደክም ፡ መድኃኒት ፡ ሌላ ፡ በሽታ ፡ ስለሚፈጥሩበት ፡ ነው ።

፩ኛው ፤ እንግዲህ ፡ እኔ ፡ ከዚህ ፡ ወድቄ ፡ ስቀር ፡ የደከምኩበት ፡ ገንዘቤ ፡ ለወገኔና ፡ ላገሬ ፡ ሳይሆን ፡ በከንቱ ፡ መቅረቱ ፡ አይደለምን ፡ በማለት ፡ ነው ።

ይልቁንም ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ያለውድ ፡ በግድ ፡ ሳይታመም ፡ በሚያደርገው ፡ መድኀኒት ፡ በምግባርም ፡ በሰውነቱም ፡ መድከም ፡ በሽታው ፡ እየጠናበት ፡ ስለ ፡ ሄደ ፡ በጣም ፡ ተጨነቀ ።

ከዕለታት ፡ ፩ ፡ ቀን ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ስለ ፡ ራስ ፡ መዞር ፡ በሽታ ፡ የሚወጋ ፡ ብርቱ ፤ መድኀኒት ፡ ወግተውት ፡ በጣም ፡ አወራጨው ፤ አካሉም ፡ የማይችለው ፡ ሆነ ።

ይልቁንም ፡ የሚያደርጉለት ፡ መድኀኒቶች ፡ ሁሉ ፡ ሳይታመም ፡ በመሆኑ ፡ የሚገድሉትና ፡ የሚያደክሙት ፡ ሚክሮብ ፡ በማጣታቸው ፡ የሱን ፡ ሰውነትና ፡ ሞራል ፡ ይገድሉ ፡ ያደክሙ ፡ ዠመር ።

ስለዚህ ፡ ሌሊቱን ፡ በጭንቅ ፡ ውስጥ ፡ ሳለ ፡ የድካም ፡ ስመመን ፡ ሽልብ ፡ አድርጎት ፡ በሕልሙ ፡ የመንፈሳዊ ፡ ድኻ ፡ ነፍስ ፡ መጥታ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርን ፡ አንተ ፡ ሀብታም ፡ ሰው ፡ ሆይ ፡ ያቺ ፡ የምታሳዝንና ፡ የምታስፈራ ፡ የምታስጨንቅ ፡ ቀን ፡ ደረሰች ።

አንተም ፡ ገንዘብኽን ፡ ሁሉ ፡ ተወርሰኽ ፡ ዕራቍትኽን ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ዜጋ ፡ ልትሆን ፡ ወደኛ ፡ ልትመጣ ፡ ነው ፡ አለችው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ በሕልሙ ፡ እየተንቀጠቀጠ ፡ እባክሽ ፡ ካንቺ ፡ ጋራ ፡ ለመኖር ፡ ነውን ፡ የምመጣው ።

ነፍስ ፤ አይደለም ፡ አንተ ፡ በመጨረሻው ፡ ፈራጅ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ተከሰስክ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ለመኖር ፡ አትችልም ፤ በኔና ፡ ባንተ ፡ መካከል ፡ ትልቅ ፡ ተራራ ፡ አለ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ማነው ፡ የከሰሰኝ ።

የመንፈሳዊ ፡ ድኻ ፡ ነፍስ ፡ ጎሊናኽ ፡ ነው ፡ የከሰሰኽ ፡ ብላ ፡ ስታነጋግረው ፡ ወዲያው ፡ በሕልሙ ፡ ውስጥ ፡ ሕልም ፡ ያይ ፡ ዠመር ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ አንድ ፡ ዳንስ ፡ ቤት ፡ ሲገባ ፡ ይህም ፡ ቤት ፡ እጅግ ፡ የተዋበ ፡ በብዙ ፡ መብራት ፡ ያጌጠ ፡ ወደ ፡ ሕዝብ ፡ መመላለሻው ፡ በኩል ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ መስኮት ፡ በሰፊ ፡ መስተዋት ፡

የተሠራ ፡ በውስጡም ፡ ብዙ ፡ ሀብታሞችና ፡ የተመረጡ ፡ ወገኖች ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ ዳንስ ፡ ሲያደርጉ ፡ ሲመለከት ፡ እሱው ፡ ራሱ ፡ አንዲት ፡ ሾጤ ፡ የተዋበች ፡ ልጅ ፡ ይዞ ፡ ዳንስ ፡ እያደረጉ ፡ ወደ ፡ ትልቁ ፡ መስኮት ፡ ሲቀርቡ ፡ በውጭ ፡ አንድ ፡ ድኻ ፡ ልብሱ ፡ የተበጫጨቀ ፡ ፊቱ ፤ በችጋርና ፡ በርዛት ፡ በውርጭና ፡ በፀሐይ ፡ ሐሩር ፡ ምክንያት ፡ ተሸረፍርፎ ፡ ተጕሳቍሎ ፡ ጢሙ ፡ አድጎ ፡ እንዳውሬ ፡ የሚያስፈራ ፡ ሰው ፡ የሰውን ፡ ልጆች ፡ ድሎት ፡ ለማየት ፡ ጓጕቶ ፡ ከመስተዋቱ ፡ ተጠግቶ ፡ ዐይኑን ፡ አፍጦ ፡ ሲመለከት ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ዳንስ ፡ የምታደርገው ፡ ቈንጆ ፡ የመልኩን ፡ መወላገድ ፡ አይታ ፡ ዋይ ፡ ብላ ፡ ጮኸች ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ሀብታሞች ፡ ሁሉ ፡ ደንግጠው ፡ ያንን ፡ ድኻ ፡ በዘበኛ ፡ አሲዘው ፡ ሲያሳስሩት ፡ አየ ።

ሁለተኛ ፡ አንድ ፡ በችግር ፡ ምክንያት ፡ በጣም ፡ የከሳ ፡ የጠቈረው ፡ ሰው ፡ ወደሱ ፡ ሲመጣ ፡ አየ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርም ፤ የተስቦ ፡ በሽታ ፡ ገገምተኛ ፡ መስሎት ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ ወደኔ ፡ አትቅረብ ፡ በሩቁ ፡ አነጋግረኝ ፡ ባልሳሳት ፡ ተስቦ ፡ የታመምክ ፡ ይመስለኛል ፡ አለው ።

ያም ፡ የከሳ ፡ ሰው ፡ በሽታ ፡ አልታመምኩም ፡ በሽታዬ ፡ አንተ ፡ ነኽ ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርም ፡ በሽታኽ ፡ የሆንኩት ፡ እንደ ፡ ምንድነው ።

ያም ፡ የከሳ ፡ ሰው ፡ መልኬ ፡ ተለዋውጦ ፡ ብከሳ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ያላወቅኸኝ ፡ እኔ ፡ የዚያ ፡ ውሃ ፡ የሚገባው ፡ ማለፊያ ፡ መሬት ፤ ጌታ ፡ ነኝ ፤ በእጅ ፡ አዙር ፡ ለኔ ፡ ሳታስብ ፡ ለመሬቱ ፡ አስበኽ ፡ ባራጣ ፡ ገንዘብ ፡ አበድረኽ ፡ መሬቴን ፡ ነቅለኽ ፡ እንደዚህ ፡ በችጋር ፡ የለዋወጥከኝ ፡ አለው ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ብልጠቱ ፡ ትዝ ፡ ብሎት ፡ በሕልሙ ፡ ሲያለቅስ ፡ ደግሞ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ እግሩ ፡ የተቈረጠ ፡ እየተንፏቀቀ ፡ ወደሱ ፡ ሲመጣ ፡ አይቶ ፡ በጣም ፡ ስላሳዘነው ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ ምን ፡ ሆንክና ፡ ነው ፡ እግርኽ ፡ የተቈረጠው ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ።

ያም ፡ ድኻ ፡ አንተ ፡ ለጥቅም ፡ ቀጠሮኽ ፡ ቸኵለኽ ፡ በአቶ ሞቢል ፡ ስትሮጥ ፡ ያስዳጥከኝ ፡ ነኝ ፤ እኔን ፡ ወንድምኽን ፡ በላዬ ፡ በመሄድኽ ፡ አዝነኽ ፡ ሳታነሣኝ ፡ ወደ ፡ ሐኪም ፡ ቤት ፡ ሳትወስ ደኝ ፡ ለጥቅምኽ ፡ ስትል ፡ እንደውሻ ፡ ሬሳ ፡ ጥለኸኝ ፡ በመሄድኽ ፡ አስታማሚ ፡ አጥቼ ፡ እግሬ ፡ ተቆረጠ ፡ ብሎ ፡ ሲነግረው ፡ ትዝ ፡ ብሎት ፡ የበለጠ ፡ ኀዘን ፡ ወደቀበትና ፡ ያለቅስ ፡ ዠመር ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ዴማስ ፡ የሚባለው ፡ የቅዱስ ፡ ጳውሎስ ፡ አሽ ከር ፤ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርን ፡ ና ፡ የወርቅና ፡ የብር ፡ መከማቻ ፡ ቦታ ፡ ላሳይኽ ፡ ብሎ ፡ የሱ ፡ ገንዘብ ፡ ወዳለበት ፡ ባንክ ፡ ወሰደ ውና ፡ የብሩንና ፡ የወርቁን ፡ ጕድጓድ ፡ ቆመው ፡ ሲመለከቱ ፡ ያገሩ ፡ ድኾችና ፡ እናት ፡ አባት ፡ የሞቱባቸው ፡ ሕፃናት ፡ ጠዋሪ ፡ ያጡ ፡ ሽማግሌዎች ፡ ብዙዎች ፡ ከልክ ፡ ያለፉ ፡ ድኾች ፡ ተሰብስበው ፡ የዚህን ፡ የገንዘብ ፡ ጌታ ፡ አቄራኙን ፡ ወደ ፡ መጨረሻ ፡ ፈራጅ ፡ ፊት ፡ አቅርቡን ። ይህ ፡ ሰው ፡ የጌታውን ፡ ወርቅ ፡ የቀበረ ፡ እናት አገሩን ፡ ገፎ ፡ የባዕድ ፡ አገር ፡ ውሽማውን ፡ ያለበሰ ፡ በደለኛ ፡ ነው ፤ የዘለዓለም ፡ ቅጣት ፡ ፍርድ ፡ ይገባዋል ፡ እያሉ ፡ ሲጮኹና ፡ ጥርሳቸውን ፡ እያፋጩ ፡ ዓይናቸውን ፡ አፍጠው ፡ ወደ ፡ እሱ ፡ ሲመጡ ፡ አይቶ ፡ በድንጋጤ ፡ ብንን ፡ ብሎ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ እያለ ፡ ይጮኽ ፡ ዠመር ።

በሆስፒታል ፡ ሌሊት ፡ የሚጠባበቁ ፡ አስታማሚዎች ፡ ሴቶች ፡ ደንግጠው ፡ እየሮጡ ፡ ቢገቡ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በሕልሙ ፡ ባየው ፡ ነገርና ፡ በሰውነቱም ፡ መድከም ፡ ምክንያት ፡ እየተንቀጠ ቀጠ ፡ ሲያለቅስ ፡ አይተው ፡ በሽታው ፡ ተለውጦበታል ፡ በማለት ፡ ቶሎ ፡ ብለው ፡ የሆሲፒታሉን ፡ ዲሬክተር ፡ ጠሩት ።

ዲሬክተሩም ፡ ካንድ ፡ ፕሮፌሰር ፡ ጋራ ፡ ገብተው ፡ ሲጨነ ቅና ፡ ሲቃትት ፡ ሲያለቅስ ፡ አይተው ፡ ደነገጡና ፡ ይመረምሩት ፡ ዠመር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሕመሙ ፡ ምንም ፡ ባይለወጥ ፡ ልቡ ፡ በጣም ፡ ደክሞ ፡ አገኙት ።

ወዲያው ፡ ፕሮፌሰሩ ፡ ምን ፡ ሆኑ ፡ ለምን ፡ እንደዚህ ፡ ያዝ ናሉ ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ።

አቶ ፡ ሀብተኽ ፡ ይመር ፡ ፕሮፌሰር ፡ ሆይ ፡ በጣም ፡ ማዘን ፡ ይገባኛል ፡ ምክንያቱም ፡ ዛሬ ፡ ሌሊት ፡ ያባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ ነፍስ ፡ መጥታ ፡ መሞቴን ፡ ነገረችኝ ፡ ስለዚህ ፡ ከልጅነት ፡ እስከ ፡ ዕውቀት ፡ የደከምኩበት ፡ ገንዘቤ ፡ ሁሉ ፡ ሥፍራ ፡ ሳላሲዘው ፡ የትም ፡ ባክኖ ፡ ሊቀር ፡ ነው ፡ እኔም ፡ በሰው ፡ አገር ፡ ወድቄ ፡ እንደምቀር ፡ አይጠረጠርም ።

ዲሬክተሩና ፡ ፕሮፌሰሩ ፡ ርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተያዩና ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ ምንም ፡ አልተሻለውም ፡ ራሱ ፡ እንደ ፡ ዞረ ፡ ነው ፡ ሲባባሉ ፡ አቶ ፡ ሀብተኽ ፡ ይመር ፡ ሰምቶ ፡ በብርቱ ፡ እየጮኽ ፡ ራሴ ፡ አል ዞረም ፡ ደኅና ፡ ነኝ ፡ በሽታዬ ፡ እናንተ ፡ ያላያችሁትን ፡ እኔ ፡ በማ የቴ ፡ እናንተ ፡ ያላመናችሁትን ፡ እኔ፡ በማመኔ ፡ ነው ።

እባካችሁ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ብላችሁ ፡ እንድናዘዝ ፡ አንድ ፡ ቄስና ፡ የማናዘዝ ፡ ሥልጣን ፡ ያላቸውን ፡ ሹማምንት ፡ ጥሩ ልኝ ፡ እያለ ፡ ያለቅስ ፡ ዠመር ።

ዲሬክተሩ ፡ እሺ ፡ ነገ ፡ ጧት ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ ቄሱና ፡ አና ዛዥ ፡ ይመጡልዎታል ፡ ብለው ፡ ከሕመሙ ፡ እንዲያሳርፈው ፡ አንድ ፡ መርፌ ፡ ወግተውት ፡ ሄዱ ።

ይህ ፡ አቶ ፡ ሀብተኽ ፡ ይመር ፡ ሳይታመም ፡ ታሚል ፡ ተብሎ፡ በመታከም ፡ የደከመ ፡ በመርፌው ፡ ምክንያት ፡ የድካም ፡ ሰመመን ፡ እንቅልፍ ፡ ወሰደው ።

በማግስቱ ፡ የሆስፒታሉ ፡ ዲረክተር ፡ አንድ ፡ ቄስና ፡ ሁለት ፡ የማናዘዝ ፡ ሥልጣን ፡ ያላቸው ፡ የመንግሥት ፡ ሹማምንት ፡ ይዞ ፡ መጣ ።

ምዕራፍ ፡ ፲፫ ።

ጥያቄ ፡ የመንግሥት ፡ ባለሥልጣኖች ፡ አገርዎ ፡ ወዴት ፡ ነው ።
አቶ ፡ ሀብተኽ ፡ ይመር ፡ ኢትዮጵያዊ ፡ ነኝ ።
ጥያቄ ፡ ሥራዎ ፡ ምድነው ።
አቶ ፡ ሀብተኽ ፡ ይመር ፡ ሥራዬ ፡ ንግድ ፡ ነው ።
ጥያቄ ፡ ገንዘብዎ ፡ ባገርዎ ፡ ውስጥ ፡ ነውን ፡ ወይስ ፡ በውጭ ፡ አገርም ፡ አለዎ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ የሚበልጠው ፡ ገንዘቤ ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ ነው ።

ጥያቄ ፤ ሚስት ፡ አለችዎትን ።
አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ሚስት ፡ የለችኝም ።
ጥያቄ ፤ ሚስት ፡ በምን ፡ ምክንያት ፡ የለችዎትም ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ጌቶቼ ፡ ሆይ ፡ የመጨረሻ ፡ ሰዓቴ ፡ ስለሆነ ፡ ኑዛዜዬን ፡ ከናንተ ፡ የምደብቀው ፡ ስለሌለ ፡ ልገልጥ ላችሁ ፡ እፈቅዳለሁ ።

ሚስት ፡ ያላገባሁበት ፡ ምክንያት ፡ ገንዘቤን ፡ ከሁሉም ፡ ነገር ፡ ይበልጥ ፡ ስለምወድ ፤ ሚስት ፡ አግብቼ ፡ የፈታኋት ፡ እን ደሆን ፡ ያልደከመችበትን ፡ ገንዘብ ፡ ተካፍላ ፡ እንዳትሄድ ፡ በማ ለት ፡ ነው ።

ጥያቄ ፤ እንግዲያማ ፡ ልጅም ፡ የለዎትም ።
አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ልጅስ ፡ ነበረኝ ፡ ግን ፡ ዲቃላ ፡ በመ ሆኑ ፡ በትልልቅ ፡ ሰዎች ፡ ፊት ፡ በመጥሯ ፡ ስሜን ፡ ያስገምተኛል ፡ በማለት ፡ የታወቀ ፡ ልጄ ፡ አይደለም ።

ጥያቄ ፤ ርስዎ ፡ ልጅ ፡ በመውለድዎ ፡ ምክንያት ፡ ሰው ፡ በምን ፡ ይገምትዎታል ፧ ቢወልዱስ ፡ መነኵሴ ፡ አይደሉ ፤ በልዩ ፡ ጉዳይዎ ፡ ማን ፡ ይገባል ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ እኔ ፡ ብዙ ፡ ጥቅም ፡ ያገኘሁት ፡ ለጕ ዳዬ ፡ ሁሉ ፡ ዋና ፡ መሣሪያ ፡ የሆነኝ ፡ ከንቱ ፡ ውዳሴ ፡ ስለሆነ ፡ የጥ ቅም ፡ ጓደኞቼ ፡ ሁሉ ፡ እኔን ፡ እንዳንድ ፡ ንጹሕ ፡ ሰው ፡ ከሌቶች ፡ ጋራ ፡ ያላደፍኩ ፡ አድርገው ፡ ስለሚያዩኝ ፡ ነው ።

ጥያቄ ፤ ይህ ፡ የሚሉት ፡ በከንቱ ፡ ውዳሴ ፡ የተሸፈነ ፡ ንጽ ሕና ፡ ለጥቅምዎ ፡ መውጫ ፡ መሰላል ፡ የሆነዎ ፡ ይመስለኛል ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ አዎን ፡ ዐወቁት ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ሊያናዝዙት ፡ የመጡ ፡ ቄስ ፡ ዕንባቸው ፡ ከይ ናቸው ፡ እየፈሰሰ ፡ አዬ ፡ ጕድ ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ ሰሎሞን ፡ ከሱ ፡ ይልቅ ፡ ጭንጋፍ ፡ ይሻላል ፡ ያለውን ፡ ችግረኛ ፡ ይመስላል ፡ ብለው ፡ አዘኑ ።

የማናዘዝ ፡ ሥልጣን ፡ ያለው ፡ ሹም ፡ ትንሽ ፡ ይቆዩኝ ፡ ብሎ ፡ ከበሽተኛው ፡ ቤት ፡ ወጥቶ ፡ ለዲሬክተሩ ፡ የሕመሙን ፡ ራፖር ፡ ይስጡኝ ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ።

ፕሮፌሰሩም ፡ ራፖሩን ፡ ሰጠው ።

የመንግሥቱም ፡ ሹም ፡ ራፖሩን ፡ አነበበና ፡ ራሱ ፡ የዘረ ፡ በሽተኛ ፡ መሆኑን ፡ በፕሮፌሰሮቹ ፡ ራፖር ፡ መረጋገጡን ፡ ከተረዳ ፡ በኋላ ፡ ሹሙ ፡ ተመልሶ ፡ ከበሽተኛው ፡ ቤት ፡ ገብቶ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርን ፡ አሁን ፡ ለመናዘዝ ፡ የፈቀዱበት ፡ ነገር ፡ ምንድነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ጌታው ፡ ገንዘቤ ፡ ሁሉ ፡ በውጭ ፡ አገር ፡ ተበታትኗል ፡ እኔ ፡ የደከምኩበትን ፡ ሀብት ፡ ላገሬ ፡ ድኾችና ፡ እናት ፡ አባት ፡ ለሌላቸው ፡ ልጆች ፡ ማሳደጊያ ፤ ለሆስፒታል ፤ ለተማሪ ፡ ቤት ፡ ሳይሆን ፡ በከንቱ ፡ ጠፍቶ ፡ እንዳይቀር ፡ ብዬ ፡ ነው ።

ጥያቄ ፡ ጤናዎ ፡ ደኅና ፡ ነው ፡ ምን ፡ አስፈራዎ ፡ አገርዎ ፡ ሲመለሱ ፡ አይናዘዙምን ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ጌታው ፡ ጊዜ ፡ የለኝም ፡ ሞት ፡ ከበራፌ ፡ ቆሟል ።

የመንግሥቱ ፡ ሹም ፤ ሞት ፡ ከበራፍዎ ፡ መቆሙን ፡ በምን ፡ ዐወቁት ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ጌታው ፡ አባ ፡ ሰው ፡ በከንቱ ፡ የሚባሉ ፡ መነኰሴ ፡ ባገሬ ፡ የነበርኩ ፡ ጊዜ ፡ የማውቃቸው ፡ መንፈሳዊ ፡ ፈላስፋ ፡ ሰው ፡ ሞተው ፡ ኖሮ ፡ ነፍሳቸው ፡ ከኒዮርክ ፡ እንደ ፡ መጣሁ ፡ ካንዲት ፡ ከተማ ፡ ውጭ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ከመቃብር ፡ አትክልት ፡ ውስጥ ፡ ስናፈስ ፡ ተገናኝተን ፡ ብዙ ፡ ንግግር ፡ አድርገን ፡ ነበር ።

ጌታው ፡ እነሆ ፡ ከዚህ ፡ ሆስፒታል ፡ የሚያዩኝ ፡ ነፍስን ፡ አየሁ ፡ በማለቴ ፡ ራሱ ፡ ዞሯል ፡ ተብዬ ፡ ሳልታመም ፡ እጅግ ፡ ብርቱዎች ፡ መድኃኒቶች ፡ በማድረግ ፡ ነው ፡ እንግዴህ ፡ አሁንማ ፡ እውነቱ ፡ ቢታወቅልኝ ፡ እንኳ ፡ ለኔ ፡ ምንም ፡ አይረባኝም ፡ ደክሜያለሁ ።

አሁንም ፡ ደግሞ ፡ ዛሬ ፡ ሌሊት ፡ በሕልሜ ፡ ያችው ፡ የኛ ፡ የቅዱስ ፡ ነፍስ ፡ መጥታ ፡ ያ ፡ የሚያስፈራው ፡ የሚያስጨንቀው ፡ ሰዓት ፡ ሊደርስብኽ ፡ ነው ፡ ገንዘብኽ ፡ ባልሆነው ፡ ገንዘብ ፡ ወዳጅ ፡ ግዛበት ፡ አለችኝ ።

ጌታው ፡ ይህ ፡ ያከማቻሁት ፡ ገንዘብ ፡ የመወቀሻና፡የመጨቃጨ
ቂያ ፡ ምንጭ ፡ ሊሆን ፡ነው ፤ እኔ ፡ ሳልከዳው ፡ አሁኑኑ ፡ የምወደው ፡
ገንዘብ ፡ ከድቶት ፡ ወዳገሩ ፡ ለመመለስ ፡ እንቢ ፡ አለኝ ፤ እንግዴህ ፡
ውሻ ፡ ሊሞት ፡ ሲል ፡ ከጌታው ፡ እግር ፡ ሥር ፡ መጥቶ ፡ እንደሚ
ወድቅ ፡ እኔም ፡ ከሁሉም ፡ አብልጬ ፡ ከምወደው ፡ ገንዘብ ፡
አጠገብ ፡ በባዕድ ፡ አገር ፡ ልወድቅ ፡ ነው ፤ ወዮ ፡ ምን ፡ ይሻለ
ኛል ፡ እያለ ፡ ይጮኽ ፡ ዠመር ።

የመንግሥቱ ፡ ሹም ፡ ምንም ፡ የሐኪሞቹን ፡ ምርመራ ፡
በማንበብ ፡ ራሱ ፡ እንደ ፡ ዞረ ፡ ቢያምን ፡ እንኳ ፡ ንግግሩ ፡
በጣም ፡ ልቡን ፡ ስለ ፡ ነካው ፡ አዘነ ።

ቄሱ ፡ ግን ፡ ጌታው ፡ ነፍስ ፡ በማየትዎ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ የወደ
ቁት ፡ ወይስ ፡ ሌላ ፡ የሚያስፈራ ፡ ነገር ፡ ገጠመዎ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ ነፍስ ፡ በማየቴ ፡ ብቻ ፡ አይደለም
ይልቁንም ፡ ነፍስ ፡ በታየችኝ ፡ ጊዜ ፡ ደስ ፡ ብሎኝ ፡ ፍርሃት ፡ ሁሉ ፡
ጠፍቶልኝ ፡ ነበረ ።

ምክንያቱም ፡ በነፍስ ፡ ማማርና ፡ ርቀት ፡ ንጽሕና ፡ ይልቁንም ፡
ብርሃኗ ፡ በመሬቱ ፡ ላይ ፡ ውጋገን ፡ ሆኖ ፡ በማየቴ ፡ ልዩ ፡ የሆነ ፡
ስሜት ፡ ተሰምቶኝ ፡ ነበር ፡ ነገር ፡ ግን ፡ ነፍስ ፡ ደኅና ፡ ያገኘኝን ፡
ብላ ፡ ስትሰወረኝ ፡ ያ ፡ የመቃብር ፡ ቦታ ፡ ሁሉ ፡ ውድቅት ፡ ጨለማ ፡
ሆነብኝ ።

ወዲያው ፡ ሰምቼው ፡ የማላውቅ ፡ የሚያሳዝን ፡ ድምፅ ፡ በመቃ
ብር ፡ ውስጥ ፡ ሰምቼ ፡ ስገላመጥ ፡ በጨለማው ፡ ውስጥ ፡ ከመቃብሩ ፡
ላይ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ የሚመስሉ ፡ ነገሮች ፡ ብማየቴ ፡ ከእግሬ ፡ እስከ ፡
ራሴ ፡ በፍርሃት ፡ ተሡነጠቅሁ ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አእምሮዬ ፡ ጠፋ ፤
ወደቅሁ ።

ቄሱ ፡ ወደ ፡ ኖቴሩ ፡ ዘወር ፡ ብለው ፡ ርግጥ ፡ እኒህ ፡ በሽ
ተኛ ፡ እንደሚሉት ፡ ነፍስን ፡ ለማየት ፡ ይቻላል ፤ ስለዚህ ፡ አእም
ሯቸው ፡ ጠፍቷል ፡ ብለን ፡ ሳናናዝዝ ፡ መሄድ ፡ ይገባ ፡ አይ
መስለኝም ፡ አሉት ።

የመንግሥቱ ፡ ሹም ፤ ይህ ፡ እውነት ፡ ነገር ፡ አይደለም ፡ ርግጥ ፡ አንዳንድ ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ ያሳዝናል ፤ ቢሆንም ፡ በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ የተመሠረተውን ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ቅዠት ፡ ልን ቈጥረው ፡ ይገባናል ።

ስለዚህ ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ ራሱ ፡ የዘረ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ልናናግዘው ፡ አይቻለንም ፡ በሕግ ፡ የታወቀ ፡ ልጅ ፡ ቢኖረው ፡ ለልጁ ፡ ሕግ ፡ የሚፈቅድለትን ፡ እንሰጥ ፡ ነበር ፤ ሚስት ፡ ብትኖረው ፡ ለሚ ስቱ ፡ የሚደርሳትን ፡ ገንዘብ ፡ እንሰጣት ፡ ነበር ፤ ይህ ፡ ሁሉ ፡ የለም ።

ስለዚህ ፡ የዚህ ፡ የሰው ፡ ሀብት ፡ እንደዚሁ ፡ በየመንግሥቱ ፡ ስም ፡ በባንክ ፡ ቢቀመጥ ፡ በሕጉ ፡ ረገድ ፡ የተገባ ፡ ነው ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ቂሱና ፡ የመንግሥቱ ፡ ሹም ፡ በሹክሹ ክታ ፡ ሲነጋገሩ ፡ ከልጋው ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተጋደመ ፡ ይሰማ ፡ ነበርና ፡ በብርቱ ፡ ቃል ፡ እየጮኽ ፡ ወይኔ ፡ ብልሹ ፡ የሆንኩ ፡ ፍጥረት ፡ ካገሬ ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ያገኘሁትን ፡ ሀብት ፡ በባዕድ ፡ አገር ፡ በትኜ ፡ እኔም ፡ እንደ ፡ ውሻ ፡ ከሀብቴ ፡ እግር ፡ ሥር ፡ በባዕድ ፡ አገር ፡ ልወድቅ ፡ ነኝ ።

እኔ ፡ ያልታመንኩ ፡ ባሪያ ፡ የጌታዬን ፡ ወርቅ ፡ የቀበርኩ ፡ የኔ ፡ ባልሆነው ፡ ገንዘብ ፡ ወዳጅ ፡ ያልገዛሁ ፡ ኀጢአተኛ ፤ ያገሬ ፡ ድኾች ፡ ሲጮኹና ፡ ሲፋረዱኝ ፡ እንሆ ፡ አሁኑኑ ፡ በዠሮዬ ፡ ይሰማኛል ።

እንግዴህ ፡ የቀረኝ ፡ ሥጋዬን ፡ እንዳሮጌ ፡ ልብስ ፡ በመቃብር ፡ ጥዬ ፡ በጸጸት ፡ እሳት ፡ መቃጠል ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እያለ ፡ ካልጋው ፡ ላይ ፡ እየተንፈራፈረ ፡ ያለቅስ ፡ ዠመር ።

የመንግሥቱ ፡ ሹምና ፡ ቄሱ ፡ ደንግጠው ፡ ካጠገቡ ፡ ቆመው ፡ እነሱም ፡ ዕንባቸው ፡ ይፈስ ፡ ነበር ።

ወዲያው ፡ ደወል ፡ ደውለው ፡ ሐኪሙ ፡ እንዲጠራ ፡ ላስታ ማሚዎቹ ፡ አስታወቁና ፡ ሐኪሙ ፡ ወዲያው ፡ መጣ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርም ፡ ዕንባው ፡ ካልጋው ፡ ላይ ፡ እየፈሰሰ ፡ ልቡ ፡ በጣም ፡ እየመታ ፤ ትኵሳቱም ፡ ወጥቶ ፡ ሲወራጭ ፡ አይቶ ፡ የእን ቅልፍ ፡ መርፌ ፡ ወጋውና ፡ የጣር ፡ ሰመመን ፡ ሽልብ ፡ አደረገው ።

ምዕፍራ ፡ ፲፬ ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ሌሊቱን ፡ ትኵሳት ፡ ያለልክ ፡ በገዛቶ በት ፡ በጣር ፡ ተይዞ ፡ ሲንፈራገጥ ፡ በጭንቅ ፡ አደረ ።

ከጧቱ ፡ በ፲፪ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ካንገቱ ፡ ቀና ፡ ብሎ ፡ ርጉም ፡ ነው ፤ ገንዘቡን ፡ በፊቱ ፡ ያላስቀደመ ።

ወዮልኝ ፡ እኔ ፡ በጥቂት ፡ ያልታመንኩ ፡ ባሪያ ፡ በጌታዬ ፡ ፊት ፡ ምን ፡ እመልስ ፡ እሆን ፡ ብሎ ፡ ዐንገቱን ፡ አዘነበለና ፡ ሁለት ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ስርቅ ፡ ካለው ፡ በኋላ ፡ እንሆ ፡ ያች ፡ የመጨረሻ ፡ ቀን ፡ ነፍስ ፤ ከደመ ፡ ነፍስ ፡ ጋራ ፡ ያላት ፡ ያንድነት ፡ ማሠሪያ ፡ በግድ ፡ ሲቈረጥ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ጭንቅ ፤ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ጣር ፤ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ አስተያየት ፤ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ድምፅ ፡ ትሰማ ፤ ያችን ፡ የጭ ንቅ ፡ ሰዓት ፡ ማየት ፡ ሰው ፡ መሆን ፡ አያስመኝም ።

በጣም ፡ የሚያሳዝነው ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በዚያች ፡ በምታስጨ ንቅ ፡ የሞት ፡ ጥላ ፡ ባጨለመበት ፡ ደቂቃ ፡ ውስጥ ፡ ባጠገቡ ፡ ያለውን ፡ የርስት ፡ ካርታና ፡ የባንክ ፡ ደረሰኝ ፡ የገንዘብ ፡ ትሬትር ፡ በየባንኩ ፡ ያለውን ፡ ገንዘብ ፤ ደረሰኝ ፡ ያለበትን ፡ ኰረጆ ፡ በጣሩ ፡ ውስጥ ፡ አን ሥቶ ፡ በጥፍሩና ፡ በጥፍሩ ፤ ከደረቱ ፡ ላይ ፡ አንቆ ፡ ይዞ ፡ ነፍሱ ፡ ከሥጋው ፡ ተለያየች ።

በውነት ፡ ሰሎሞን ፡ በመጽሐፉ ፡ መክብቡ ፡ እንደዚህ ፡ ብሎ ፡ የጻፈው ፡ ተፈጸመ ።

በሕፃንነትኽ ፡ ወራት ፡ ፈጣሪኽን ፡ አስብ ፤ የጭንቀት ፡ ቀን ፡ ሳይመጣ ፡ ደስም ፡ አያሰኙኝም ፡ የምትላቸው ፡ ዓመታት ፡ ሳይደርሱ ፤ ፀሐይና ፡ ብርሃን ፤ ጨረቃና ፡ ከዋክብትም ፡ ሳይጨልሙ ፤ ደመናም ፡ ከዝናም ፡ በኋላ ፡ ይመለሳል ፤ ቤት ፡ ጠባቂዎች ፡ በሚንቀጠቀጡ በት ፡ ቀን ፤ ኀያላንም ፡ ሰዎች ፡ ይዋረዳሉ ፤ ፈጮችም ፡ ዝም ፡ ይላሉ ፤ ጥቂቶች ፡ ሆነዋልና ፤ በመስኮትም ፡ የሚመለከቱ ፡ ይጨ ልማሉ ፤ ወደ ፡ አደባባይም ፡ የሚወስዱ ፡ ደጆች ፡ ይዘጋሉ ፤ የወ ፍጮውም ፡ ድምፅ ፡ ይላሿል ፤ ድምፁም ፡ እንደ ፡ ታናሽ ፡ ወፍ ፡ ይሆናል ፤ ዜማም ፡ የሚጮኹ ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ዝግ ፡ ይሆናሉ ።

ደግሞም ፤ ቀናውን ፡ መንገድ ፡ መውጣት ፡ ይፈራሉ ፤ በመንገ
ድም ፡ ይደነግጣሉ ፤ ለውዝም ፡ ታብባለች ፡ አንበጣም ፡ እንደ ፡
ሸክም ፡ ትከብዳለች ፤ ፊቃድም ፡ ይጠፋል ፤ ሰው ፡ ወደ ፡ ዘለዓለሙ ፡
ቤት ፡ ይሄዳልና ፤ አልቃሾችም ፡ በደባባይ ፡ ላይ ፡ ይዞራሉ ፤ የብሩ ፡
ድሪ ፡ ሳይበጠስ ፤ የወርቁም ፡ ኵስኵስት ፡ ሳትፈጭ ፤ ማድጋው ፡ በም
ንጩ ፡ ላይ ፡ ሳይሰበር ፤ መሬትም ፡ ወደ ፡ ነበረበት ፡ ወደ ፡ ምድር ፡
ሳይመለስ ፤ መንፈስም ፡ ወደ ፡ ሰጠው ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመለ
ሳል ፤ ሰባኪም ፡ አለ ፤ ሁሉም ፡ የከንቱ ፡ ከንቱ ፡ ነው ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ ይህ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ የመዠመሪያና ፡
የመጨረሻ ፡ ታሪኩ ፡ ዘወትር ፡ ከፊታችን ፡ እንዲሆን ፡ ያስፈልጋል ።
ይህ ፡ ጽሑፍ ፡ ዘወትር ፡ በሀብታችን ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ መልከም ፡
መጋቢ ፡ እንድናውቅበት ፡ ያሳስባል ።

ይልቁንም ፡ ገንዘባችን ፡ ባልሆነው ፡ ገንዘብ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ተሾ
ምን ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ወዳጅ ፡ እንድንገዛበት ፡ አስፈላጊ ፡ ነው ።
የሰው ፡ ልጅ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ እንደ ፡ መሸ ፡ አዳሪ ፡ ቀኑ ፡ ባልተ
ወሰነ ፡ የቤት ፡ ኪራይ ፡ የተቀመጠ ፡ ሙያተኛ ፡ መሆኑን ፡ አለመርሳት ፡
ዋና ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ነው ።

እነሆ ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ጥሮ ፡ ግሮ ፡
ኀሊናውን ፡ ሞራሉን ፡ ኵራቱን ፡ ለገንዘብ ፡ መሥዋዕት ፡ አድርጎ ፡
እናቱን ፡ ገፎ ፡ ውሽማውን ፡ እንደሚያለብስ ፡ ዕብድ ፡ ሰው ፡ ከእ
ናት ፡ አገሩ ፡ ያገኘውን ፡ ሀብት ፡ ለባዕድ ፡ አገር ፡ አሳልፎ ፡ በመስ
ጠቱ ፡ ለዘለዓለም ፡ በማይጠፋ ፡ የጸጸት ፡ እሳት ፡ ይቃጠላል ።

ይልቁንም ፡ በጣም ፡ የሚያሳዝነው ፡ ከሚስት ፡ ይልቅ ፡ ገንዘ
ቡን ፡ ስለ ፡ ወደደ ፤ ከልጁ ፡ ይልቅ ፤ የሥጋ ፡ መውጫ ፡ ርካቡን ፡
ከንቱ ፡ ውዳሴን ፡ ስላፈቀረ ፤ ወራሽ ፡ እንኳ ፡ አጥቶ ፡ ድካሙ ፡ ሁሉ ፡
የከንቱ ፡ ከንቱ ፡ ሆኖ ፡ በመጨረሻ ፡ ሰዓቱ ፡ ርጉም ፡ ነው ፡ ገንዘ
ቡን ፡ ሳያስቀድም ፡ የሞተ ፡ ብሎ ፡ እሱም ፡ ገንዘቡም ፡ በባዕድ ፡
አገር ፡ ተቀብረው ፡ ቀሩ ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ ሰውነትን ፡ የሚያስጠላ ፡ ከሁሉም ፡ ይልቅ ፡
አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ የገንዘቡንና ፡ የርስቱን ፡ ደረሰኝ ፡ ያለበትን ፡
ኮረጆ ፡ በእጁ ፡ አንቆ ፡ ገናዠች ፡ በግድ ፡ ያላቀቁት ፡ ነው ፤ ከገን
ዘቡ ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ፍቅር ፡ ቢኖረው ፡ ነው ።

በመጻሕፍት ፡ የተነገረው ፤ ሰው ፡ እናት ፡ አባቱን ፡ ይተዋል ፤ ከሚስቱም ፡ ጋራ ፡ ይጣበቃል ፤ ሁለቱም ፡ አንድ ፡ ሥጋ ፡ ይሆናሉ ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፡ ግን ፡ ከሚስት ፡ ገንዘብን ፡ ወዶ ፤ ከገንዘብ ፡ ጋራ ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ሕይወቱ ፡ ተጣብቆ ፡ በግድ ፡ ተለያየ ፤

ልጁንም ፡ ለጥቅም ፡ ማግኛ ፡ ከንቱ ፡ ውዳሴ ፡ ሲል ፡ በሕግ ፡ ፊት ፡ ሳያውቀው ፡ ስለ ፡ ቀረ ፡ የወላድ ፡ መካን ፡ ሆኖ ፡ በችግር ፡ ላይ ፡ ጣለው ።

ያገሩን ፡ ድኾች ፡ እንዳይወልድ ፡ ለገንዘቡ ፡ ምቹ ፡ ሥፍራ ፡ ሲፈልግ ፡ ከባዕድ ፡ አገር ፡ ስላኖረው ፡ ከድቶት ፡ ቀረ ።

ይህ ፡ ሰው ፡ እንደዚህ ፡ ሕይወቱንም ፡ ነፍሱንም ፡ ክብሩንም ፡ ጥሎ ፡ ያገኘውን ፡ ሀብት ፡ ምን ፡ ያኽል ፡ አነማለት ። የለም ፡ ለራሱ ፡ ጒዳይ ፡ ምንም ፡ ያኽል ፡ አላወጣም ፤ ያንድ ፡ ብርቱ ፡ ገበሬ ፡ ያኽል ፡ እንኳ ፡ አልበላለትም ።

ምክንያቱም ፡ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመር ፤ የድሎት ፡ በሽታ ፡ ስለ ፡ ታመመና ፡ ጣፋጭ ፡ መብልና ፡ ሥጋ ፡ መጠጥ ፡ ስለ ፡ ተከለከለ ፡ ድኻ ፡ የሆነ ፡ ምግብ ፡ እንደ ፡ ተመገበ ፡ ነው ፡ የሞተው ።

አመንዝራ ፡ ሴት ፤ ለሴቶች ፡ ነውር ፡ ናት ፡ እንደ ፡ ተባለው ፤ አቶ ፡ ሀብትኽ ፡ ይመርም ፡ ለሀብታሞች ፡ ሁሉ ፡ ነውርና ፡ ዕፍረት ፡ ሆኖ ፡ አሰደባቸው ።

ይህ ፡ መጽሐፍ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በግንባሩ ፡ ወዝ ፡ ሠርቶ ፡ ሀብታም ፡ መሆንን ፡ አይነቅፍም ።

ነገር ፡ ግን ፡ ለሰው ፡ ብዙ ፡ ሀብት ፡ የሚሰጠው ፡ ብዙ ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ መሆኑን ፡ ያስታውሳል ፤ እኛ ፡ የሀብታችን ፡ አዛዥና ፡ ሠራተኛ ፡ መሆናችንን ፡ ያስረዳል ።

ለምሳሌ ፤ አንድ ፡ ሚኒስቴር ፡ በቡድጄ ፡ ተወስኖ ፡ የተሰጠውን ፡ ገንዘብ ፡ ምንም ፡ ሥራ ፡ ሳይሠራበት ፡ ባመቱ ፡ መጨረሻ ፡ ለገንዘብ ፡ ሚኒስቴር ፡ እንዳለ ፡ ቢያስረክብ ፡ ይመሰገናልን ፡ አይመሰገንም ፤ እንዲያው ፡ በገደላቸው ፡ ሥራዎች ፡ ምክንያት ፡ የቅጣት ፡ ፍርድ ፡ ይፈረድበታል ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ ሶሎን ፡ የሚባል ፡ የግሪክ ፡ ፈላስፋ ፡ የሰውን ፡ መጨረሻውን ፡ ካላየሁ ፡ አላመሰግንም ፡ እንዳለው ፡ እኛም ፡ እንደ ዚህ ፡ ያለ ፡ ክፉ ፡ መጨረሻ ፡ እንዳይደርስብን ፡ እግዚአብሔርን ፡ እንለምናለን ።



## የራስ ፡ ቢ. መ. እ. አ ሳ ብ ። UENSÉES DE B. M. E.

፩ ፤ ጊዜ ፡ አይቶ ፡ የማይጠላ፡ ጊዜ ፡ አይቶ፡ የማይወድ፡ እውነተኛ፡ ወዳጅ ፡ መጽሐፍ ፡ ብቻ ፣ ነው ።

❊

፪ ፤ ሰውን ፡ በገንዘብ ፡ መስጠት ፡ ብቻ ፡ ይወደኛል ፡ ማለት ፡ ውቅያኖስን፡ ዐፈር፡ ሞልቼ፡ አደለድላለሁ፣ እንደ ማለት፡ ነው ።

❊

፫ ፤ ሆዳም ፡ ሰው ፡ ዘወትር ፡ እንደ ፡ ዛሬ ፡ ያለ ፡ ምግብ ፡ በልቼም ፣ አላውቅም ፣ በማለቱ ፡ የሚወደውን ፡ ሰው ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አያውቀውም ።

❊

፬ ፤ በገንዘብ ፡ የተገዛ ፡ ወዳጅነት ፡ በመከራ ፡ ጊዜ ፡ በነፋስ ፡ እንደ ሚበተን ፡ ደመና ፡ ብን ብሎ ፡ ይጠፋል ።

❊

፭ ፤ መከራ ፡ ባይኖር ፡ የወዳጅ ፡ መመዘኛ ፡ የሃይማኖት ፡ ሚዛን ፡ ባልተገኘም ፡ ነበር ።

❊

፮ ፤ ዓይኑ ፡ የታመመ ፡ ሰው ፡ ፀሐይን ፡ ትኵር ፡ ብሎ ፡ ለማየት ፡ እንደማይችል፡ ራሱን፡ ብቻ፡ የሚወድ፡ ሰው፡ እውነትን ፡ ማየት ፡ አይችልም ።

❊

፯ ፤ የሰው ፡ ልጅ ፡ እውነተኛ ፡ ኀዘኑ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ በተጣለ ፡ ጊዜ ፡ በሕፃንነቱ ፡ ያለቀሰው ፡ መራራ ፡ ልቅሶ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

❊

፰ ፤ ሰው ፡ ዕራቁቱን ፡ ከናቱ ፡ ማሕፀን ፡ ስለ ፡ ወጣ ፡ ከጌትነት ፡ ይልቅ ፡ ድኽነትን ፡ በቶሎ ፡ ይለምዳል ።

❊

፱ ፤ የሞትን ፡ ፊት ፡ እንኖራለን ፡ በማለት ፡ መጋረጃ ፡ ባንሸፍነው ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ ሰፊ ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ አንችልም ፡ ነበር ።

❊

፲ ፤ በዓለም ፡ ላይ እውነተኛ ፡ የፍርድ ፡ መጽሐፍ ፡ አለ ፤ እውነተኛ ፡ ፈራጅ ፡ ግን ፡ እስካሁን ፡ አልተገኘም ።

፨

፲፩ ፤ የውነተኛ ፡ ፍርድ ፡ ሚዛን ፡ ተይዞ ፡ የሚታየው ፡ በሞት ፡ እጅ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

፲፪ ፤ የሐሰት ፡ ፍርድ ፡ ጌትነትን ፡ ስትለብስ ፡ መልኳም ፡ ደም ፡ ግባቷም ፡ እውነትን ፡ ትመስላለች ።

፨

፲፫ ፤ የሰው ፡ ልጅ ፡ ገንዘቡ ፡ እንዳይሰረቅ ፡ ለመጠበቅ ፡ ይችል ፡ ይሆናል ፤ ራሱን ፡ ከመሰረቅ ፡ ግን ፡ አያድንም ።

፨

፲፬ ፤ ጠንቋይና ፡ ሕልም ፡ የሚያዩ ፡ ሰዎች ፡ የሚወደዱት ፡ ሞትንና ፡ ድኽነትን ፡ በማታለል ፡ መጋረጃ ፡ ሸፍነው ፡ ስለሚያቀርቡ ፡ ነው ።

፨

፲፭ ፤ የሰው ፡ ልጆች ፡ ዕድሜ ፡ ባለመወሰኑ ፡ ያታላዮች ፡ መነገጃ ፡ ሆነ ።

፲፮ ፤ ሰነፍ ፡ ሰው ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለማወቅ ፡ ብትፈልግ ፡ እኔ ፡ ዐውቃለሁ ፡ ሲል ፡ ታገኘዋለኽ ።

፨

፲፯ ፤ በዓለም ፡ ላይ ፡ አንዳንድ ፡ ፈላስፋ ፡ ባይኖር ፤ የሰው ፡ ልጆች ፡ ከተናጣቂ ፡ አውሬ ፡ የከፋ ፡ ጠባይ ፡ ይፈጠርባቸው ፡ ነበር ።

፨

፲፰ ፤ በሰው ፡ የሚታመን ፡ የሰውን ፡ ተፈጥሮ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የማያውቅ ፡ ነው ።

፨

፲፱ ፤ ሃይማኖት ፡ በጕርፍና ፡ በነፋስ ፡ ማዕበል ፡ ቢመታ ፤ የማይወድቅ ፡ ብርቱ ፡ ግንብ ፡ ነው ።

፨

፳ ፤ ክህደት ፡ ጥቅጥቅ ፡ ባለ ፡ ዱር ፡ ውስጥ ፡ በጽኑ ፡ ጨለማ ፡ በዳበሳ ፡ መሄድ ፡ ነው ።

፨

፳፩ ፤ ሰው ፡ መግደል ፡ የገዛ ፡ መልኩን ፡ ማጥፋት ፡ ነው ።

፨

፷፪ ፡ ሰው ፡ መግደል ፡ ከብት ፡ ከማረድ ፡ የመጣብን ፡ ክፉ ፡ የጭካኔ ፡ ልምድ ፡ ነው ።

፨

፷፫ ፡ ቀጣ ፡ ክራቱ ፡ ባሕርያተ ፡ ሥጋ ፡ ውስጥ ፡ የሚፈነዳ ፡ ቮልካን ፡ (እሳተ ፡ ገሞራ) ፡ ማለት ፡ ነው ።

፨

፷፬ ፡ ሰብቅ በማይጮኽ ፡ ጠመንዣ ፡ ወንድምን ፡ መግደል ፡ ነው ።

፨

፷፭ ፡ ትዕቢት ፡ ራስን ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ መርሳት ፡ ነው ።

፨

፷፮ ፡ ኵራት ፡ የድኽነት ፡ በሽታ ፡ የመታመም ፡ ምልክት ፡ ነው ።

፨

፷፯ ፡ መፍራት ፡ የሃይማኖት ፡ መጕደል ፡ ነው ።

፨

፷፰ ፡ ቂም ፡ የልብ ፡ ነቀርሳ ፡ ነው ።

፨

፷፱ ፡ በቀል ፡ ለመግደል ፡ ማድፈጥ ፡ ነው ።

፨

፸ ፡ ትሕትና ፡ የወዳጅ ፡ መሳቢያ ፡ ገመድ ፡ ነው ።

፨

፸፩ ፡ መለማመጥ ፡ ዋና ፡ የመንጠቅያ ፡ መሣሪያ ፡ ነው ።

፨

፸፪ ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ የማይለይ ፡ ወዳጅ ፡ ነው ።

፨

፸፫ ፡ የሰው ፡ ወዳጅነት ፡ እስከ ፡ መቃብር ፡ ድረስ ፡ ነው ።

፨

፸፬ ፡ የዘመድ ፡ ወዳጅነት ፡ እስከ ፡ ኑዛዜ ፡ መፍሰስ ፡ ይቈያል ።

፨

፸፭ ፡ የልጅ ፡ ፍቅር ፡ ከገንዘብ ፡ መውደድ ፡ ውስጥ ፡ የተገኘ ፡ ነው ።

፴፮ ፤ ከሁሉም ፡ አብልጠን ፡ የምንወደው ፡ ገንዘባችን ፡ ገና ፡ ስንታ
መም ፡ ይከዳናል ።

፨

፴፯ ፤ እውነተኞች ፡ ባልና ፡ ሚስት ፡ በመቃብርም ፡ ውስጥ ፡ አይለያዩም ።

፨

፴፰ ፤ ክፉ ፡ ሴት ፡ የትዕግሥት ፡ ማጥኛ ፡ ተማሪ ፡ ቤት ፡ ናት ።

፨

፴፱ ፤ የሰው ፡ ልጅ ፡ ወንድሙን ፡ ባለማመኑ ፡ ውሻ ፤ ያሳድጋል ፡
ስለዚህ ፡ ባሁኑ ፡ ጊዜ ፡ ከውሻ ፡ የተሻለ ፡ ወዳጅ ፡ አልተገኘም ።

፨

፵ ፤ ዐዋቂ ፡ ማለት ፡ አለማወቁን ፡ የሚያውቅ ፡ ሰው ፡ ነው ።

፨

፵፩ ፤ ብልጥግና ፡ የጭንቅና ፡ የሐሳብ ፡ መገዘሪያ ፡ ሰፊ ፡ እርሻ ፡ ነው ።

፨

፵፪ ፤ ድኽነት ፡ የተሻለ ፡ ሲሆን ፡ የዕብለትና ፡ የመሠሠት ፡ በሽታ ፡
ይጠናበታል ።

፨

፵፫ ፤ የሀብታም ፡ የተለየ ፡ ደዌው ፡ ክህደትና ፡ ትምክሕት ፡ የመም
ሰል ፡ በሽታ ፡ ናቸው ።

፨

፵፬ ፤ ሰው ፡ ማለት ፡ በዛሬና ፡ በነገ ፡ መካከል ፡ የሚዘል ፡ ተጫዋች ፡
ነው ።

፨

፵፭ ፤ ሌሊት ፡ ማለት ፡ የሰውን ፡ ምኞትና ፡ ሐሳብ ፡ ማሰሪያ ፡
የወህኒ ፡ ቤት ፡ ነው ።

፨

፵፮ ፤ ቀዝርት ፡ ከወህኒ ፡ ቤት ፡ ያመለጠ ፡ እስረኛ ፡ ማለት ፡ ነው ።

፨

፵፯ ፤ አመስጋኝ ፡ ከጊዜ ፡ ጋራ ፡ የሚተላለፍ ፡ ደንበኛ ፡ አታላይ ፡ ነው ።

፨

፵፰ ፡ መቃብር ፡ ማለት ፡ ያረጀ ፡ ልብሳችንን ፡ የምንጥልበት ፡ ጕድ ጓድ ፡ ነው ።

፨

፵፱ ፡ ቤት ፡ ማለት ፡ ባልተወሰነ ፡ ቀን ፡ የተከራየነው ፡ መኖሪያ ፡ ነው ፡

፨

፶ ፡ ርስት ፡ ማለት ፡ የግብዝን ፡ ልብ ፡ መደገፊያ ፡ ሰባራ ። ምርኵዝ ፡ ነው ።

፨

፶፩ ፡ ዕውቀቱን ፡ በቀልድ ፡ ለማሳየት ፡ የሚጥር ፡ ሰው ፡ ሞኝነቱን ፡ በቶሎ ፡ ይገልጣል ።

፨

፶፪ ፡ ጻድቅ ፡ ማለት ፡ አገርና ፡ ወገን ፡ ዘመድ ፡ የሌለው ፡ ሰው ፡ ነው ።

፨

፶፫ ርኅሩኅ ፡ ማለት ፡ ባታላዮች ፡ ዕንባ ፡ መብቱን ፡ የሚለቅ ፡ ነው ።

፨

፶፬ ፡ የሕግ ፡ ሁሉ ፡ አባት ፡ ለራስኽ ፡ ሊደረግብኽ ፡ የማትወደውን ፡ እንደዚሁም ፡ በወንድም ፡ ላይ ፡ አታድርግ ፡ የተባለው ፡ ነው ።

፨

፶፭ ፡ ክፉ ፡ ጠባይ ፡ ከቤተ ፡ ዘመድ ፡ ላይ ፡ የሚተላለፍ ፡ የቈዳ ፡ በሽታ ፡ ነው ።

፨

፶፮ ፡ ተማሪ ፡ ቤት ፡ የክፉ ፡ ጠባይ ፡ ማከሚያ ፡ ሆስፒታል ፡ ነው ።

፨

፶፯ ፡ ምግባር ፡ ላንድ ፡ ቤተ ፡ ሰብና ፡ ላንድ ፡ መንግሥት ፡ በጠቅላላው ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ አስተዳዳሪ ፡ የዘመድ ፡ ዳኛ ፡ ነው ።

፨

፶፰ ፡ ምግባር ፡ የሌለው ፡ አገር ፡ ነፍስ ፡ የሌለው ፡ ሥጋ ፡ ማለት ፡ ነው ፡

፨

፶፱ ፡ ምጽዋት ፡ ራሳችን ፡ እንኳ ፡ ለማወቅ ፡ የማይገባን ፡ የምሥጢር ፡ ስጦታ ነው ።

፨

፺ ፤ ጸሎት ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ጋራ ፡ ለመነጋገር ፡ የተቃጠርንበት ፡ ሰዓት ፡ ነው ።

፨

፺፩፤ እውነተኛ ፡ ሰው ፡ በዓለም ፡ ሁሉ ፡ በመብራት ፡ ቢፈለግ ፡ አንድ ፡ እንኳ ፡ አይገኝም ።

፨

፺፪፤ እውነት ፡ መራራ ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ በከንቱ ፡ ውዳሴ ፡ ካልተሸፈነች ፡ አትዋጥም ።

፨

፺፫፤ የውነትን ፡ ፋና ፡ በጅኽ ፡ ይዘኽ ፡ በቀናው ፡ መንገድ ፡ ብትጓዝ ፡ አንድ ፡ እርምጃ ፡ እንኳ ፡ ሳተኼድ ፡ ራስን ፡ ብቻ ፡ መውደድ ፡ እፍ ፡ ብሎ ፡ ይጠፋብኻል ።

፨

፺፬ ፤ ነፍሰ ፡ ገዳዮችን ፡ በምትፈልግበት ፡ ጊዜ ፡ ራሱን ፡ ብቻ ፡ ከሚወድ ፡ ሰው ፡ አደባባይ ፡ ኺድ ።

፨

፺፭፤ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ የሥልጣኔንና ፡ የዕውቀትን ፡ መሠረት ፡ ማስተሳሰሪያና ፡ ማጠንከሪያ ፡ ብረትና ፡ ስሚንቶ ፡ ነው ።

፨

፺፮፤ መጋባት ፡ ከሁሉ ፡ ነገር ፡ የከበረ ፡ ሲሆን ፤ በቃል ፡ ኪዳኑ ፡ መዝገብ ፡ ውስጥ ፡ መፋታትን ፡ ያሳያል ።

፨

፺፯፤ ሚች ፡ ሰው ፡ በሀብቱ ፡ ሲኰራ ፡ በጣም ፡ ያሳዝናል ።

፨

፺፰፤ በግፍ ፡ ከተገኘ ፡ ገንዘብ ፡ ድጋፍነት ፤ የመቃ ፡ ምርኩዝ ፡ ይጠነክራል ።

፨

፺፱፤ በግፍ ፡ የተገኘን ፡ ገንዘብ ፡ የሚወርስ ፡ ልጅ ፤ የዘማውያት ፡ ሴቶች ፡ ባንክ ፡ ይሆናል ።

፨

፻ ፤ በጦር ፡ ጊዜ ፡ በምብ ፡ ከፈረሳቸው ፡ ቤቶች ፡ ይልቅ ፤ ግፍና ፡ ዕብሪት ፡ ያፈረሳቸው ፡ ቤቶች ፡ ይበልጣሉ ።

፨

፻፭ ፤ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈሩ ፡ ቤተ ፡ ዘመዶች ፡ ያሉት ፡ ዘወትር ፡ በተማሪ ፡ ቤት ፡ እንደሚኖር ፡ ሰው ፡ ነው ።

፨

፻፮ ፤ ስንፍናና ፡ ድሎት ፡ ባይኖሩ ፡ ፋርማሲዮች ፡ (መድኃኒት ፡ ቤቶች) ፡ ሁሉ ፡ ይዘጉ ፡ ነበር

፨

፻፯ ፤ ብስጭት ፡ አጥቍሮ ፡ ማየት ፤ ኀዘን ፡ ተስፋ ፡ መቍረጥ ፡ ከስንፍና ፡ ውስጥ ፡ የሚበቅሉ ፡ ኀጢአቶች ፡ ናቸው ።



# ሣልሳዊ ፡ ዳዊት ።

## ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ።

ባ፲፱፻፵፪ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡

ከራስ ፡ ቢ. መኰንን ፡ እንዳልካቸው ፡ ተጻፈ ።

ታርሞ ፡ ዓራተኛ ፡ ታተመ ።

## መ ቅ ድ ም ።

ይህ ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ፡ ለቲያትር፡ ጨዋታ፡ እንደሚመች ፡ ባጭሩ ፡ የተጻፈ ፡ ምግባር ፡ ነው ።

የመጻፉም፡ መሠረት ፡ የዘፉኙ፡የሟልሳዊ፡ ዳዊት ፡ ታሪክ ፡ ነው። ስለ ፡ ሟልሳዊ ፡ ዳዊት ፡ ከኢትዮጵያ ፡ ነገሥታት ፡ ታሪክ ፡ ውስጥ ፤ ዘፋኙ ፡ ዳዊት፡ የሚባል ፡ እናነባለን ፤ ምክንያቱ፡ ምንም ፡ ተዘርዝሮ ፡ ባይጻፍ ፡ ምናልባት ፡ ሟልሳዊ ፡ ዳዊት ፡ የመንግሥቱ ፡ ከባድ ፡ ሸክ ምና ፡ ብርቱ ፡ አላፊነት ፡ እንዳይሰማው ፡ ጊዜውን ፡ በደስታና ፡ በዘፈን ፡ ለማሳለፍ ፡ ይሆን ፡ ይሆናል ። ነገር ፡ ግን ፡ የኢትዮጵያ ፡ ነገሥታት ፡ የሚበልጡት ፡ የመንግሥታቸውን ፡ ከባድ ፡ ሸክምና ፡ ብርቱ ፡ አላፊነት ፡ ለመሸከም ፡ እንዲችሉ ፡የሚያበረታታቸው ፡ ምግ ባርና ፡ ሃይማኖት ፡ በጽኑ ፡ ሥራ ፡ ላይ ፡ ጊዜያቸውን ፡ ማሳለፍ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ከባድ ፡ ሸክም ፡ ሳይሰማቸው ፡ ታሪካቸ ውን ፡ አሳምረው ፡ አለፉ ።

ዘፋኙ ፡ ዳዊት ፡ ግን ፡ ጊዜውን፡ በደስታ፡ ለማሳለፍ፡ ስለ፡ መረጠ፡ በሕይወቱ ፡ ታሪክ ፡ ላይ ፡ ጥቁር ፡ ስም ፡ ጥሎበት ፡ ሄደ ፡ (አለፈ) ።

ያለፈው ፡ ጊዜ ፤ ያለፉትን ፡ ነገሥታት ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ በታሪክ ፡ ላይ ፡ ሥዕላቸውን ፡ ሥሎልን ፡ ያልፋል ። የሰው ፡ ምግባ ሩና ፡ ባሕርዩ ፡ መልኩም ፡ በታሪክ ፡ ላይ ፡ ተቀርጾ ፡ ለሚመጣው ፡ ትውልድ ፡ ይቈያል ፤ ዐይኑ ፡ የታወረ ፡ ሰው ፡ በዳበሳ ፡ መጽሐ ፍን ፡ እንደሚያነብ ፡ እንደዚሁም ፡ የሚመጡት ፡ ትውልዶች ፡ ታሪክ ፡ የቀረጸውን ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ሥራ ፡ በመዳሰስ ፡ ይደር ሱበታል ፤ ይህ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ያለፉት ፡ ነገሥታት ፡ አሁንም ፡ በዘመናችን ፡ የምናያቸው ፡ ነገሥታት ፡ በሥራቸው ፡ የማንን ፡ መልክ ፡ እንደ ፡ ያዙና ፡ የማን ፡ ልጆች ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ ለማመ ዛዘን ፡ እንችላለን ።

ለምሳሌ ፤ ቀዳማዊ፡ኃይለ ሥላሴ፡ የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ራስኽን ፡ በሥራ ፡ ቅጣው ፡ የሚለውን ፡ ጽሑፍ፡ በመመልከት፡ ከደስታ፡

ይልቅ ፡ ኀዘንን ፤ ከዘፈን ፡ ይልቅ ፡ ሥራ ፡ መሥራትን ፡ ስለ ፡ መረጡ ፤ የመንግሥቱን ፡ ከባድ ፡ ሸክምና ፡ ብርቱ ፡ አላፊነት ፡ በትዕግሥት ፡ ለመ ሸከም ፡ ቻሉ ። ስለዚህ ፡ ሥራ ፡ መሥራትንና ፡ ጊዜን ፡ በቁም ፡ ነገር ፡



ላይ ፡ በማዋል ፡ ይልቁንም ፡ የመንፈሳዊ ፡ ኑሮን ፡ በመምረጣቸው ፡ ካለፉት ፡ ስመ ፡ ጥሮች ፡ ነገሥታት ፡ ማንን ፡ እንደሚመስሉ ፡ ሥራ ቸው ፡ እንደ ፡ መስተዋት ፡ ገልጦ ፡ ያሳየናል ።

በቀድሞ ፡ ዘመን ፡ መንፈሳዊንና ፡ ሥጋዊን ፡ ሥራ ፡ ለማስማማት ፡ በሥራ ፡ የደከሙትን ፡ በዘመናቸው ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡ የተሠራላቸውን ፡ ስመ ፡ ጥሮች ፡ ነገሥታት ፡ በማን ፡ መልክ ፡ በማን ፡ ታሪክ ፡ እንመስላቸው ፡ ብለን፡ ስናስብ ፤ ከፊታችን ፡ ተደቅነው ፡ የሚታዩን ፡ ጊዜ ፡ ወርቅ ፡ ነው ፡ በማለት ፡ አንዲት ፡ ሰከንድ ፡ እንኳ ፡ ሳያባክኑ ፡ የሚሠሩትን ፡ በዘመናቸው ፡ ከፍ ፡ ያሉ ፡ ሥራዎች ፡ የተሠሩላቸው ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥታችንን ፡ ለማስተያየት ፡ እናቀርባቸዋለን ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ የተሠራ ፡ ቤት ፡ መሰወር ፡ እንደማይችል ፡ ታሪክን ፡ የሚሰውር ፡ ጨለማና ፡ ጥቁር ፡ ደመና ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ አይገኝም ።

ታሪክን ፡ በመቃብር ፡ ቢደፍኑት ፡ እንኳ ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ ወጥቶ ፡ ፋናውን ፡ ሲያበራ ፡ ይታያል ።

## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

ማልሳዊ ፡ ዳዊት ፡ ለሚባል ፡ የጐንደር ፡ ንጉሥ ፡ አንድ ፡ ያዕ ቆብ ፡ የሚባል ፡ ልጅ ፡ ነበረው ።

ይህ ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ የመጨረሻ ፡ ልጁ ፡ ስለሆነ ፡ ይልቁንም ፡ በ፳፱ ዓመቱ ፡ ስለሞተ ፡ ታሪክና ፡ ሕዝብ ፡ በጣም ፡ አያውቀውም ፡ ነበር ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ካንድ ፡ መንፈሳዊ ፡ የሆነ ፡ ወጣት ፡ ልጅ ፡ መስፍን ፡ ከሚባል ፡ የስሜን ፡ ባላባት ፡ ጋራ ፡ በመንፈሳዊና ፡ በፍልስፍና ፡ ትምህርት ፡ ጊዜውን ፡ ስለሚያሳልፍ ፡ ከሕዝብ ፡ ጋራ ፡ መቀላቀልና ፡ ሰውነትን ፡ ማሳወቅ ፡ አይፈልግም ፡ ነበር ። ብዙውን ፡ ጊዜ ፡ ካባቱ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ቤተ ፡ መጻሕፍት ፡ ውስጥ ፡ ከልጅ ፡ መስፍን ፡ ጋራ ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ያለው ፡ ንግግርና ፡ ክር ክር ፡ ያደርጉ ፡ ነበር ፤ ንግግር ፡ ከመጀመራቸው ፡ በፊት ፡ ልጅ ፡ መስፍን ፡ ከቤተ ፡ መጻሕፍቱ ፡ ቤት ፡ የተሰቀለውን ፡ የሰው ፡ ጭንቅላት ፡ ዐፅም ፡ በጣቱ ፡ እያመለከተ ፤ ልዑል ፡ ሆይ ፡ ሰው ፡ መሆንህን ፡ አትርሳ ፡ ይለው ፡ ነበር ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ በፈ ረስ ፡ ተቀምጠው ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ያለውን ፡ ጨዋታ ፡ እየተጨዋ ወቱ ፡ ይናፈሱ ፡ ነበር ።

የልጅ ፡ መስፍን ፡ የመንፈስ ፡ ኃይል ፡ የልዑል ፡ ያዕቆብን ፡ ልብ ፡ ማርኮ ፡ ወደ ፡ መንፈሳዊና ፡ ወደ ፡ ፍልስፍና ፡ መንገድ ፡ መራው ።

ልዑል ፡ ያዕቆብና ፡ ልጅ ፡ መስፍን ፡ በመንፈሳዊ ፡ ጓደኝነት ፡ ስለተላመዱ ፡ መንፈሳዊና ፡ ፍልስፍና ፡ ጨዋታቸውን ፡ ለመነጋ ገር ፡ ሌሊቱ ፡ እስቲነጋ ፡ ይቸኩሉ ፡ ነበር ።

ከዕለታት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብና ፡ ልጅ ፡ መስ ፍን ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ቤተ ፡ መጻሕፍት ፡ ውስጥ ፡ ተቀም ጠው ፡ ሲጫወቱ ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ወዳጄ ፡ ልጅ ፡ መስፍን ፡ ዕድሜዬ ፡ ፲፱ ፡ ዓመት ፡ ሆነ ፡ እንደ ፡ ሕገ ፡ መንግሥታችን ፡ ደንብ ፡ አንድ ፡ የምስፍና ፡ አገር ፡ ይገኛ ፡ ለማስተዳደር ፡ ግዴታ ፡ ሊሆ

ንብኝ ፡ ነው ። እኔ ፡ በመንፈሳዊና ፡ በፍልስፍና ፡ ትምህርት ፡ የደከ ምሁ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ የገኘሁትን ፡ ከባድ ፡ ሸክም ፡ እችል ፡ ይመ ስልኻል ፤ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ የየሩሳሌም ፡ ንጉሥ ፡ ሰሎሞን ፡ ልጄ ሆይ ፡ እጅግ ፡ ጥበብ ፡ አታብዛ ፡ እንዳታዝን ፡ ያለው ፡ በኔ ፡ ደረ ሰብኝ ፤ ምክንያቱም ፡ ካንተ ፡ ከወዳጄ ፡ ጋራ ፡ እግዚአብሔር ፡ ካገናኘኝ ፡ ወዲህ ፡ ሁሉም ፡ ነገር ፡ የከንቱ ፡ ከንቱ ፡ ሆኖ ፡ ስለ ታየኝ ፡ ኅሊናዬ ፡ ይወቅሰኝ ፡ ዠመር ፡ ስለዚህ ፡ እኔ ፡ ባባቴ ፡ ቤት ፡ አዘንተኛ ፡ ሆኜ ፡ ተቀምጫለሁ ።

ወዳጄ ፡ መስፍን ፡ ሆይ ፤ ባንተ ፡ ላይ ፡ ትልቅ ፡ እምነት ፡ ስላለኝ ፡ ይህነን ፡ ከባድ ፡ ሸክምና ፡ ትልቅ ፡ አላፊነት ፡ የሚችልበትን ፡ ወይም ፡ ከእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ጭንቅ ፡ የማመልጥበትን ፡ ምክርኽን ፡ እንድትሰጠኝ ፡ እለምንኻለሁ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ልዑል ፡ ሆይ ፡ የኔ ፡ ምክር ፡ ጠቃሚ ፡ መስሎ ፡ ከታየኽ ፡ እንሆ ፡ ከባድ ፡ ሸክምኽን ፡ የሚያቀሉ ፡ ሦስት ፡ ነገሮች ፡ አቅርብልኻለሁ ፤ በነሱም ፡ የምትሠራባቸው ፡ ከሆነ ፡ በትከሻህ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ የሚጫንኽን ፡ ከባድ ፡ ሸክም ፡ ከእግርኽ ፡ በታች ፡ ወድቆ ፡ ታገኘዋለኽ ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እውነተኛ ፡ ሚዛንን ፡ በጅኽ ፡ ይዘኽ ፡ ሕዝብኽን ፡ በውነትና ፡ በፍርድ ፡ በጽድቅ ፡ ለመግዛት ፡ ትችላለኽ ፤ ምክሬም ፡ ባጭሩ ፡ ይህ ፡ ነው ።

፩ ፤ የዚህን ፡ ዓለም ፡ ከንቱ ፡ ውዳሴና ፡ ጭብጨባን ፡ መናቅ ።
፪ ፤ ከምትገዛው ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ በጥቅም ፡ አለመተሳሰር ።
፫ ፤ ለውነትና ፡ ለፍርድ ፡ ዕንቅፋት ፡ በሚሆኑ ፡ ወዳጆች ፡ አለመጠመድ ፡ ነው ።

ይህነን ፡ በውነት ፤ ፈጽመኽ ፡ ያደረግኽ ፡ እንደሆን ፡ ጻድቅ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ ደቦል ፡ በመንገድ ፡ ሲሄድ ፡ ማንንም ፡ ሰው ፡ አይፈራም ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ አንተም ፡ ባንድ ፡ እጅኽ ፡ እው ነትን ፡ በሁለተኛው ፡ እጅኽ ፡ የፍርድ ፡ ሚዛንኽን ፡ ይዘኽ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ ቀኜ ፡ ነው ፤ ማንንም ፡ አልፈራም ፡ እያልክ ፡ በቀ ናው ፡ መንገድ ፡ ትጓዛለህ ፤ እግርኽን ፡ የሐሰት ፡ ዕንቅፋት ፡ አያሰናክለውም ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ይህ ፡ በጣም ፡ የሚጠቅመኝ ፡ ምክር ፡ ሳይሆን ፡ አይቀርም ። ነገር ፡ ግን ፡ ስላንደኛው ፡ ቊጥር ፡ ትንሽ ፡

ልክራክርህ ፡ እወዳለሁ ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ሰው ፡ ከሰው ፡ ጋራ ፡ ሲኖር ፡ ወዳጁ ፡ ሳያመሰግነው ፡ ጠላቱ ፡ ሳያማው ፡ እንደ ፡ ምን፡ ይቀራል ፤ ከንቱ ፡ ውዳሴና ፡ ጭብጨባ ፡ የምትለውስ ፤ ሰው ፡ ወዳጁን ፡ ያለልክ ፡ ሲወድ ፡ ከልቡ ፡ የተረፉ ፡ ደስታዎች ፡ ናቸው ፡ ጭብጨባንና ፡ እልልታን ፡ የሚወልዱ ፤ ወንድሜ ፡ አንተ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ኀጢአት፡ ትቈጥረዋለኽ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ልዑል ፡ ሆይ ፡ እንደ ፡ ኀጢአት ፡ የቈጠርኩበትን ፡ ምክንያት ፡ መጽሐፍ ፡ ጠቅሼ ፡ ላስረዳህ ፡ እችላለሁ ። ሰሎሞን ፡ እምብዛ ፡ ምስጋና ፡ መርዝ ፡ ያለበት ፡ ማር ፡ ነው፡ ብሏል ። ደግሞ ፡ ወዳጁን ፡ በማለዳ ፡ ተነሥቶ ፡ የሚያመሰግን፡ የሚረግመው ፡ ይመስላል ፡ ይላል ። ይህነን ፡ ስንተረጕመው ፡ ምስጋና ፡ የመጥላት ፡ መሽፈኛ ፡ ነው ፤ ጭብጨባም ፡ የቂም፡ ማደናገሪያ ፡ ነው ፤ ስለዚህ ፡ አመስጋኝ ፡ አማሳኝ ፡ እንደሚባለው ፡ የሚያመሰግን ፡ ሁሉ ፡ ወዳጅ ፡ አይደለም ፡ ብትፈልግ፡ ማስረጃ ፡ የሚሆኑ ፡ ከመጻሕፍት ፡ በብዙ ፡ ለመጥቀስ ፡ እችላለሁ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ ይልቅስ ፡ ጊዜያችንን ፡ በከንቱ ፡ አናጥፋ ፡ ከዚህ ፡ የበለጠ ፡ ማስረጃ ፡ ምንም፡ አያስፈልገኝ ፤ እስኪ ፡ ደግሞ ፡ ከሚገዙት ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ በጥቅም ፡ አለመተሳሰር ፡ የሚለውን ፡ ትንሽ ፡ ብታስረዳኝ ፡ እወዳለሁ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፤ አንድ ፡ መስፍን ፡ ከሚገዛው ፡ ሕዝብ ፡ በላይ ፡ ሆኖ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ አስተዳዳሪ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ያለልክ ፡ ራሳቸውን ፡ ብቻ ፡ በመውደድ ፡ ወንድሞቻቸውን ፡ እንዳይጐዱ ፡ በውነተኛ ፡ ሚዛን ፡ አስተዳዳሪና ፡ አደላዳይ ፡ እውነተኛ ፡ ዳኛ ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ ከሚገዛው ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ በጥቅም ፡ የተሳሰረ ፡ እንደሆን ፡ እውነተኛ ፡ ሚዛን ፡ ተጁ ፡ ትወድቅና ፡ እንዳንድ ፡ ሰው ፡ ለራሱ ፡ ብቻ ፡ አሳቢ ፡ ይሆናል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ወንዞች ፡ ሁሉ ፡ ተሰብስበው ፡ ከውቅያኖስ ፡ ተቀላቅለው ፡ እንደሚጠፉ ፤ እውነትና ፡ ፍርድ ፡ ራስን ፡ በመውደድ ፡ ውስጥ ፡ ሰጥመው ፡ ይጠፋሉ ፡ እንደተባለው ፡ የእግዚአብሔር ፡ እንደራሴ ፡

ተብሎ ፡ የተሾመው ፡ መስፍን ፡ በጥቅም ፡ ሰንሰለት ፡ ተይዞ ፡ በተገዥዎች ፡ እጅ ፡ ይጐተታል ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ በውነትም ፡ ይህ ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ምክርኽ ፡ ዋና ፡ ጠቃሚዬ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ልከታተለው ፡ ይገባኛል ። እስቲ ፡ ደግሞ ፡ በሦስተኛው ፡ ቍጥር ፡ ለውነትና ፡ ለፍርድ ፡ ዕንቅፋት ፡ በሚሆኑ ፡ ወዳጆች ፡ አለመጠመድ ፡ ያልከውስ ፡ ምንድነው ።

ልጅ ፡ መስፍን ፡ ልዑል ፡ ሆይ ፡ አንድ ፡ የሕዝብ ፡ አስተዳዳሪ ፡ መስፍን ፡ ለውነትና ፡ ለፍርድ ፡ ዕንቅፋት ፡ በሚሆኑ ፡ ራሳቸውን ፡ ብቻ ፡ በሚወዱ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በማይፈሩ ፡ ወዳጆች ፡ ከተጠመደ ፡ በኋላ ፡ በሚገዛው ፡ አገር ፡ ውስጥ ፡ በመንፈስ ፡ የታሰረ ፡ እስረኛ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ለምሳሌ ፤ ይህ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሽባ ፡ በትሩን ፡ ሳይዝ ፡ እንደ ማይንቀሳቀስ ፤ እሱም ፡ በመንፈስ ፡ ያሰሩትን ፡ ወዳጆቹን ፡ ሳይጠይቅ ምንም ፡ ለመሥራት ፡ አይችልም ።

ልዑል ፡ ሆይ ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በምሥጢር ፡ የሐሰት ፡ ወሬ ፡ በማውራት ፡ ጥቅም ፡ በማሳየት ፡ ያልሆነ ፡ ነገር ፡ አስመስሎ ፡ በማስፈራራት ፡ የነሱን ፡ ጠላት ፡ የመስፍኑ ፡ ጠላት ፡ አስመስሎ ፡ በማቅረብ ፡ ይህነን ፡ በመሰሉ ፡ በእጅ ፡ በማይዳሰሱ ፡ ሰንሰለቶች ፡ እጅና ፡ እግሩን ፡ ካሰሩት ፡ በኋላ ፡ የብዙ ፡ ሕዝብ ፡ አስተዳዳሪ ፡ የሆነው ፡ መስፍን ፡ የሁለት ፡ የሦስት ፡ ሰዎች ፡ አገልጋይ ፡ ሆኖ ፡ በመንፈሱ ፡ ታስሮ ፡ ይቀመጣል ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ይህ ፡ በውነት ፡ የሚገርም ፡ ነገር ፡ ነው ፤ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ መስፍኑ ፡ ከልብ ፡ ሲወዳቸው ፡ እንደ ፡ ምን ፡ እነሱ ፡ ታሪኩን ፡ የሚያበላሽ ፡ ሥራ ፡ እሱን ፡ መከታ ፡ አድርገው ፡ ይሠሩበታል ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ርግጥ ፡ ልዑልነትኽ ፡ እንዳለው ፡ ለወዳጅ ፡ በበጎ ፡ ፈንታ ፡ ክፉ ፡ መመለስ ፡ አይገባም ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ለመስፍኑ ፡ ወዳጆቹ ፡ አይደሉም ፤ መስፍኑ ፡ ለነሱ ፡ የጥቅም ፡ መፈለጊያ ፡ ሙብራታቸው ፡ ነው ፡ እሱን ፡ ይዘው ፡ የሰውን ቤትና ፡ ንብረት ፡ ሁሉ ፡ ይበዘብዙታል ።

ልዑል ፡ ሆይ ፡ በነሱ ፡ እጅ ፡ የተያዘ ፡ መብራት ፡ እየተቃጠለ ቢያልቅ ፡ ስንኳንስ ፡ ለጊዜው ፡ ለነሱ ፡ የሥጋ ፡ መውጫ ፡ ርካባቸው ስለ ፡ ሆነ ፡ ካሰቡት ፡ ነገር ፡ በሱ ፡ መሰላልነት ፡ ይደርሳሉ ፤ እነሱም ፡ ከክፉ ፡ ሰውነታቸው ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ማውጣት ፡ ስለማይችሉ ፡ የተሰጣቸውን ፡ ሥልጣንና ፡ መብት ፡ ለራሳቸው ፡ መጠቀሚያ ፡ ለጠላታቸው ፡ መጕጃ ፡ በማድረግ ፡ ወዳጃቸውን ፡ ከሕዝብ ፡ ያጣሉታል ፡ መስፍኑም ፡ ለነሱ ፡ ጠላት ፡ መምቻ ፡ ዱላ ፡ ሆኖ ፡ የተቀደሰ ፡ ሰውነቱን ፡ ያስጠላል ።

ስለዚህ ፡ ልዑል ፡ ሆይ ፤ አንተ ፡ ከፊትኽ ፡ ያለውን ፡ እንደ ዚህ ፡ ያለ ፡ የልምድን ፡ አጥር ፡ ጥሰኽ ፡ በውነት ፡ መንገድ ፡ ብትሔድ ፡ በዘመንህ ፡ እውነትና ፡ ፍርድ ፡ ይነግሣሉ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ የተወደድኽ ፡ ወዳጄ ፡ መስፍን ፡ ሆይ ፡ ልምድ ፡ ከሰይጣን ፡ ይከፋል ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ከዚህ ፡ ልምድ ውስጥ ፡ ለመውጣት ፡ የተተበተቡ ፡ የብረት ፡ አጥሮች ፡ ስለሚገጥሙኝ ፤ እነሱን ፡ ጥሼ ፡ ለመውጣት ፡ እችል ፡ አይመስለኝምና ፡ ስለዚህ ፡ ራሴ ፡ ነፃ ፡ ሆኜ ፡ የምኖርበትን ፡ ሌላ ፡ ምክር ፡ ብትመክረኝ ፡ በጣም ፡ አመሰግንኻለሁ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ልዑል ፡ ሆይ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ እንግዲያስ ፡ ልምድን ፡ ጥሶ ፡ ለመውጣት ፡ የማትችል ፡ ከሆነ ፡ አንድ ፡ ጸሐፊ ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ የለም ፡ ቢኖር እንኳ ፡ ጥቂት ፡ የሚሻለው ፡ ካንዲት ፡ ርስቱ ፡ ላይ ፡ የዕሙና ፡ ጐጆ ፡ ሠርቶ ፡ ከሰው ፡ ርቆ ፡ የተቀመጠ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንዳለው ፡ ሁሉ ፤ ልዑልም ፡ አሳብኽን ፡ አሳንሰኽ ፡ በርስትኽ ፡ ላይ ፡ የሰላም ፡ ኑሮ ፡ ብትኖር ፡ ለልብኽ ፡ ደስታ ፡ ለመንፈስኽ ፡ ነፃነት ፡ ታገኝ ፡ ይመስለኛል ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ወይ ፡ ግሩም ፡ ሰው ፡ ምንም ፡ ፈላስፋና ፡ ሊቅ ፡ ቢሆን ፡ መሳሳቱ ፡ አይቀርም ፤ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ እኔ ፡ ሰላም ፡ ለመፈለግ ፡ ወደ ፡ ርስቴ ፡ ብሄድ ፡ ሰላምና ፡ እውነት ፡ ፍርድ ፡ ካልነገሡ ፡ ጸጥታ ፡ ከሌለ ፡ የሰላምን ፡ ኑሮ ፡ ከወዴት ፡ አገኛዋለሁ ፤ ይልቁንም ፡ በድኾች ፡ ላይ ፡ የሚደርሰውን ፡ ግፍ ፡ እኔ ፡ በገዛ ፡ እጄ ፡ ለኔም ፡ ሳደርገውና ፡ ትዳሬ ፡ ሲበላሽ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ኀዘንና ፡

ብስጭት ፡ እንደሚደርስብኝ ፡ አይሰማኝም ፤ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ ከዚ
ህስ ፡ ይልቅ ፡ የሚሻለው ፡ እኔ ፡ መሆኔ ፡ ከማይታወቅበት ፡ አገር ፡
ጠፍቼ፡ ሄጄ ፡ የምኖርበትን ፡ መንገድ ፡ ብታመለክተኝ ፡ የተሻለ፡ነው።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ እንደዚህ ፡ ያለው ፡ ነገር ፡ በምክር ፡ ሳይሆን ፡
የራሱ ፡ የቈራጥነትና ፡ የአርበኝነት ፡ መንፈስ፡ የሚሠራው ፡ ስለ ፡ ኾነ፡
ምክሬ ፡ ምንም ፡ ያግዝህ ፡ አይመስለኝም ፡ እንጂ ፡ እንዳንተ ፡ የተ
ጨነቀ ፡ ያንድ ፡ ንጉሥ ፡ ልጅ ፡ ያደረገውን ፡ የመንፈሳዊ ፡ አርበኝ
ነት ፡ ታሪክ ፡ ላጫውትህ ፡ እፈቅድ ፡ ነበር ፤ ደስ ፡ ያሰኝህ ፡ ይሆናን ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ወንድሜ ፡ መስ
ፍን ፡ ሆይ ፡ እባክህ ፡ አጫውተኝ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ አንድ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ የሚባል ፡
የንጉሥ ፡ ልጅ ፡ ነበር ፤ ይህ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ ምንም ፡
በቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ውስጥ ፡ በውጭ ፡ ሰውነቱ ፡ በደስታ ፡
መልክ ፡ ቢታይ ፡ መንፈሱ ፡ በኀዘን ፡ ይታወክ ፡ ነበር ፤ በኋሊ
ናውም ፤ ስለምንድነው ፡ ለዚህ ፡ ከንቱ ፡ ዓለም ፡ የምንደክመው ፡
አባቴና ፡ እናቴስ ፡ ለምን ፡ ለዚህ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ለሚያልፍ ፡
ዓለም ፡ ይጨነቃሉ ፡ እያለ ፡ ያዝን ፡ ይተክዝ ፡ ነበር ፤ ንጉሥ ፡
አባቱም ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ እሱ ፡ ብቻ ፡ በመሆኑ ፡ ያስብለትና ፡
ይሟሟለት ፡ ነበር ።

ከዕለታት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ንጉሡ ፤ መኳንንቱንና ፡ መሳፍ
ንቱን ፡ የጦር ፡ አለቆችንም ፡ ሰብስቦ ፡ እንደዚህ ፡ አላቸው ፤
ልጄ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ ዕቅመ ፡ አዳም ፡ አደረሰ ፤ እናንተም ፡
እንደምታውቁት ፡ በሕገ ፡ መንግሥታችን ፡ ልጅ ፡ ከሌለው ፡ ያባ
ቱን ፡ ዙፋን ፡ አይወርስም ፤ ስለዚህ ፡ ሰውና ፡ እንጨት ፡ ተሰ
ባሪ ፡ ነውና ፤ እኔ ፡ ሳልሞት ፡ ሚስት ፡ አጋብቸው ፡ ለዙፋና
ችን ፡ ዘር ፡ እንዲያስቀር ፡ በማለት ፡ አንዲት ፡ ልጅ ፡ አጭቸ
ለታለሁ ፡ እናንነተስ ፡ ምን ፡ ታስባላችሁ ።

መኳንንቱና ፡ መሳፍንቱ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፤ ሲሆን ፡ ርስዎን ፡
ለዘለዓለም ፡ ያኑርልን ፤ አሳቡ ፡ ግን ፡ እጅግ ፡ መልካም ፡ ነው ፡
ብለው ፡ አስታወቁ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ንጉሡ ፡ ልጁን ፡ ጠርቶ ፡
የተወደድኸ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ አንዲት ፡ ነገር ፡ እለምንኻለሁ ፡
እሺ ፡ በለኝ ፡ አለው ።

ገብረ ፡ ክርስቶስ ፤ አባቴ ፡ እኔ ፡ ልጅህ ፡ ከሞት ፡ የሚያ ያደርስ ፡ ነገር ፡ እንኳን ፡ ቢሆን ፡ ላንተ ፡ ታዛዥ ፡ ነኝ ።

ንጉሡ ፡ እንግዲያውስ ፡ የተወደድህ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ሚስት ፡ አግብተኽ ፡ ላያት ፡ ለቅድም ፡ አያትኽ ፡ ዙፋን ፡ ዘር ፡ አስቀር ፤ እንደምታውቀው ፡ በሕገ ፡ መንግሥቱ ፡ ውስጥ ፡ የተጻፈው ፡ ልጅ ፡ የሌለው ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ፡ ያባቱን ፡ ዙፋን ፡ አይወርስም ፤ ይህ ፡ ነው ፡ የምለምንኽ ።

ገብረ ፡ ክርስቶስ ፣ አባባ ፡ እጅግ ፡ የሚያስጨንቅ ፡ ነገር ፡ ስለ ፡ ነገርኽኝ ፡ በጣም ፡ አዘንኩ ፤ ስንኳን ፡ ለኔ ፡ ላባባም ፡ መንግሥት ፤ ለማግባት ፡ መውለድ ፡ ቢቀርባችሁ ፡ ፈቃዴ ፡ ነበር ። ምክንያቱም ፡ አባባም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ በሚነሡብኽ ፡ ጠላቶችኽ ፡ ስትናደድና ፡ ስታዝን ፤ የብዙም ፡ ሰዎች ፡ ደም ፡ በከንቱ ፡ ስታፈስ ፤ ያንተም ፡ ጠላት ፡ ያልሆኑትን ፡ ሰዎች ፡ ባለማስተዋል ፡ በሰው ፡ ጠብ ፡ ተደባልቀኽ ፡ ንጹሕ ፡ ደም ፡ ስታፈስና ፡ ስታስጨንቅ ፡ ወዲያው ፡ ስታዝንና ፡ ስትጸጸት ፡ ሁለተኛ ፡ ትመለስበት ፡ አይመስለኝም ፡ ነበር ። ኢማማም ፡ በጻዕር ፡ በገዓር ፡ ልጅ ፡ ስትወልድ ፤ ደግሞ ፡ የወለደቻቸው ፡ ልጆች ፡ ሲሞቱ ፡ በመቃብራቸው ፡ ላይ ፡ የሚደርስባትን ፡ ብርቱ ፡ ኀዘንና ፡ ሥቃይ ፡ ስመለከት ፡ ሁለተኛ ፡ ካንተ ፡ ትገናኛለች ፡ ብዬ ፡ አላስብም ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ ወዲያው ፡ እየቀጠለ ፡ ይሄዳል ፡ እንጂ ፡ አያቋርጥም ፤ ስለዚህ ፡ ይህ ፡ የቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ትዳራችን ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ወጥመድ ፡ ነው ፡ እያልኩ ፡ ሳዝን ፤ የተወደድኽ ፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡ እንደምን ፡ ከዚህ ፡ ከክፉ ፡ ወጥመድ ፡ ታገባኛለህ ፤ እባክኽ ፡ አባባ ፡ ተወኝ ፡ እያለ ፡ ከእግሩ ፡ በታች ፡ ወድቆ ፡ ይለምነው ገመር ።

አባቱም ፡ የምወድኽ ፡ ልጄ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፤ ከኀምሳ ፡ ትውልድ ፡ የሚበልጥ ፡ ሳያቋርጥ ፡ የወረደው ፡ የንጉሥ ፡ ዙፋናችን ፡ ባንተ ፡ ምክንያት ፡ የዘራችን ፡ የመንግሥት ፡ ተከታታይነት ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይጥፋ ፤ ልጄ ፡ ሆይ ፡ አያሳዝንኽምን ፡ እያለ ፡ ከእግሩ ፡ ላይ ፡ አንሥቶ ፡ ታቅፎ ፡ እያለቀሰ ፡ ይለምነው ፡ ነበር ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፤ የተወደድኽ ፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡ መዠመሪያ ፡ እንደ ፡ ነገርኩኽ ፡ ሞትም ፡ ቢሆን ፡ መቃዘዝ ፡ ስለሚገባኝ ፡ ከሞት ፡ የሚከፋ ፡ ልመናኽን ፡ አባባን ፡ ደስ ፡ ለማሰኘት ፡ ስል ፡ እሺ ፡ አገባለሁ ፡ አለው ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ንጉሡ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ዘሪኽን ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ አሸዋ ፡ እንደ ፡ ሰማይ ፡ ኮከብ ፡ ያብዛው ፡ ብሎ ፡ መርቆ ፡ በፍቅር ፡ ሳመው ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ሚስት ፡ አግብቶ ፡ ተቀመጠን ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ሚስት ፡ ማግባትን ፡ አገባ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አብረው ፡ አልተቀመጡም ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ከተጋቡ ፡ በኋላ ፡ ተፋቱ ፡ ወይስ ፡ ሞተችበት ፡ ማለትኽ ፡ ነው ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ አልተፋቱም ፤ አልሞተችበትም ፤ ልዑል ፡ ሆይ ፤ በጣም ፡ የሚገርም ፡ ታሪክ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ደኅና ፡ አድርገኽ ፡ ስማኝ ፡ ባጭሩ ፡ አጫውትኻለሁ ። የጋብቻውን ፡ ሥርዓት ፡ በሚገባ ፡ ማለዳ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሄደው ፡ ከፈጸሙ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ተመለሱ ፤ እኩለ ፡ ሌሊት ፡ ሲሆን ፡ መኳንንቱና ፡ መሳፍንቱ ፡ ወይዛዝሮቹ ፡ ሁሉ ፡ በልተው ፡ ጠጥተው ፡ ሲያንጐላጁ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ ሙሽራዪቱን ፡ እኅቴ ፡ ደክሞኛልና ፡ ከመኝታችን ፡ ቤት ፡ ገብተን ፡ እንጫወት ፡ ብሎ ፡ ጠየቃት ።

እሷም ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ብላው ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ መኝታቸው ፡ ቤት ፡ ገብተው ፡ በሩን ፡ ዘጋውና ፡ የተወደድሽ ፡ እህቴ ፡ ሆይ ፡ ዋና ፡ ምሥጢር ፡ ልነግርሽ ፡ ነውና ፡ ለማንም ፡ ላትነግሪ ፡ ስመ እግዚአብሔር ፡ ጠርተሽ ፡ ማዪልኝ ፡ አላት ።

እሷም ፡ የተማረች ፡ በመልካም ፡ አስተዳደግ ፡ ያደገች ፡ ነበረችና ፤ የተወደድክ ፡ ወዳጄ ፡ እኔ ፡ ሚስትኽ ፡ ስሆን ፡ አካልኽና ፡ ታዛዥኽ ፡ አይደለሁምን ፡ ብላ ፡ ስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጠርታ ፡ ለማንም ፡ ላትነግር ፡ ማለችለት ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ እኅቴ ፡ ወዳጄ ፡ ይህ ፡ ዓለም፡ ለኔ ፡ እንደ ፡ ትልቅ ፡ ሸክም ፡ ከብዶኛል ፤ የተወደድሽ ፡ እኅቴ ፡ ሆይ፡ በልቤ ፡ የሚሰማኝን ፡ እንዳላጫውትሽ ፡ ጊዜ ፡ የለኝም ፤ ከዚህ ፡ ካባቴ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ውስጥ ፡ ከሚያልፍ ፡ ደስታ ፡ ይልቅ ፡ የዘለዓለምን ፡ ሕይወት ፡ የሚያስከትለውን ፡ መከራ ፡ ስለ ፡ መረጥሁ ፡ ጥዬሽ፡ ወደ ፡ በረሃ ፡ መሄዴ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ሳማት ።

ሙሽራዩቱም ፤ ምነው ፡ ወዳጄ ፡ እኔን ፡ ለማን ፡ ጥለኸኝ ፡ ትሄዳለኽ ፡ እያለች ፡ ከእግሩ ፡ ላይ ፡ ተጠምጥማ ፡ ስታለቅስ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ እግሩን ፡ በእጇ ፡ አስለቅቆ ፡ በመስኮት ፡ ዘሎ ፡ ወጣና ፡ ባለጋራው ፡ እንደሚያሳድደው ፡ ሰው ፡ ሕይወት ፡ ሕይወት ፡ የዘለዓለም ፡ ሕይወት ፡ እያለ ፡ ወደ ፡ በረሃ ፡ ሩጦ ፡ ዠመር ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ የሚገርም ፡ ነገር ፡ ነው ፡ አባቱ ፡ ከሰማ ፡ በኋላ አስፈልጎ ፡ አልያዘውምን ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ አባቱ ፡ የሰማው ፡ ከነጋ ፡ በኋላ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በያለበት ፡ ቢያስፈልግ ፡ ምንም ፡ ለማግኘት ፡ አልቻለም ። ገብረ ፡ ክርስቶስም ፡ ብዙ ፡ መንገድ ፡ ከተጓዘ ፡ በኋላ ፡ ካንድ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ደረሰ ፤ እንዳጋጣሚ ፡ ይህነን ፡ ዓለም ፡ የጠሉና ፡ የንብረት ፡ ምሬት ፡ የተሰማቸው ፡ መናንያን ፡ ከሚኖሩበት ፡ ቦታ ፡ ደረሰ ። እነሱም ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ በቄራጥነት ፡ ሸሽቶ ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ ስላወቁ ፡ በገዳማቸው ፡ እንዲኖር ፡ ተቀበሉት ፤ ከዚያም ፡ ጥቂት ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ተቀመጠ ፡ ከመናንያን ፡ ጋራ ፡ ወዳጅ ፡ መሆን ፡ ዠመረ ። ነገር ፡ ግን ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ መከራን ፡ መቀበል ፡ እንጂ ፤ ወዳጅ ፡ ማበጀትን ፡ እንደ ፡ ደስታ ፡ ስለ ፡ ቈጠረው ፡ ከዚህ ፡ የሚበልጥ ፡ ነገር ፡ ማድረግ ፡ አሰበ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ከዚህ ፡ የሚበልጥ ፡ ነገር ፡ ምን ፡ ልማድረግ ፡ ይችላል ፡ ንጉሥ ፡ አባቱንና ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱን ፤ ንግሥት ፡ እናቱንና ፡ ሙሽራ ፡ ሚስቱን ፡ ጥሎ ፡ ወደ ፡ በረሃ ፡ መሄድ ፡ ቀላል ፡ ነገር ፡ መሰለውን ፤ ከዚህ ፡ የበለጠ ፡ መከራስ ፡ ቢፈልግ ፡ ከወዴት ፡ ይገኛል ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ልዑል ፡ ሆይ ፡ ይህነን ፡ ዓለም ፡ የናቀ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ ተመልሼ ፡ ካባቴ ፡ ቅጥር ፡ በራፍ ፡ ወድቄ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ባየሁበት ፡ ከተማ ፡ ከድኾች ፡ ወንድሞቼ ፡ ጋራ ፡ ግፍ ፡ ካልተቀበ

ልኩ ፡ ፍጹም ፡ ንስሓ ፡ አይሆንኝም ፡ በማለት ፡ ከባቱ ፡ ዕድሞ፡ ሥር፡ ተመልሶ ፡ ወደቀ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ እንደምን ፡ የሚገርም ፡ ነገር ፡ ሰማሁ ፤ ሰው ያለ ፡ ፈቃዱ ፡ በሚመጣበት ፡ መከራ ፡ ያዝን ፡ ይናደድ ፡ ይበሳጭ፡ ነበር ፤ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ ግን ፡ በገዛ ፡ ፈቃዱ ፡ ድኻ ፡ ችግረኛ ፡ ሆኖ ፡ ባባቱ ፡ በራፍ ፡ መከራ ፡ መቀበሉ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ከፍ፡ ያለ ፡ መሥዋዕትነት ፡ ነው ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ርግጥ ፡ በጣም ፡ የሚገርምና ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ መሥ ዋዕትነት ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ የታሪክ ፡ መገምሪያ ፡ የሆኑ ፡ ትል ልቆች ፡ ሰዎች ፡ ታሪካቸውን ፡ በድኽነትና ፡ በመከራ ፡ በችግር፡ ላይ የመሠረቱ ፡ ናቸው ፤ ያለፉትም ፡ አሁንም ፡ ወደፊት ፡ የሚወለዱት ቁም ፡ ነገራቸውን ፡ ሲገምሩና ፡ ሲጨርሱ ፡ የሕይወታቸው ፡ ታሪክ የሚታተመው ፡ በመከራቸው ፡ ብራና ፡ ላይ ፡ በደማቸው ፡ ነው ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ይህ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ ካባቱ ፡ በራፍ ፡ ወድቆ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያባቱ ፡ አገልጋዮች ፡ አያውቁትም ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ አላወቁትም ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስም ፡ ሰውነቱን፡ ለመከራ ፡ አሳልፎ ፡ በመስጠቱ ፡ በፍጹም ፡ ተለውጦ ፡ ነበርና ። ይል ቁንም ፡ በሌሊቱ ፡ ቁርና ፡ በፀሐዩ ፡ ሐሩር ፡ ምክንያት ፡ በቅምጥል፡ የኖረ ፡ ሰውነቱ ፡ ተኰሳቍሎ ፡ ፊቱ ፡ ተፍረክርኮ ፡ እጅና ፡ እግሩ ፡ ነቅቶ ፡ ቢስ ፡ ገላ ፡ የያዘው ፡ ይመስል ፡ ነበር ፡ ስለዚህ ፡ ንጉሡ ንና ፡ መሳፍንቱን ፡ መኳንንቱን ፡ ሲወጡና ፡ ሲገቡ ፡ እንዳያስጠይፍ፡ ራቅ ፡ አድርገው ፡ ከግንቡ ፡ ውጭ ፡ አስተኝተውት ፡ ነበር ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ እንደዚህ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ተጸይፎት ፡ ምግ ቡን ፡ ማን ፡ ይሰጠው ፡ ኖሯል ።

ልጅ ፡ መስፍን ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚፈራ ፡ ሰው ፡ ቍራሽ ፡ እንጀራ ፡ ይጥልለት ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የዘወትር ፡ ምግቡ ፡ ከግብር ፡ የተረፈውን ፡ ጥራጊ ፡ ከለው ፡ የጕድፍ ፡ መጣያ ፡ ይጥሉት ፡ ነበርና ፡ ያንን ፡ ከከተማ ፡ ውሾች ፡ ጋራ ፡ ይካፈል ፡ ነበር ። ይህ ፡ ሁሉ ፡ ሲሆን ፡ ልቡ ፡ በእግዚአብሔር ፡ መንፈስ ፡ የበረታ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ ባባቱ ፡ አደባባይ ፡ በድኾች ፡ ላይ ፡ የሚሠራውን ፡



ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ ካባቱ ፡ ቅጥር ፡ ውጭ ፡ ተኝቶ ።

ከድኾች ፡ ወንድሞቹ ፡ ጋራ ፡ ተካፋይ ፡ በመሆኑ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ በትዕግሥት ፡ ይቀበለው ፡ ነበር ፡ እንጂ ፤ አይመረርም ። የዘወትር ፡ ጸሎቱም ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ኀይልንና ፡ ብርታትን ፡ ስጠኝ ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ መከራ ፡ የዘለዓለምን ፡ ደስታ ፡ እንደሚያስከትል ፡ ስላመንሁ ፡ ያባቴን ፡ ደጃፍ ፡ የግፍ ፡ መቀበያ ፡ በማድረጌ ፡ እንደ ፡ ኀጢአት ፡ አትቍጠርብኝ ፤ መስቀሌን ፡ ተሸክመኽ ፡ ተከተለኝ ፡ የሚል ፡ ድምፅኽን ፡ ስለ ፡ ሰማሁ ፡ ቤተ ፡ መንግሥቴንና ፡ ንጉሥ ፡ አባቴን ፡ ንግሥት ፡ እናቴንና ፡ ሙሽራ ፡ ሚስቴን ፡ ትቼ ፡ መስቀልኽን ፡ ተሸክሜ ፡ እንሆ ፡ ካባቴ ፡ ግንብ ፡ ውጭ ፡ ከድኾች ፡ ወንድሞቼ ፡ ጋራ ፡ መከራን ፡ እሳተፋለሁ ፤ ቢሆንም ፡ እኔ ፡ ሥራ ፡ ፈት ፡ ባሪያ ፡ ስለ ፡ ሆንኩ ፡ በሥራዬ ፡ ሳልመካ ፡ ባንተ ፡ ቸርነትና ፡ ጸጋ ፡ ብቻ ፡ እታመናለሁ ፡ እያለ ፡ ዘወትር ፡ በግንባሩ ፡ ተደፍቶ ፡ ይለምን ፡ ነበር ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ዐጥንት ፡ ሰብሮ ፡ የሚገባ ። ታሪክ ፡ ነው ፡ እባክኽ ፡ መከራውን ፡ እያየ ፡ ብዙ ፡ ዓመት ፡ ተቀመጠን ፤

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ብዙ ፡ ዓመት ፡ እንኳ ፡ አይደለም ፡ ቢሆንም ፡ ጥቂቶች ፡ ዓመቶች ፡ ከቈየ ፡ በኋላ ፡ በብርድና ፡ በችጋር ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ መከራ ፡ ታሞ ፡ ሞተ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ እንደዚሁ ፡ ሳይታወቅ ፡ ባባቱ ፡ ደጃፍ ፡ ከጕድፍ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ቀረን ፤ እንዴት ፡ ያሳዝናል ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ሳይታወቅ ፡ አልቀረም ፡ ልዑል ፡ ሆይ ፤ በሞተ ፡ ማግሥት ፡ አገፋሪው ፡ በጣም ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ግንብ ፡ ቀርቧልና ፡ ራቅ ፡ ካለ ፡ ቦታ ፡ ወስዳችሁ ፡ አስተኙት ፡ ብሎ ፡ ትእዛዝ ፡ ስለ ፡ ሰጠ ፡ የታዘዙት ፡ ሰዎች ፡ ለማንሣት ፡ ቢሄዱ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ ዐይኑን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አቅንቶ ፡ እየተመለከተ ፡ አንዲት ፡ ወረቀት ፡ በእጁ ፡ ይዞ ፡ ሞቶ ፡ አገኙት ። መልክተኞቹም ፡ ደንግጠው ፡ ወረቀቱን ፡ ከእጁ ፡ ተቀብለው ፡ ከመቃብሩ ፡ በፊት ፡ ለማሳየት ፡ ተመለሱ ።

መልክተኞቹም ፡ ላጋፋሪው ፡ ክቡር ፡ ሆይ ፡ ከቅጥሩ ፡ ውጭ ፡ የወደቀውን ፡ ድኻ ፡ አንሥተን ፡ እልፍ ፡ ለማድረግ ፡ ታዘን ፡ ሄደን ፡ ነበር ፤ እንደ ፡ ደረስን ፡ ለማንሣት ፡ ብንጠጋ ፡ ሞቶ ፡ ይህነን ፡ ወረቀት ፡ በእጁ ፡ ይዞ ፡ አገኘነው ፤ ስለዚህ ፡ ከመቃብሩ ፡ በፊት ፡ ወረቀቱን ፡ ለማሳየት ፡ መጣን ፡ አሉት ።

አጋፋሪውም ፡ ወረቀቱን ፡ ገልጦ ፡ ቢያየው ፡

ግርማዊ ፡ አባቴ ፤ ግርማዊት ፡ እናቴ ፡ በድያችኋለሁና ፡ ይቅር ፡ በሉኝ ፡ ይልቁንም ፡ እኔ ፡ ከፍ ፡ ያለውን ፡ ሰማያዊ ፡ ደስታ ፡ ለማግኘት ፡ ስል ፡ ደጃችሁን ፡ የግፍ ፡ መቀበያ ፡ ስላደረግሁት ፡ ላባባና ፡ ለማማ ፡ ለዘመዶቼም ፡ ሁሉ ፡ መራራ ፡ ኀዘን ፡ እንደ ሚሆን ፡ ዐውቀዋለሁና ፡ ይቅር ፡ በሉኝ ፡ ለኔ ፡ ግን ፡ ከሁሉ ፡ የሚ በልጥ ፡ ደስታዬ ፡ ነው ። አባባም ፡ እማማም ፡ ዕጮኛዬም ፡ እኅቶ ቼም ፡ ወንድሞቼም ፡ ዘመዶቼም ፡ ስለኔ ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፤ እኔ ፡ በዚህ ፡ ቀን ፡ ያረፍሁ ፡ ልጃችሁ ፡ ገብረ ፡ ክርስቶስ ፡ ነኝ ፡ የሚል ፡ ሆኖ ፡ ተገኘ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አጋፋሪው ፡ በብዙ ፡ ደንግጦ ፡ ሬሳውን ፡ በሚያውቁት ፡ ሰዎች ፡ አስመርምሮ ፡ ምልክት ፡ ካገኘበት ፡ በኋላ ፡ ለመኳንንቱና ፡ ለመሳፍንቱ ፡ አማክሮ ፡ ለንጉሡና ፡ ለንግሥቲቱ ፡ ለዘመዶቹ ፡ ሁሉ ፡ አርድተው ፡ በእጁ ፡ የተገኘውን ፡ ወረቀት ፡ አነበቡላቸው ።

ልዑል ፡ ሆይ ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ የተደረገው ፡ ኀዘን ፡ ምን ፡ ይሆን ፤ ልዩ ፡ ነገር ፡ ሳይሆን ፡ አይቀርም ።

እንግዴህ ፡ ሌላ ፡ ጨዋታ ፡ ይሻል ፡ ይመስለኛል ፡ ይህ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ የሚል ፡ ታሪክ ፡ አይመስለኝም ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ የተወደድኽ ፡ ወንድሜ ፡ ልጅ ፡ መስፍን ፤ ይህ ፡ ታሪክ ፡ ሥጋ ፡ ደካማ ፡ በመሆኑ ፡ ማባባያና ፡ ማታለያ ፡ ከንቱ ፡ ውዳሴ ፡ ስለሚፈልግ ፡ ለሥጋዊ ፡ ሰው ፡ ደስ ፡ አይለውም ፡ ይሆናል ፤ ለመንፈሳዊ ፡ ሰው ፡ ግን ፡ ከዚህ ፡ የሚበልጥ ፡ ደስ ፡ የሚል ፡ ታሪክ ፡ አይገኝም ። ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ የዚህን ፡ የንጉሥ ፡ ልጅ ፡ የምግባርና ፡ የሃይማኖት ፡ የአርበኝነት ፡ ታሪክ ፡ መስማት ፡ ለቤተ ፡ መንግሥት ፡ ዘሮች ፡ ሁሉ ፡ ትልቅ ፡ ኵራት ፡ ነው ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ከኪሱ ፡ ሰዓቱን ፡ አውጥቶ ፡ ልዑል ፡ ሆይ ፡ ዐሥራ ፡ ሁለት ፡ ሰዓት ፡ ሆነ ፡ ዛሬ ፡ ማታ ፡ ስለ ፡ ዘውዱ ፡ በዓል ፡ ጌታዬ ፡ ልብስኽን ፡ መለወጥ ፡ አለብኽና ፡ እንሂድ ፡ እኔም ፡ ተጠ ርቻለሁ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ሳናውቀው ፡ እንዴት ፡ ጊዜው ፡ ሄዷል ፤ ወንድሜ ፡ ይህነን ፡ ታሪክ ፡ ደግሞ ፡ እንደግመዋለን ፡ እንጂ ፡ እንደዚህ ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ የምንተወው ፡ አይደለም ፤ እንሂድ ፡ ልብሳችንን ፡ እንለውጥ ፡ አንተም ፡ እንደ ፡ ምንም ፡ ብለኽ ፡ በበዓሉ ፡ ውስጥ ፡ ካጠገቤ ፡ እንድትሆን ፡ ተባብለው ፡ ከሌሊቱ ፡ ባራት ፡ ሰዓት ፡ ስለሚደረገው ፡ የዘውድ ፡ በዓል ፡ ልብሳቸውን ፡ ለመለወጥ ፡ ወደየቤታቸው ፡ ሄዱ ።

ምዕራፍ ፡ ፱ ።

ማልሳዊ ፡ ዳዊት ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ተወላጆች ፡ ጋራ ፡ በ፱ ፡ ሰዓት ፡ የራት ፡ ግብዣ ፡ ካደረጉ ፡ በኋላ ፡ ባራት ፡ ሰዓት ፡ በዓል ፡ ከሚደረግበት ፡ አዳራሽ ፡ ከንግሥቲቱ ፡ ጋራ ፡ በዙፋናቸው ፡ ተቀምጠው ፡ ወዲያው ፡ የንጉሡ ፡ የእልፍኝ ፡ አስከልካይ ፡ የንጉሡን ፡ ቤተ ፡ ሰቦች ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያንን ፡ አለቆች ፡ መኳንንቱንና ፡ መሳፍንቱን ፡ የጦር ፡ አለቆችንና ፡ ወይዛዝሮችን ፡ በየማዕርጋቸው ከስቀመጠ ፡ በኋላ ፡ የያገሩ ፡ ስመ ፡ ጥሮች ፡ ዘፋኞች ፡ በተራ ፡ በተራ ፡ እየገቡ ፡ ሥፍራቸውን ፡ ያዙ ።

ዘፋኞቹም ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ የተመለከቱት ፡ ናቸው ።

| | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|
| ፩ | ፤ | የጎንደር ። | ፮ | ፤ | የሱማሌ ። |
| ፪ | ፤ | የትግሬ ። | ፯ | ፤ | የሻንቅላ ። |
| ፫ | ፤ | የሸዋ ። | | | |
| ፬ | ፤ | የወሎ ። | ፰ | ፤ | የአዳል ። |
| ፭ | ፤ | የየጁ ። | ፱ | ፤ | የጋላ ። |

ከነዚህም ፡ በቀር ፡ የሱዳን ፡ የልዩ ፡ ልዩ ፡ አገሮች ፡ ዘፋኞች ፡ ነበሩ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አንድ ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መምህር ፡ ተነሥቶ ፡ ግርማዊ ፡ ሆይ ፡ በፊትዎ ፡ ሞገስ ፡ አግኝቼ ፡ እንደሆን ፡ በዓሉን ፡ እኔ ፡ ልክፈት ፡ ብሎ ፡ ለመነ ። ንጉሡም ፡ ፈቀዱለት ፡ መምህሩም ፡ እንደዚህ ፡ ብሎ ፡ ተቀኘ ።

ሰላም ፡ እ·ብል ፡ ለሰ·ብአ ፡ አዘዘ ፡ ፀረ ፡ ቅባት ።
ወዕፌጌሆመ·ኒ ፡ ዕጨጌነት ፡ ከሚስት ።

ሶበ ዕንቢ ፡ ለእግዜር ፡ ይቤሉ ፡ ወዕንቢ ፡ ለንጉሥ ፡ ዳዊት ፡
ጃዊ ፡ ቀደደ ፡ ሆድሆዶሙ ፡ ወሰለበሙ ፡ እስከ ፡ ሕንብርት ፡
ወበእንተ ፡ ዝ ፡ ይቤሎ ፡ በኀምሳ ፡ ዓመት ፡ ግዝረት ፡
ብሎ ፡ ሲጨርስ ፡ በብዙ ፡ ተጨበጨበ ።

ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ዘፋኞች ፡ እንደያገራቸው ፡ ልምድና ፡ ዜማ ፡ ሲዘምሩና፡ሲዘፍኑ፡ለሰሚ ፡ እጅግ፡የሚያስደንቅና ፡ ደስ፡የሚያሰኝ ፡ ነበር ። ይልቁንም ፡ ዘፋኞቹ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ የያገራቸውን ፡ ልብስ ፡ ለብሰው ፡ ሲታዩ ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ መብራት ፡ ጋራ ፡ አበባ ፡ የፈነዳ ፡ ይመስል ፡ ነበር ፤ እንደዚሁ ፡ በተራ ፡ በተራ ፡ ከንጉሡና ፡ ከንግሥቲቱ ፡ አጠገብ ፡ እየቀረቡ ፡ ከዘፈኑ ፡ በኋላ ፡ አንዲት ፡ የጐንደር ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ዘፋኝ ፡ ወይዘሮ ፡ አታላይ ፡ የምትባል ፡ ብዙ ፡ የሚያምሩ ፡ ልጃገረዶች ፤ ከራሳቸው ፡ ላይ ፡ ዐደይ ፡ አበባ ፡ ያሰሩ ፡ ከወደ ፡ ኋላዋ ፡ አስከትላ ፡ እየዘፈነች ፡ ወደ ፡ ንጉሡና ፡ ወደ ፡ ንግሥቲቱ ፡ መጣች ። ወዲያው ፡ አንዱ ፡ መኰንን ፡ ብድግ ፡ ብሎ ፡ እንደዚህ ፡ ዝፈኚ ፡ አለና ፡ ግጥም ፡ ነገራት ፤ እሷም ፡ ባማረ ፡ ዜማ ፡ ተቀበለችው ።

ዳዊት ፡ ከዙፋን ፡ ላይ ፡ ቢያበራ ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡
ዓለም ፡ እየሞቃት ፡ አበቀለች ፡ ሲሳይ ።

አሁንም ፡ በኛ ፡ ዕድሜ ፡ ኋላም ፡ በሚመጡት ፡
አራተኛ ፡ የለም ፡ ካንተ ፡ ወዲያ ፡ ዳዊት ።

ኀዘንና ፡ ለቅሶ ፡ ጠፋ ፡ ከጐንደር ፡
ዳዊት ፡ በበገና ፡ መዝሙር ፡ ሲዘምር ።

የቀድሞ ፡ ነገሥታት ፡ አለፉት ፡ ባዘን ፡
ንጉሡ ፡ ባንተ ፡ ቤት ፡ ተድላና ፡ ዘፈን ።

የሮፓ ፡ ነገሥታት ፡ ካንተ ፡ በተማሩ ፡
የዚህን ፡ ዓለም ፡ ጣዕም ፡ እንዲመረምሩ ።

ያለም ፡ ከባድ ፤ ሸክም ፡ እንዳይሰማው ፡
ደስታን ፡ የያዘ ፡ ዳዊት ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ከለፉት ፡ ነገሥታት ፡ ተዘምዶም ፡ የለኽ ፡
ዳዊት ፡ አባትኽ ፡ ነው ፡ ዕዝራ ፡ ወንድምኽ ።

ለኔ ፡ እንደሚመስለኝ ፡ እንደሚሰማኝ ፡
ካንት ፡ ወዲህ ፡ ደስታ ፡ መቼም ፡ አይገኝ ።

ብላ ፡ ዘፈኗን ፡ ስትጨርስ ፡ ማልሳዊ ፡ ዳዊት ፡ በደስታ ፡ ተነክቶ ፡ ብድግ ፡ ብሎ ፤

የዘፈኗን ፡ ጣዕም ፡ የማያውቅ ፡ ሰው ፡
ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ኑሮ ፡ የተለየ ፡ ነው ፤
ሊቈጠር ፡ ይገባል ፡ እንደ ፡ ሞተ ፡ ሰው ፡

ብሎ ፡ ሲጨርስ ፡ የተቀመጡት ፡ መኳንንትና ፡ መሳፍንት ፡ ባንድነት ፡ ቢያጨበጭቡ ፡ የቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ አዳራሽ ፡ የተሠነጠቀ ፡ መሰለ ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ አገጩን ፡ በእጁ ፡ ይዞ ፡ በኀዘን ፡ ሲመለከት ፡ ያባቱን ፡ ዘፈንና ፡ የሕዝቡን ፡ ጭብጨባ ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ራሱ ፡ በኀዘን ፡ ዞሮ ፡ ከወንበሩ ፡ ላይ ፡ ተወርውሮ ፡ በግንባሩ ፡ ከመሬት ፡ ወደቀ ።

ማልሳዊ ፡ ዳዊትና ፡ ንግሥቲቱ ፡ ደንግጠው ፡ ከዙፋናቸው ፡ ተነሥተው ፡ የልጃቸውን ፡ አንገት ፡ አቅፈው ፡ ያለቅሱ ፡ ነበር ። ሊቀ ፡ መኳሱና ፡ የእልፍኝ ፡ አስከልካዩ ፡ ቶሎ ፡ ብለው ፡ መኳንንቱንና ፡ መሳፍንቱን ፡ ዘፋኞቹን ፡ አስወጡ ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የንጉሡ ፡ ቤተ ፡ ሰቦችና ፡ ሊቀ ፡ መኳሱ ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብን ፡ ተሸክመው ፡ ወደ ፡ መኝታው ፡ ቤት ፡ ወስደው ፡ አስተኙት ። ሊቀ ፡ መኳሱ ፡ ብቻ ፡ ካጠገቡ ፡ ተቀምጦ ፡ ይጠብቀው ፡ ነበር ፤ እኩል ፡ ሰዓት ፡ ያኽል ፡ ምንም ፡ ሰው ፡ ሳያውቅ ፡ አእምሮው ፡ ጠፍቶ ፡ ያንቋርር ፡ ነበር ፤ ከጥቂት ፡ ጊዜ ፡ በኋላ ፡ ከእንቅልፉ ፡ እንደሚነቃ ፡ ሰው ፡ ብንን ፡ ብሎ ፡ ሊቀ ፡ መኳሱም ፡ ወንድሜ ፡ ምን ፡ ሆኜ ፡ ኖሯል ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ፤ ሊቀ ፡ መኳሱን ፡ ልዑል ፡ ሆይ ፡ ጥቂት ፡ አሞኽ ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ ግን ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ዳንክ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ አሁንስ ፡ ትዝ ፡ አለኝ ፡ የታመምኩበትንም ፡ ነገር ፡ ዐወቅሁት ፡ እያለ ፡ የመረረ ፡ ለቅሶ ፡ ያለቅስ ፡ ዠመር ፤ ወዲያው ፡ ሊቀ ፡ መኳሱን ፡ ወንድሜ ፡ ልጅ ፡ መስፍንን ፡ አምጣልኝ ።

ሊቀ ፡ መኳሱ ፤ ልዑል ፡ ሆይ ፡ መዠመሪያ ፡ ግርማዊ ፡ አባትኽ ፡ ተጨንቀዋልና ፡ የደኅንነትኽን ፡ ወሬ ፡ ነግሬያቸው ፡ መጥተው ፡ ይዩኽ ፤ ልጅ ፡ መስፍንንም ፡ አምጥቼ ፡ ካንዱ ፡ ክፍል ፡ አስቀምጠ

ሙና ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ሲወጡ ፡ ይገባልኻል ፡ ብሎት ፡ ለንጉሡ ፡
ለመንገር ፡ ወጣ ፤ ከጥቂት ፡ ጊዜ ፡ በኋላ ፡ አንድ ፡ አሽከር ፡ በሩን ፡
ከፍቶ ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሥ ፡ መጡ ፡ ሲል ፡ ንጉሡ ፡ ገብተው ፡ ከል
ጃቸው ፡ አጠገብ ፡ ከወንበር ፡ ላይ ፡ ተቀምጠው ፡ በእጃቸው ፡ እየ
ዳሰሱ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ እንደ ፡ ምንድነኽ ፡ በጣም ፡ ተሽሎኻልን ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ አባባ ፡ በጣም ፡ በጎ ፡ ነኝ ።

ማልሳዊ ፡ ዳዊት ፤ እስኪ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ሁኑ ፡ ከልጄ ፡ ጋራ ፡
ልነጋገር ።

ሊቀ ፡ መኳሱና ፡ ከንጉሡ ፡ ጋራ ፡ የመጡት ፡ አሽከሮች ፡ ወጥ
ተው ፡ በሩን ፡ ዘጉት ።

ዐፄ ፡ ዳዊት ፤ የተወደድኽ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ አይቼብኽ ፡ የማ
ላውቀውን ፡ በሽታ ፡ በማየቴ ፡ በጣም ፡ አዘንኩ ፤ በምን ፡
ምክንያት ፡ ይመስልኻል ፡ እንደዚህ ፡ ድንገት ፡ የሚጥል ፡ በሽታ ፡
የወደቀብኽ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ግርማዊ ፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡ ይህ ፡ በሽታ ፡ ለኔም ፡
አዲስ ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እንደሚመስለኝ ፡ ትናንትና ፡ ማታ ፡
በተደረገው ፡ በዓል ፡ አዲስ ፡ የሚያሳዝን ፡ ስሜት ፡ ተሰምቶ ፡
ነበር ። በመዠመሪያ ፡ አባባን ፡ ደስ ፡ በሚያሰኝ ፡ ከንቱ ፡ ውዳሴ ፡
ዘፈን ፡ በመውደድኽ ፡ ሲያመሰግኑኽ ፡ ትከሻዬን ፡ ቀፎኝ ፡ ጥልቅ ፡
የሆነ ፡ ኀዘን ፡ ሳዝን ፡ ወዲያው ፡ አባባ ፡ በከንቱ ፡ ውዳሴ ፡ ምክን
ያት ፡ በደስታ ፡ ተነክተኽ ፡ የተሸከምከው ፡ ከባድ ፡ ሸክምና ፡
አላፊነት ፡ ሳይሰማህ ፡ ተነሥተኽ ፡ በግጥም ፡ ደስታኽን ፡ ስት
ገልጥ ፡ በሰማሁ ፡ ጊዜ ፡ ትከሻዬን ፡ ጨመደደኝ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡
መኳንንቱና ፡ መሳፍንቱ ፡ እየመላለሱ ፡ ሲያጨበጭቡ ፡ በሰማሁ ፡
ጊዜ ፡ ‹ወዳጁን ፡ በማለዳ ፡ ተነሥቶ ፡ የሚያመሰግን ፡ የሚረግ
መው ፡ ይመስላል› ፤ እምብዛ ፡ ምስጋና ፡ መርዝ ፡ ያለበት ፡ ማር ፡
ነው ፡ የተባለው ፡ ትዝ ፡ ሲለኝ ፤ አባባን ፡ ምን ፡ ያኽል ፡ የሚያ
ታልሉ ፡ የወዳጅ ፡ ጠላቶች ፡ እንዳሉብኽ ፡ ሳስብ ፡ ራሴን ፡ አዞ
ረኝ ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ እሰማይ ፡ እምድር ፡ የሆንኩ ፡ አላውቅም ፡
ወደቅሁ ፡

ማልሳዊ ፡ ዳዊት ፤ የተወደድኽ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ የሚወደኝ ፡ ሕዝቤ ፡ የልቡን ፡ ፍቅር ፡ በጭብጨባ ፡ ቢገልጥልኝ ፡ አንተ ፡ በዚህ ፡ ምክንያት ፡ ይህነን ፡ ያኽል ፡ በሽታ ፡ የሚጥል ፡ ነገር ፡ በምን ፡ ምክንያት ፡ ደረሰብኽ ፡ አይገባኝም ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ አባባ ፡ ጭብጨባ ፡ መውደድ ፡ አይደለም ፤ የቂም ፡ ማደናገሪያ ፡ ነው ፡ እንጂ ብትፈቅድልኝ ፡ ለምሳሌ ፤ የሕዝብ ፡ ጭብጨባ ፡ ከንቱ ፡ መሆኑን ፡ ላስረዳኽ ፡ እችላለሁ ።

ጐርጐራ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ያስደበደብኳቸው ፡ የተዋሕዶ ፡ ሃይማኖት ፡ ካህናት ፡ ደም ፡ እንደ ፡ አቤል ፡ ደም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሲጮኽ ፡ ዛሬ ፡ በተደረገው ፡ በዓል ፡ ውስጥ ፡ አንዱ ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አለቃ ፡ በቅኔ ፡ ሲያላግጥብኽ ፡ የነበረው ፡ በውነት ፡ መውደዱ ፡ ነውን ፤ የተሰበሰቡት ፡ መሳፍንትና ፡ መኳንንት ፡ ሲያጨበጭቡ ፡ የነበሩት ፡ መጥላታቸውን ፡ በከንቱ ፡ ውዳሴ ፡ ሸፍነው ፡ እንዳላገጡብኽ ፡ አይሰማኽምን ፤ ይህነን ፡ መውደድ ፡ ትለዋለኽን ። አባባ ፡ በውነት ፡ ልንገርኽ ፡ ወዳጅ ፡ የለኽም ፡ ወዳጅኽ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነበር ፤ በደም ፡ ተለያይታችኋል ፤ እንግዴህ ፡ ይህነን ፡ ያለፈውን ፡ ነገር ፡ እንተወውና ፡ የዚህን ፡ ድንገት ፡ የደረሰብኝን ፡ በሽታ ፡ እንነጋገር ።

ዐፄ ፡ ዳዊት ፤ ብዙ ፡ ተክዞ ፡ ከቈየ ፡ በኋላ ፡ እሺ ፡ ያለፈውን ፡ እንተወውና ፡ ያሁኑን ፡ እንነጋገር ፤ የዛሬ ፡ ዓመት ፡ በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ በዓል ፡ ውስጥ ፡ ነበርኽ ፤ ምነው ፡ እንደዚህ ፡ አልተሰማኽ ፡ ዛሬ ፡ ምን ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ አገኘኽ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ መጻሕፍት ፡ ባለመመልከቴ ፡ ከዚያ ፡ በዓልና ፡ ዘወትር ፡ ካባባ ፡ ቤት ፡ ከሚደረገው ፡ ዘፈን ፡ የበለጠ ፡ ደስታ ፡ ያለ ፡ አይመስለኝም ፡ ነበር ፤ ዛሬ ፡ ግን ፡ ዐይኔ ፡ ማየት ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ማስተዋልንም ፡ ጨመረ ። ስለዚህ ፡ አባባ ፡ ይህን ፡ ያኽል ፡ ከባድ ፡ ሸክም ፡ ተሸክመኽ ፡ ሳይሰማኽ ፡ በሕዝብህ ፡ ፊት ፡ መዝፈን ፡ ሕዝብህንም ፡ አመስጋኝ ፡ አማሳኝ ፡ እንደሚባለው ፡ መጥላታቸውን ፡ በማጨብጨብ ፡ ሸፍነው ፡ ሲያላግጡብኽ ፡ በማየቴ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ በሽታ ፡ ወደቀብኝ ።

ዐጺ ፡ ዳዊት ፡ ልጄ ፤ ሆይ ፡ በውነት ፡ የሸክሜ ፡ ክብደት ፡ ሳይሰማኝ ፡ ቀርቶ ፡ የዘፈንኩ ፡ ይመስልኻልን ። ለምሳሌ ፤ አንድ ፡ ትልቅ ፡ ሸክም ፡ የተሸከመ ፡ ሰው ፡ ለድካሙ ፡ መደገፊያና ፡ ለክብደቱ ፡ ማጽናኛ ፡ እንደሚያንጐራጕር ፡ አታውቁምን ፤ በውነት ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ይመስልኻል ፡ የሚዘፍነው ፤ ደግሞስ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ በጣም ፡ የመረረ ፡ ኀዘን ፡ የወደቀበት ፡ ጊዜ ፡ ልቅሶው ፡ ወደ ፡ ደረቅ ፡ ሣቅ ፡ እንደሚለወጥ ፡ አታውቅምን ። ልጄ ፡ ሆይ ፡ ዕንባ ፡ የቅምጥሎች ፡ ኀዘን ፡ ነው ፤ ዋናው ፡ ኀዘን ፡ ሲመጣ ፡ ያሥቃል ፡ ያዘፍናል ፤ እንደዚሁም ፡ ሁሉ ፡ የኔ ፡ ዘፈን ፡ መውደድ ፡ የጽኑ ፡ ሸክሜ ፡ ማጽናኛ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የደስታ ፡ አይደለም ።

ልውል ፡ ያዕቆብ ፤ አባባ ፡ ርግጥ ፡ እንዳልከው ፡ ይሆን ፡ ይሆናል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የግብዞች ፡ ሰዎች ፡ ኀዘን ፡ ማጽናኛ ፡ ልምድ ፡ ሆነው ፡ የሰውን ፡ ኑሮና ፡ ሕይወት ፡ የሚያበላሹ ፡ ዋና ፡ ኀጢአቶች ፡ ናቸው ።

ለምሳሌ ፤ እንደ ፡ ትንባኾ ፡ መጠጥ ፤ ወደ ፡ ሴት ፡ እንደ ፡ መሄድ ፡ ኀዘንን ፡ ያጽናኑ ፡ የሐሳብንም ፡ ሸክም ፡ ያቃልሉ ፡ ይሆናል ። ነገር ፡ ግን ፡ በጣም ፡ ሲለመዱ ፡ የነሱ ፡ ዝምድና ፡ ያንስና ፡ የበለጡ ፡ መርዝ ፡ የሆኑ ፡ ነገሮች ፡ ይተኩበታል ። ለምሳሌ ፤ እንደ ፡ ዕፀ ፡ ፋርስ ፡ ሐሺሽ ፡ ኦፒዮም ፡ ይህነን ፡ የመሳሰሉ ፡ የሰውን ፡ ልጅ ፡ ሕይወትና ፡ የመንፈስ ፡ ዕውቀት ፡ የሚያጠፉ ፡ ናቸው ። እንደዚህም ፡ ሁሉ ፡ ያባባ ፡ ኀዘን ፡ ማረሳሻዎች ፡ ዘፈንና ፡ ከንቱ ፡ ውዳሴ ፡ መውደድ ፡ ከነዚሁም ፡ ተራ ፡ ውስጥ ፡ የሚገኙ ፡ ሳይሆኑ ፡ አይቀሩም ። እንደ ፡ ንጉሡ ፡ አጐንብሱ ፡ እንደሚባለው ፡ ያባባ ፡ ዘፈን ፡ መውደድ ፡ ላንተ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ሕዝቡንም ፡ ከምግባርና ፡ ከሕግ ፡ ውጭ ፡ ያሚያደርግና ፡ ያለልክ ፡ ገንዘብን ፡ የሚያስወድድና፡ የሚያስባክን ፡ የደስታና ፡ የዘፈንን ፡ ሰዎች ፡ አርነት ፡ የሚያወጣ ፡ ይሆናል ። የዚህም ፡ ጓዝ ፡ ዝሙት ፤ ስርቆት ፤ ማታለል ፤ በመጨረሻውም ፡ መግደል ፡ ይህነን ፡ የመሳሰሉ ፡ የሕዝብን ፡ ምግባር ፡ የሚያበላሹ ፡ ነገሮች ፡ ሁሉ ፡ ካባባ ፡ ዘፈን ፡ መውደድ ፡ ውስጥ ፡ የሚፈልቁና ፡ ሕዝቡን ፡ የሚመርዙ ፡ ናቸው ። አባባ ፡ እባክኽን ፡ ጊዜ ያቸውን ፡ በቁም ፡ ነገርና ፡ በሥራ ፡ የሚያሳልፉትን ፡ ያያቶችኽን ፡ የሕይወት ፡ ታሪክ ፡ ተመልከት ፡ እያለ ፡ ያለቅስ ፡ ዠመር ።

ዐፄ ፡ ዳዊት ፤ አገጩን ፡ እጁ ፡ ላይ ፡ አድርጎ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ተክዞ ፡ ከቈየ ፡ በኋላ ፡ የተወደድኽ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ያያቶቼ ፡ ታሪክ ምንድነው ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ አባባ ፡ ያያቶችኽ ፡ ታሪክ ፡ ብዙ ፡ ነው ። ከብዙውም ፡ በጥቂቱ ፡ ያንዱን ፡ አባትኽን ፡ ታሪክ ፡ አስረዳኻለሁ ።

ጻድቁ ፡ ዮሐንስ ፡ የሚባለው ፡ ስመ ፡ ጥሩው ፡ የጐንደር ፡ ንጉሥ ፡ በሕይወቱ ፡ ሁሉ ፡ ዋና ፡ ሥራው ፡ የሕዝቡን ፡ ምግባርና ፡ ሃይማኖት ፡ መቈጣጠርና ፡ ጊዜውን ፡ በሥራ ፡ ማሳለፍ ፡ ነበር ። ዘወትር ፡ ለሕዝቡ ፡ ምሳሌ ፡ ለመሆን ፡ በቁም ፡ ነገር ፡ መልክ ፡ ይታይ ፡ ነበር ። ዋኖቹ ፡ የመንግሥቱ ፡ ምልክቶች ፡ የውነት ፡ ፍርድና ፡ ራስን ፡ አለመውደድ ፡ ነበሩ ፤ ትላንት ፡ አባባን ፡ በዘፈን ፡ የቀድሞው ፡ ነገሥታት ፡ አለፉት ፡ ባዘን ፤ ነገሡ ፡ ባንተ ፡ ቤት ፡ ተድላና ፡ ዘፈን ብለው ፡ በሕዝብኽ ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ሰደቡኽ ፡ ሳይሆን ፡ በጻድቁ ፡ ዮሐንስ ፡ ቤት ፡ እውነትና ፡ ጽድቅ ፡ ፍርድ ፡ ነግሠው ፡ ነበር ። ይህ ፡ ሁሉ ፡ ሲሆን ፡ ጻድቁ ፡ ዮሐንስ ፡ አገልግሎቱ ፡ ላገሩ ፡ እንደ ፡ማይ ጠቅም ፡ ዋጋ ፡ እንደማያወጣ ፡ ስለቈጠረው ፡ ይልቁንም ፡ ትዳሩ ፡ የተወሰነ ፡ ስለሆነ ፡ የኔ ፡ አገልግሎት ፡ የሕዝቤን ፡ ገንዘብ ፡ ለመ ብላት ፡ የሚበቃ ፡ አይደለም ፡ በማለት ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ውስጥ ፡ ሰሌን ፡ እየሠራ ፡ ይሸጥና ፡ በሱው ፡ እንጀራ ፡ እያስገዛ ፡ ይበላ ፡ ነበር ። አባባ ፡ ይህነን ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ ባይቻ ልኽ ፡ እንኳ ፡ ከቤተ ፡ መንግሥታችን ፡ የትውልድ ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ ዘፋኙ ፡ ዳዊት ፡ መባልን ፡ ብትፍቅልን ፡ በጣም ፡ አመሰግ ንኻለሁ ። በተቀረ ፡ እኔ ፡ በኀዘን ፡ በሽታ ፡ ብሞት ፡ አባቴ ፡ በግድ በኀዘን ፡ ምክንያት ፡ ዘፈንኽን ፡ ሳትተው ፡ አትቀርም ። ነገር ፡ ግን ፡ ምን ፡ ትጠቀማለኽ ፡ አንተም ፡ በሕይወትኽ ፡ እኔም ፡ በሕይወቴ ፡ ሳለሁ ፡ ካልተውከው ፡ በዚህ ፡ አኳኋን ፡ ያለፈ ፡ እንደሆን ፡ ታሪክ ፡ ያንተንም ፡ ዘፋኝነት ፡ የኔንም ፡ በኀዘን ፡ በንዴት ፡ መሞት ፡ ለሚ መጣው ፡ ትውልድ ፡ ያስታውሳል ።

ዐፄ ፡ ዳዊት ፤ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ከልክ ፡ ያለፈ ፡ ነገር ፡ ትናገራለህ ፤ እንደሚመስለኝ ፡ ባልንጀራኽ ፡ መስፍን ፡ የሚባለው ፡ የስሜን ፡ ባላባት ፡ ከስሜን ፡ ባሕታዊ ፡ የሰማውን ፡ አሚውቶኽ ፡ ይሆናል ፤ ልጄ ፡ ሆይ ፡ የቤተ ፡ መንግሥትና ፡ የብሕትውና ፡ ሥራ ፡ ለየራሱ ፡

ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ ልጅ ፡ በመሆንኽ ፡ የሱን ፡ ወሬ ፡ ገልብጠኽ ፡ እሱን ፡ መስለኽ ፡ ትናገራለኽ ፤ ይህ ፡ ለሚመጣው ፡ ዕድልኽ ፡ የሚያዋጣኽ ፡ ነገር ፡ አይደለም ። ይህነን ፡ አሳብኽን ፡ ተውና ፡ የሚደርስብኽን ፡ አላፊነት ፡ ለመሸከም ፡ እንድትችል ፡ ሁሉንም ፡ ነገር ፡ በደስታና ፡ በጨዋታ ፡ አሳልፈው ፡ የሰው ፡ ምክር ፡ አትስማ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ አባባ ፡ ደፈረኝ ፡ ብለኽ ፡ እንዳታዝንብኝ ፡ እየለመንኩ ፡ ጥቂት ፡ ላሳስብኽ ፡ እወዳለሁ ። ሰው ፡ በሕሪው ፡ ካልገዛው ፡ የሌላው ፡ ሰው ፡ ምክር ፡ ብቻ ፡ ሊለውጠው ፡ አይችልም ። ለምሳሌ ፤ ባባባ ፡ ዘፈን ፡ መውደድ ፡ ከተማው ፡ ተበላሸ ፡ ምግባር አጣ ፡ እየተባለ ፡ ስለሚታማው ፡ ያባባ ፡ ባለሟሎች ፡ ናቸው ፡ ንጉሡን ፡ ያበላሹ ፡ እየተባሉ ፡ ይታማሉ ። እኔ ፡ ግን ፡ በውነት ፡ ያባባ ፡ ፈቃድ ፡ ወደ ፡ ዘፈን ፡ በማዘንበሉ ፡ ነው ፡ እላለሁ ፡ እንጂ ፡ ባባ ለሟሎቹ ፡ ብቻ ፡ አልፈርድም ። አሁንም ፡ ግርማዊ ፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡ የኔ ፡ ፈቃድ ፡ ስለሆነ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ በልጅ ፡ መስፍን ፡ አትፍረድ በት ፤ ያውስ ፡ ከጨለማ ፡ ወደ ፡ ብርሃን ፡ ስላወጣኝ ፡ ምን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሠራ ።

ማልሳዊ ፡ ዳዊት ፤ በሽታኽ ፡ በጣም ፡ ስላለቀቀኽ ፡ ንግግርኽ ፡ የሻከረ ፡ ሆኖ ፡ ይታያል ። ስለዚህ ፡ አሁን ፡ በክርክር ፡ ላበሳጭኽ ፡ አልፈቅድም ፤ በጎ ፡ ስትሆን ፡ አስረዳኻለሁ ።

አሁን ፡ ግን ፡ ባጭሩ ፡ የማመለክትኽ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ተቀምጠኽ ፡ ዓለማውያን ፡ የማይሠሩትን ፡ ማሰብ ፡ ወይም ፡ ይህነን ፡ ዓለም ጥለኽ ፡ ለመሄድ ፡ እንደማይሆንልኽ ፡ ስታውቀው ፡ የመንታ ፡ እናት ተንጋላ ፡ ትሞት ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ሁለቱንም ፡ እጆችኽን ፡ እሁለት ፡ ጒዳዮች ፡ ላይ ፡ ዘርግተኽ ፡ አንዱንም ፡ ሳትይዘው ፡ በከንቱ እንዳትቀር ፡ ብቻ ፡ አሳስብኻለሁ ፡ ብሎት ፡ ወጣ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ደወል ፡ ደወለ ፤
አሽከር ፡ ገባ ።
ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ልጅ ፡ መስፍንን ፡ ጥራው ፤
ልጅ ፡ መስፍን ፡ ገባ ።
ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ተቀመጥ ፡ ወዳጄ ፡ እንጫወት ።
ልጅ ፡ መስፍን ፡ ከተቀመጠ ፡ በኋላ ፡ ልዑል ፡ ሆይ ፡ በጣም ፡ ተሻለኽን ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ በጣም ፡ በጎ ፡ ነኝ ፡ ወንድሜ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ዛሬ ፡ ካባትኽ ፡ ጋራ ፡ ስትነጋገር ፡ ቃሎቹ ፡ አልተያዙልኝም ፡ እንጂ ፤ ድምፃችሁ ፡ እንደ ፡ ነጐድጓድ ፡ ይሰማ ፡ ነበር ። ስለዚህ ፡ ካባትኽ ፡ የተቀያየምህ ፡ መስሎኝ ፡ በጣም ፡ አዝኜ ነበር ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ መቀያየም ፡ እንኳ ፡ አልተቀያየምንም ። ነገር ፡ ግን ፡ አባቴን ፡ እንደ ፡ ዛሬ ፡ ደፍሬው ፡ አላውቅም ፤ እሱም እንደ ፡ ዛሬ ፡ ብርቱ ፡ ቃል ፡ ተናግሮኝ ፡ አያውቅም ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ የቍጣና ፡ የዘለፋ ፡ ቃል ፡ ነውን ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ የቍጣና ፡ የዘለፋ ፡ እንኳ ፡ አይደለም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ያባትና ፡ የልጅ ፡ አኳኋን ፡ ሳይሆን ፡ የባልንጀራ ፡ ክርክር ፡ ነበር ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ንጉሥ ፡ አባትኽ ፤ በመድፈርኽ ፡ ደስ ፡ ብሎት ምክርኽን ፡ ተቀብለኽን ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ በመዠመሪያ ፡ ለማስረጃ ፡ ስላቀረብኩት ፡ ምሳሌ ፡ አባቴ ፡ በጣም ፡ ተክዞ ፡ ለምሳሌዩ ፡ ምሳሌ ፡ አምጥቶ ፡ ሊያስረዳኝ ፡ አሰበ ። ነገር ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ምሳሌው ፡ ብርቱ ፡ የሆኑ ፡ ቃሎች ፡ ከምሳሌ ፡ ጋራ ፡ ደኅና ፡ አድርጌ ፡ በመመለሴ ፡ ተቈጥቶ ፡ የመንታ ፡ እናት ፡ ተንጋላ ፡ ትሞት ፡ እንደሚባለው ፡ ሁለት ፡ እጅኽን ፡ እሁለት ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ ዘርግተኽ ፡ አንዱን ፡ ሳትይዘው ፡ በከንቱ ፡ እንዳትቀር ፡ አሳስብኻለሁ ፡ ብሎኝ ፡ ወጣ ። ወንድሜ ፡ መስፍን ፡ ሆይ ፡ ባንተም ፡ ደስ ፡ ያለው ፡ አይመስለኝምና ፡ ተጠንቀቅ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ልዑል ፡ ሆይ ፡ አባትኽ ፡ ደኅና ፡ መክሮኻል ሰው ፡ በሁለት ፡ መንታ ፡ መንገድ ፡ መካከል ፡ ቆሞ ፡ ቢመለከት ፡ ባንዱ ፡ መንገድ ፡ ቈርጦ ፡ ካልሄደ ፡ ካሰበው ፡ ሥፍራ ፡ አይደርስም ። ስለኔ ፡ ግን ፡ እኔ ፤ እኔ ፡ ስለ ፡ ሆንኩ ፡ ካባትኽ ፡ የምፈልገው ፡ ነገር ፡ የለኝምና ፡ ምንም ፡ የምፈራው ፡ ነገር ፡ የለም ፤ ልዑል ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ አንተን ፡ ግን ፡ እስትሞት ፡ ድረስ ፡ አልተውኽም ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ መንፈሳዊ ፡ የሆነውን ፡ ንግግራችንን ፡ መለዋወጥ ፡ የሚከለክለን ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ የለም ፤ እንግዴህ ፡ ደኅንነትህን ፡ ካየሁ ፡ ልሂድ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ነገም ፡ አትምጣ ፤ ከነገ ፡ ወዲያ ፡ ከወንዝዳር ፡ አንገረብ ፡ ከሚባለው ፡ ቦታ ፡ ድረስ ፡ እመጣለሁ ፤ አንተም በፈረስ ፡ ሆነህ ፡ ባራት ፡ ሰዓት ፡ ከዚያው ፡ ቦታ እንገናኝ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ እሺ ፡ እግዚአብሔር ፡ በደኅና ፡ ለመገናኘት ፡ ያብቃን ፡ ብሎ ፡ ወጣ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

በሁለተኛው ፡ ቀን ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብና ፡ ልጅ ፡ መስፍን ፡ ከተቃጠሩበት ፡ ቦታ ፡ ልክ ፡ በዚያው ፡ ሰዓት ፡ ተገናኙ ፤ ከፈረሶቻቸው ላይ ፡ ወርደው ፡ አንገት ፡ ላንገት ፡ ተያይዘው ፡ ከተሳሳሙ ፡ በኋላ ፡ ሁለቱም ፡ ከለምለም ፡ ሣር ፡ ላይ ፡ ጋደም ፡ ብለው ፡ ይጫወቱ ፡ ገርመር ።

ልዑል ፡ ያዕቆብም ፤ ወንድሜ ፡ ይህ ፡ ቦታ ፡ እንዴት ፡ ደስ ፡ ይላል ፡ ከተራራው ፡ ከፍታና ፡ ዝቅታ ፡ ላይ ፡ የለመለመው ፡ ሣር ፡ አበቃቀልና ፡ በመካከልና ፡ በመካከል ፡ ተበታትነው ፡ የበቀሉት ፡ አበቦች ፡ ቀለም ፡ ሲታይ ፡ የሥጋና ፡ የነፍስ ፡ ደስታ ፡ ነው ፤ ይልቁንም ፡ የኛኞቼው ፡ አወራረድ ፡ ከምሥራቅ ፡ ፀሐይ ፡ ጋራ ፡ እንደብርሃን ፡ በተራራው ፡ ላይ ፡ ሲወርድ ፡ ደኅና ፡ ሥእሊ ፡ በጥሩ ፡ ቀለም ፡ የሣለው ፡ አይመስልኽምን ፡ በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ቦታ ፡ መጻሕፍትን ፡ ይዞ ፡ ከሰው ፡ ተለይቶ ፡ በዕሙና ፡ መኖር ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ደስ ፡ ይል ፡ ይሆን ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ርግጥ ፡ ነው ፡ ከቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ብዙ ፡ ችግር ፡ ያለበት ፤ የቤተ ፡ ሰቦቹ ፡ ኑሮ ፡ የሰለቸው ፡ ልጆቹ ፡ የሚበሉትና ፡ የሚለብሱት ፡ ያጡ ፤ ከሚስቱ ፡ ጋራ ፡ በችግር ፡ ምክንያት ፡ የሚነዛነዝ ፤ የመጥፎ ፡ ኑሮው ፡ ሐሳብ ፡ ከመኝታው ፡ አለመመቸት ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ እሾህ ፡ እየወጉት ፡ እንቅልፍ ፡ ከማይወስደው ፡ ችግረኛ ፡ ከቤቱ ፡ ኑሮ ፡ ከእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ቦታ ፡ መኖር ፡ የተሻለ ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ልዑል ፡ ያለ ፡ መስፍን ፡ በወርቅ ፡ አልጋ ፡ ላይ ፡ በሐር ፡ በተሰፋ ፡ ፍራሽ ፡ በጠጕር ፡ የተሠሩ ፡ ውድ ፡ የብርድ ፡ ልብሶች ፡ ተጐናጽፎ ፡ ለሚተኛ ፡ በኑሮው ፡ ለማይቸገረው ፡ ዕድለኛ ፡ ሰው ፡ በለምለም ፡ ሜዳና ፡ በሚያምሩ ፡ ሸለቆዎች ፡ ብቻውን ፡ መኖር ፡ ምን ፡ ያደርግለታል ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ወዳጄ ፡ ልጅ ፡ መስፍን ፡ ዛሬ ፡ ገና ፡ ተሳሳትኽ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በሐሳብና ፡ በኀዘን ፡ ሲጨነቅ ፡ ይልቁንም ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ከንቱነት ፡ ተገልጦ ፡ ሲታየው ፡ በወርቅ ፡ አልጋ ፡ በሐርና ፡ በጠጕር ፡ በተሠሩ ፡ ፍራሾችና ፡ የብርድ ፡ ልብሶች ፡ ተጠቅሎ ፡ ቢተኛ ፡ ምን ፡ ደስ ፡ ይለው ፡ ይመስልኻል ። ለምሳሌ ፤ አንድ ፡ በሽተኛ ፡ ሰው ፡ በወርቅ ፡ በዕንቍ ፡ በተሠራ ፡ አልጋ ፡ ቢያስተኙት ፡ በሐርና ፡ በጠጕር ፡ በተሠሩ ፡ ልብሶች ፡ ቢጠቀልሉት ፡ እሱ ፡ የሚያዳምጠው ፡ የሕመሙን ፡ ሥቃይና ፡ ጭንቀቱን ፡ ቅጥቃጤውን ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ለሱ ፡ የከበረ ፡ አልጋና ፡ የከበሩ ፡ ልብሶች ፡ ምኑም ፡ አይደሉ ፡ እንዲያውም ፡ ከትከሳቱ ፡ የተነሣ ፡ ከላዩ ፡ ላይ ፡ እንዲያነሡለት ፡ ይለምናል ፤ እንዚሁም ፡ በኀዘን ፡ ለታመመ ፡ የሰው ፡ ልብ ፡ የድሎት ፡ ኑሮዎች ፡ ሁሉ ፡ አስጨናቂዎች ፡ መሆናቸው ፡ ካንተ ፡ ከወንድሜ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይሳታል ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ አልተሳሳተኹም ፡ ነገር ፡ ግን ፡ አንተ ፡ ከዚሁ ፡ ደረጃ ፡ መድረስኽን ፡ ስላወቅሁ ፡ ነው ፤ ይህነን ፡ ካንተ ፡ በመስማቴ ፤ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግንሁ ። መድኃኒታችን ፡ ‹ባለጸጋ ፡ ይጸድቃል ፡ ከማለት ፡ ግመል ፡ በመርፌ ፡ ቀዳዳ ፡ ይሾልካል ፡ ማለት ፡ ይቀላል» ፡ እንዳለው ፡ ይህ ፡ ላንተ ፡ የተሰማኽ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ስሜት ፡ በቤተ ፡ መንግሥት ፡ ውስጥ ፡ ለሚኖር ፡ ሰው ፡ ምንም ፡ እንዳይሰማው ፡ ስላወቅሁትና ፡ ያንተንም ፡ አስተያየት ፡ ሰፊ ፡ መሆኑን ፡ ለመሰለል ፡ ነበር ፡ እየተባባሉ ፡ ሲጫወቱ ፤ ልጅ ፡ መስፍን ፤ ምንድነው ፡ በሩቅ ፡ ሰው ፡ ሲመጣ ፡ አየሁ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ዘወትር ፡ መነጽር ፡ ይይዝ ፡ ነበርና ፡ በመነጽሩ ፡ እየተመለከተ ፡ አንድ ፡ ድኻ ፡ ልብሱ ፡ ሁሉ ፡ የተበጫጨቀ ፡ የሚያሳዝን ፡ ሰው ፡ ነው ፡ እያለ ፡ ሲነግረው ፡ ድኻው ፡ ወደነሱ ፡ ቀርቦ ፡ ጌቶቼ ፡ ዓለም ፡ አላፊ ፡ ናት ፡ መልክ ፡ ረጋፊ ፡ ነው ፡ እንደኔ ፡ አግኝቻለሁ ፡ አትጡ ፡ እባካችሁ ፡ ምጽዋት ፡ ስጡኝ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ በጣም ፡ አዝኖ ፡ ከኪሱ ፡ ገንዘብ ፡ ለማውጣት ፡ ሲዳብስ ፡ ልጅ ፡ መስፍን ፡ ቈይ ፡ አትቸኵል ፡ እንደኔ ፡ አግኝታችሁ ፡ አትጡ ፡ ያለበትን ፡ እንጠይቀው ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ምንድነው ፡ እንደኔ ፡ አግኝታችሁ ፡ አትጡ ፡ ያልከው ።

ድ'ኻው ፤ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ጥያቄ ፡ ስለ ፡ ጠየቅ'ኸኝ ፡ አመስግን'ኻለሁ ፡ እኔ ፡ በጐንደር ፡ የታወቅ'ኹ ፡ አንድ ፡ ሀብታም ፡ ሰው ፡ ነበርኩ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ስምኽ ፡ ማን ፡ ይባላል ።

ድ'ኻው ፤ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ስሜ ፡ ስለ ፡ ጠፋ ፡ እኔም ፡ ስሜን ፡ ላውቀው ፡ አልችልም ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ይሁን ፡ ግድ ፡ የለም ፡ ስምህን ፡ ለመንገር ፡ እንዳልፈቀድ'ክ ፡ ተረዳ'ኹት ፤ ታዲያ ፡ ይህ ፡ ችግር ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ደረሰብ'ክ ።

ድ'ኻው ፤ ይህነንስ ፡ ደኅና ፡ አድርገ'ክ ፡ ስማኝ ፡ እነግር'ኻለሁ ፡ ቅድም ፡ እንደ ፡ ነገርኩ'ኽ ፡ በጐንደር ፡ ባለብዙ ፡ ገንዘብና ፡ የተከበርኩ ፡ ሰው ፡ ነበርኩ ፤ ሚስቴም ፡ የተዋበች ፡ ቈንዦ ፡ ስመ ፤ ጥሩ ፡ ዘፋኝ ፡ ነበረች ፤ ዐፄ ፡ ዳዊት ፡ ዘፈን ፡ በመውደዳቸው ፡ መኳንንቱም ፡ መሳፍንቱም ፡ የኔን ፡ ሚስት ፡ ይቀባበሏት ፡ ዠመር ። እሷም ፡ ለውበቷና ፡ ለደም ፡ ግባቷ ፡ የበለጠ ፡ ማሣመሪያ ፡ እንዲሆናት ፡ ልብስና ፡ ውድ ፡ ድንጋይ ፡ ሉል ፡ በመግዛት ፡ ገንዘቤ ፡ ሁሉ ፡ አለቀ ፤ ሚስቴም ፡ በነዚሁ ፡ መኳንንትና ፡ መሳፍንት ፡ ፍቅር ፡ በመብልና ፡ መጠጥ ፡ ምክንያት ፡ ፈጽማ ፡ ተወችኝ ፤ ቢሆንም ፡ ስሟ ፡ የሚጠራው ፡ በኔ ፡ ነበርና ፡ የራሴን ፡ ሀብት ፡ ጨርሼ ፡ በሷ ፡ ጥላ ፡ ውስጥ ፡ የለት ፡ ጕርሥ ፡ አገኝ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ ይህ ፡ የውርደት ፡ ሥራ ፡ እንደ ፡ ደስታ ፡ ተቈጥሮብኝ ፡ ሚስቴ ፡ መኳንንትና ፡ መሳፍንት ፡ ሰልችተዋት ፡ አንድ ፡ ጋሬ ፡ ነጂ ፡ ወዳ ፡ በቅናት ፡ ምክንያት ፡ ወይም ፡ እሱን ፡ ንቃ ፡ ሌላ ፡ ፈልጋ ፡ እንደሆን ፡ አይታወቅም ። ከዕለታት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ይህ ፡ ጋሬ ፡ ነጂ ፡ ሰውነቱን ፡ ሳታውቅ ፡ ከቤቷ ፡ እንዲወስዳት ፡ ከጋሬው ፡ ስትወጣ ፡ እንዳበደ ፡ ሰው ፡ ፈረሱን ፡ እየገረፈ ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ ቢከተል ፡ አልደርስበት ፡ ብሎ ፡ ከጣና ፡ ባሕር ፡ ሲደርስ ፡ አብረው ፡ ከነጋሬው ፡ ሰጥመው ፡ ቀሩ ። እኔ ፡ የራሴን ፡ ገንዘብ ፡ ጨርሼ ፡ በሷ ፡ ገንዘብ ፡ የምኖር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከከበርኩበት ፡ ከተማ ፡ እየለመንኩ ፡ ከመብላት ፡ በባላገር ፡ ከማልታወቅበት ፡ ቦታ ፡ እየለመንኩ ፡ መኖር ፡ ይሻለኛል ፡ ብዬ ፡ ወደዚህ ፡ መጣሁ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ እኔም ፡ ወሬውን ፡ ሰምቻለሁ ፡ ባልሳሳት ፡ ሚስትኽ ፡ ወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈር ፡ የምትባለው ፡ አይደለችምን ።

ድኻው ፤ አንገቱን ፡ እየነቀነቀ ፡ አዎን ፡ እሷው ፡ ናት ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ልጅ ፡ መስፍን ፤ ልዑል ፡ ያዕቆብን ፡ ልዑል ፡ ሆይ ፡ ይህ ፡ ድኻ ፡ ያባትኽ ፡ ዘፈን ፡ መውደድ ፡ የገደለው ፡ ነውና ፡ እንግዴህ ፡ ገንዘብኽን ፡ ስጠው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የዚህን ፡ ሰው ፡ ሚስት ፡ ታሪክ ፡ ነገ ፡ ወይም ፡ ከነገ ፡ ወዲያ ፡ ጣና ፡ ድረስ ፡ እንቃጠርና ፡ ከዚያው ፡ ከቦታው ፡ እንጫወታለን ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ለድኻው ፡ መቶ ፡ ብር ፡ ሰጥቶት ፡ ለተነገ ፡ ወዲያ ፡ ቅዳሜ ፤ ከጣና ፡ ዳር ፡ ደንቢያ ፡ ከሚባለው ፡ ሥፍራ ፡ በምስት ፡ ሰዓት ፡ ተቃጥረው ፡ ተለያዩ ።

## ምዕራፍ ፡ ፬

ቅዳሜ ፡ ባምስት ፡ ሰዓት ፡ ከዚያው ፡ ከተቃጠሩበት ፡ ቦታ ፡ ተገናኙ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ወንድሜ ፡ መስፍን ፡ ሆይ ፡ እስኪ ፡ ከዚህ ፡ ከለመለመው ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ጋደም ፡ ብለን ፡ የጣናን ፡ ደሴቶች ፡ እየተመለከትን ፡ የገሥመርነውን ፡ የዚያን ፡ የድኻ ፡ ሚስት ፡ ታሪክ ፡ እንጫወት ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ እሺ ፡ እንግዴህ ፡ ልዑልነትኽ ፡ በጠቅላላ ፡ ልብ ፡ እንዲሰማኝ ፡ እለምንኻለሁ ። አንድ ፡ ቀን ፡ ወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈር ፡ ካፄ ፡ ዳዊት ፡ ቤት ፡ ዘፍና ፡ ስትወጣ ፡ አንድ ፡ መልከ ፡ መልካም ፡ ጋሬ ፡ ነጅ ፡ አይታ ፡ በፍቅር ፡ ተነደፈችና ፡ ከቤቷ ፡ ይዟት ፡ ሲሄድ ፡ መውደዷን ፡ ገልጣ ፡ ነገረቻው ፤ እሱም ፡ እኔ ፡ ድኻ ፡ እድሩም ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ከእመቤቴ ፡ ጋራ ፡ ወዳጅ ፡ መሆን ፡ ይገባኛል ፡ አላት ፤ እሷም ፡ አንተን ፡ ወዳጅ ፡ ማድረግ ፡ ከክብሬና ፡ ከገንዘቤ ፡ ሁሉ ፡ ይበልጥብኛል ፡ እኔ ፡ ሳላስብ ፡ አንተን ፡ የመረጥሁ ፡ አይምሰልኽ ፡ እያለች ፡ በለመለመ ፡ መላሷ ፡ አሳተቸው ፡ ያም ፡ ችግረኛ ፡ ድኻ ፡ በወጥመድ ፡ እንደ ፡ ተያዘ ፡ አውሬ ፡ በከንቱ ፡ ፍቅሯ ፡ ተነደፈ ፡ በፍቅር ፡ ጦር ፡ ልቡ ፡ ተወጋ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ወይ ፡ ግሩም ፡ ይህች ፡ ሴት ፡ የብዙ ፡ መኳንንትና ፡ መሳፍንት ፡ ወዳጅ ፡ ስትሆን ፡ ስለ ፡ ምንድነው ፡ ከሥራው ፡ በስተቀር ፡ የዚህን ፡ ዐይነት ፡ ድፍረት ፡ የማያውቀውን ፡ የዕለት ፡ ሠራ

ተኛ ፡ ምግባር ፡ ለማበላሸት ፡ የድኻ ፡ ቤቱን ፡ ለማጥፋት ፡ የምትጥ ረው ፤ በጣም ፡ ያሳዝናል ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ልዑል ፡ ሆይ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ከሐሳብ ፡ አርነት ፡ ከወጣ ፡ በኋላ ፡ ምኞቱን ፡ የሚፈጽምበት ፡ የታቀደ ፡ ወሰን ፡ የለውም ፡ ሰው ፡ ለፍትወቱ ፡ ነፃነት ፡ ካገኘና ፡ የልምድ ፡ ታዛዥ ፡ ከሆነ ፡ በኋላ ፡ ለደስታው ፡ የሚበቃ ፡ ነገር ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ አያገኝም ፤ ዘወትር ፡ እንደ ፡ ሜዳ ፡ አህያ ፡ ፍትወትን ፡ እያነፈነፈ ፡ በዓለም ዙሪያ ፡ ይዞራል ፡ እንጂ ፤ እሱን ፡ የሚያረካ ፡ ደስታና ፡ ገንዘብ ፡ አያገኝም ። ልዑል ፡ ሆይ ፡ ይህች ፡ ሴት ፡ በዝሙት ፡ ጦር ፡ በመወጋቷ ፡ ስንገረም ፡ ሁላች ንም ፡ በተወጋንበት ፡ አንዳንድ ፡ ኀጢአት ፡ እንደዚሁ ፡ ነን ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ከዚህ ፡ በኋላስ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ሆነ ፤ እንዴት ፡ የሚገርም ፡ ነገር ፡ ነው ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ርግጥ ፡ የሚገርም ፡ ነው ፤ ይሀ ፡ ጋሪ ፡ ነጂ ፡ ከወ ይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈር ፡ ቤት ፡ ሲጫወት ፡ አምሽቶ ፡ ከሌሊቱ ፡ በ፯ ፡ ሰዓት ፡ ለመሄድ ፡ ፈቃድ ፡ ጠየቃት ፤ እሷም ፡ እሺ ፡ አሁን ፡ ሄደኽ ፡ ነገ ፡ በ፲ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ አንድትመጣ ፡ ቃልኽን ፡ ስጠኝ ፡ አለችው ፤ እሱም ፡ እሺ ፡ በዚሁ ፡ ሰዓት ፡ እመጣለሁ ፡ ብሎ ፡ ተሰነባብተው ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ። ያ ፡ ችግረኛ ፡ ሰው ፡ የመልኳን ፡ ደም ፡ ግባት ፡ የንግግ ሯን ፡ ጣዕም ፡ በማሰብና ፡ ከላዩ ፡ ላይ ፡ የቀረውን ፡ የሽቱ ፡ መዐዛ ፡ በማ ሽተት ፡ በሳብ ፡ ተውጦ ፡ ከሷ ፡ የተጫወተ ፡ እየመሰለው ፡ ብቻውን ፡ ከሳቡ ፡ ጋራ ፡ እየተነጋገረ ፡ ከቤቱ ፡ ደረሰ ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ያ ፡ የድኻ ፡ ጐጆው ፡ ጨለማ ፡ ወረሶት ፡ አንዲት ፡ የመቅረዝ ፡ መብራት ፡ ብልጭ ፡ ብልጭ ፡ እያለች ፡ ስትበራ ፤ ሚስቱም ፡ ከርጌ ፡ የዕንጨት ፡ ገበታ ፡ ላይ ፡ ተደግፋ ፡ ባሏን ፡ ስጠብቅ ፡ እንቅልፍ ፡ ወስዷት ፤ መብላቸውም ፡ በርዶ ፡ ልጃቸው ፡ አባቱን ፡ ሲጠብቅ ፡ ከልጋው ፡ ሥር ፡ እንቅልፍ ፡ ወስዶት ፡ ደረሰ ። ወዲያው በሩን ፡ ከፍቶ ፡ እንደ ፡ ገባ ፡ ሚስቱንም ፡ ልጁም ፡ ከእንቅልፋቸው ፡ ነቅተው ፡ እንደ ፡ ወትሮው ፡ መስኳቸው ፡ ሚስቱም ፡ ቶሎ ፡ ብላ ፡ የብርድ ፡ ልብሱን ፡ ለመቀበል ፡ ልጁም ፡ አበባ ፡ መጣኽ ልኝ ፡ ወይ ፡ ብሎ ፡ አንገቱ ፡ ላይ ፡ ቢጠመጠም ፡ በክፉ ፡ ፍላጻ ፡ የተወጋ ፡ ችግረኛ ፡ ሰው ፡ የብርድ ፡ ልብሱን ፡ አውልቆ ፡ ከልጋው ፡ ላይ ፡ ወር ውሮ ፡ ልጁንም ፡ ሳይስመው ፡ ከወንበር ፡ ላይ ፡ ተቀመጠ ። ሚስቱም ፡

ምን ፡ ነገር ፡ አገኘው ፡ እያለች ፡ ደንግጣ ፡ ወዳጄ ሆይ ፡ ምን ፡ ሆንክ ፡ እኛ ፡ ደኅና ፡ እንሁን ፡ እንጂ ፡ አትናደድ ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ድኻም ፡ ሀብታምም ፡ አንድ ፡ ነው ።

ይልቁንም ፡ «በጥል ፡ እርድ ፡ ከመላበት ፡ ቤት ፡ በፍቅር ፡ ደረቅ ፡ ቁራሽ ፡ እንጀራ ፡ ይሻላል ፡ ተብሏል» ፡ እኛ ፡ ይህችን ፡ የድኻ ፡ ጐጆአችንን ፡ በደስታና ፡ በፍቅር ፡ ከያዝናት ፡ በሐሳብ ፡ ከሚጨነቅ ፡ ንጉሥ ፡ እንበልጣለን ። ለሰው ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ብልጭልጭ ፡ ነገሮች ፡ ሁሉ ፡ ለኀዘኑና ፡ ለመከራው ፡ ለንዴቱ ፡ ማረጋጊያ ፡ አይሆኑትም ፤ አሁንም ፡ ወዳጄ ፡ በትዳርኽ ፡ አትበሳጭ ፡ እኔና ፡ ልጅኽ ፡ ደኅና ፡ እንሁንልኽ ፡ እያለች ፡ ስታጽናናው ፡ እሱ ፡ ምንም ፡ አይሰማትም ፡ ነበር ። ለሱ ፡ በሐሳቡ ፡ የሚታየውና ፡ የሚያነጋግረው ፡ ወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈር እጁን ፡ ይዛ ፡ የምታጫውተውና ፡ የምትስመው ፡ ይልቁንም ፡ የሐሰት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ የገባችለትን ፡ በማሰብ ፡ ተለውጦ ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ የለም ፡ ነበር ። በመጨረሻው ፡ እባክሽ ፡ የምንበላውን ፡ በልተን ፡ እንተኛ ፡ አላት ፤ እሷም ፡ እሱን ፡ በመጠበቅ ፡ የቀዘቀዘውን ፡ ወጥና ፡ እንጀራ ፡ ጠላ ፡ አቀረበችለትና ፡ እንብላ ፡ ወዳጄ ፡ አለችው ። እሱም ፡ ቀመስ ፡ አድርጎ ፡ አልበላም ፡ ወጡም ፡ ቀዝቅዟል ፡ ጠላውም ፡ ከምጥጧል ፡ ብሎ ፡ ተቈጥቶ ፡ ልብሱን ፡ ሳያወልቅ ፡ ካልጋው ፡ ወጥቶ ፡ ተከናንቦ ፡ ተኛ ፡ እሷም ፡ ልጃቸውም ፡ እያዘኑ ፡ ልብሳቸውን ፡ ሳያወልቁ ፡ ተጋደሙ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ወዳጄ ፡ መስፍን ፡ ሆይ ፡ አሁን ፡ ስታጫውተኝ ፡ በሐሳቤ ፡ ከነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ንብረት ፡ ውስጥ ፡ ገብቼ ፡ ስመለከት ፡ ያች ፡ የፍቅርና ፡ የመተዛዘን ፡ ጐጆአቸው ፡ በዚች ፡ በሴት ፡ ምክንያት ፡ ጨለማ ፡ ወርሷት ፡ ልትፈታና ፡ ልትዘጋ ፡ ስታጣጥር ፡ ታየችኝ ። ይህ ፡ ሰው ፡ የዚችን ፡ ሴት ፡ ቤት ፡ ባያይና ፡ እሷም ፡ የሐሰት ፡ ፍቅሯን ፡ ባትገልጥለት ፡ የድኻ ፡ ሚስቱንና ፡ ቤቱን ፡ አይጠላም ፡ ነበር ፡ እኮ ፤ አዬ ፡ ጉድ ፡ ይህ ፡ ችግረኛ ፡ ሰው ፡ በምን ፡ ይህችን ፡ ሴት ፡ አጋጠመው ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ እውነት ፡ ነው ፡ ያንዱን ፡ ትዳር ፡ አንዱ ፡ ካላየው ፡ ሁሉም ፡ በየቤቱ ፡ ንጉሥ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ መተያየት ፡ መበላለጥን ፡ ያሳያል ፡ መበላለጥም ፡ መጠላላትን ፡ መቀናናትን ፡ ፈጠረ ፤ መቀናናት ፡ ሞትን ፡ ይፈጥራል ።

አንድ ፡ ንጉሥ ፡ ከግንቡ ፡ ውስጥ ፡ ሲናፈስና ፡ አንድ ፡ ገበሬ ፡ ከር ሻው ፡ ውስጥ ፡ ሲናፈስ ፡ ሁለቱም ፡ ካልተያዩ ፡ በትዳር ፡ አንድ ፡ ናቸው ፡ ተብሏል ። ልዑል ፡ ሆይ ፤ አሁንስ ፡ የዚህን ፡ ሰውዬ ፡ ታሪክ ፡ ልቀጥልልኽ ፤ በማግስቱም ፡ እንደ ፡ ተቃጠሩት ፡ ከእኩለ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ባ፲ ፡ ሰዓት ፡ ጋሪውን ፡ ጭኖ ፡ ወደሷ ፡ ሄደ ፤ ወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈርም ፡ ልብሷን ፡ ለብሳ ፡ ትጠብቀው ፡ ነበርና ፡ እንደ ፡ ደረሰ ፡ ካጠገቡ ፡ ተቀምጣ ፡ እየተጫወቱ ፡ ሰው ፡ ከሌለበት ፡ ቦታ ፡ ብዙ ፡ ደን ፡ ካለበትና ፡ ውሃ ፡ ከሚፈስበት ፡ ከወንዝ ፡ ዳር ፡ ወርደው ፡ ካንድ ፡ ትልቅ ፡ ዛፍ ፡ ሥር ፡ ተቀምጠው ፡ ይጫወቱ ፡ ነበር ።




ጫን ፡ ያለውና ፡ ወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈር ።

ወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈርም ፡ ወዳጇ ፡ ካንተ ፡ በመገናኘቴ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ ብሎኛል ፡ እንግዴህ ፡ አንተን ፡ አገባኻለሁ ፡ ሚስት ፡

እንዳለችኝ ፡ ፍታ ፡ እያለች ፡ የሐሰት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ በለመለመ፡ ምላሷ ፡ ስታጫውተው ፡ ፲፪ ፡ ሰዓት ፡ ሆነ ፡ እንዳጋጣሚ ፡ አጠገባቸው ፡ ካለው ፡ ዛፍ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ቍራ ፡ መጥቶ ፡ ተቀምጦ ፡ ዋ ፡ ዋ ፡ ዋ ፡ እያለ ፡ ይጮኽ ፡ ዠመር ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ በጐንደር ፡ ይልቁንም ፡ በሰቈጣ ፡ አንድ ፡ ቍራ ፡ ብቻ ፡ መጥቶ ፡ ባጠገቡ ፡ የጮኸ ፡ እንደሆን ፡ አይቀናውም፡ ክፉ ፡ ዕድል ፡ ይሆናል ፡ የሚባል ፡ አምልኮ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፤ እነሱም ፡ በዚህ ፡ ስለሚያምኑ ፡ በጣም ፡ ደነገጡ ፤ ወይዘሮ ፡ የውብ፡ ሰፈርም ፡ ወንድሜ ፡ ወደ ፡ ቤታችን ፡ እንመለስና ፡ ከዚያው ፡ እንጫወት ፡ ብላው ፡ በጋሪ ፡ ሆነው ፡ እየተሳሳሙ ፡ ሲሄዱ ፡ የነዚያ፡ ድኾች ፡ ጎረቤታቸው ፡ የሆነ ፡ አንድ ፡ ጋሪ ፡ ነጂ ፤ እንግዳ ፡ ሴት፡ ይዞ ፡ እየተሳሳመ ፡ በመሄዱ ፡ ገርሞት ፡ ሄዶ ፡ ለሚስቱ ፡ ባልሽ፡ ዛሬ ፡ ካንዲት ፡ ሀብታም ፡ ሴት ፡ ጋራ፡እየተሳሳመ ፡ ሲሄድ ፡ አየሁት፡ ብሎ ፡ ነገራት ፡ ሚስቱም ፡ ሐሰት ፡ ነው ፡ እንዳትል ፡ ትላንት ፡ ማታ ፡ አኳኋኑን ፡ ስላየች ፡ ባጣም ፡ አዝና ፡ ቤቴ ፡ ንብረቴ ፡ እንግዴህ ፡ ልንጠፋ ፡ ነው ፡ እያለች ፡ ብቻዋን ፡ ቤቷን ፡ ዘግታ ፡ ታለቅስ ፡ ዠመር ። ልጅዋም ፡ ከግንቡ ፡ ሥር ፡ ተኰራምቶ ፡ የናቱን ፡ ኀዘን ፡ እያየ ፡ ሲያለቅስ ፡ ያ ፡ ችግረኛ ፡ ጋሪ ፡ ነጂ ፡ ማታ ፡ ከዘፈን ፡ ቤት ፡ ደኅና ፡ ልብስ ፡ ለብሶ ፡ እንዲመጣ ፡ ወይዘሮ ፡ የውብ፡ ሰፈር ፡ ስለ ፡ ጠራችው ፡ ልብሱን ፡ ለመለወጥ ፡ ቸኵሎ ፡ እየሮጠ ፡ መጥቶ ፡ በሩን ፡ በኀይል ፡ ከፍቶ ፡ ቢገባ ፡ ሚስቱ ፡ ከመሬት ፡ ወድቃ ፡ ስታለቅስ ፡ ልጁም ፡ ከግንቡ ፡ ተኰራምቶ ፡ ሲያለቅስ ፡ ደረሰ ፤ እሱም ፡ የሚስቱና ፡ የልጁ ፡ ኀዘን ፡ ሳይሰማው ፡ ወደ ፡ ጓዳ ፡ ገብቶ ፡ በድካማቸው ፡ ያጠራቀሙትን ፡ መቶ ፡ አምሳ፡ ብር ፡ አውጥቶ ፡ ሚስቱን ፡ ዛሬ ፡ ማታ ፡ ከባልንጀሮቼ ፡ ቤት ፡ ለበዓል ፡ ስለ ፡ ተጠራሁ ፡ አመሻለሁና ፡ አትጠብቂኝ ፡ አላት ። እሷም፡ ብድግ ፡ ብላ ፡ ያላወቅሁ ፡ አይምሰልኽ ፡ ላንተ ፡ ብቻ ፡ ለማትሆን፡ ለዓለም ፡ ሴት ፡ የድኻ ፡ ጕዠኽን ፡ ልታፈርስ ፡ ነው ፤ እንደ ፡ ምን፡ ከሚያሳዝን ፡ ወጥመድ ፡ ውስጥ ፡ ገባኽ ፤ አዬ ፡ ቤቴ ፡ ንብረቴ ፡ እያለች ፡ ጮኻ ፡ ከመሬት ፡ ላይ ፡ ወደቀች ፡ እሱም ፡ ተቈናጥሮ ፡ የብርድ ፡ ልብሱን ፡ ቶሎ ፡ ብሎ ፡ ለብሶ ፡ ሲወጣ ፡ ልጁ ፡ አባባ፡ የት ፡ ጥለኸኝ ፡ ትሄዳለኽ ፡ እያለ ፡ ልብሱን ፡ ቢይዘው ፡ ነጥቆት፡

ሄደ ፤ ልጁም ፡ አባባ ፡ አባባ ፡ እያለ ፡ ተከተለው ። አባቱም ፡ መከተሉን ፡ ሳያይ ፡ ልጁ ፡ ብዙ ፡ መንገድ ፡ ከሄደ ፡ በኋላ ፡ ደክሞት ፡ በጨለማ ፡ ሲሮጥ ፡ በድንገት ፡ ካንድ ፡ ፈፋ ፡ ውስጥ ፡ ዐንቅሮት ፡ ወደቀና ፡ ሞተ ፤ እናቱም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ከመሬት ፡ ወድቃ ፡ ስታለቅስ ፡ ቈይታ ፡ ቀና ፡ ብላ ፡ ልጅዋን ፡ ብትመለከት ፡ ከቤት ፡ ውስጥ ፡ አጣችው ። ከደጅ ፡ ወጥቶ ፡ ይሆናል ፡ ብላ ፡ ወጥታ ፡ ብትጠራው ፡ ምንም ፡ መልስ ፡ አጣች ፤ ወይኔ ፡ አባቱን ፡ ሲከተል ፡ በውድቅት ፡ ጨለማ ፡ ወድቆ ፡ ይሆናል ፡ ብላ ፡ ጎረቤቶቿ ፡ እንዲያፋልጓት ፡ አጥብቃ ፡ ትጮኽ ፡ ዠመር ። ጩኸት ፡ በተሰማ ፡ ጊዜ ፡ ጎረቤቶች ፡ ሁሉ ፡ ችቧቸውን ፡ አብርተው ፡ ወጡ ፤ እሷም ፡ ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ ልጄ ፡ አሁን ፡ ከዚህ ፡ ጠፋብኝ ፡ የራቀ ፡ እንደሆን ፡ በዚህ ፡ ዝናብ ፡ በውድቅት ፡ ጨለማ ፡ አውሬ ፡ ይበላኛልና ፡ እባካችሁ ፡ በልጅ ፡ አምላክ ፡ አፋልጉኝ ፡ እያለች ፡ የመረረ ፡ ልቅሶ ፡ ታለቅስ ፡ ዠመር ። ጎረቤቶቿም ፡ ሳይርቅ ፡ ዱካውን ፡ እየተመለከትን ፡ እንከተል ፡ ብለው ፡ ፍለጋውን ፡ ሲፈልጉ ፡ እልፍ ፡ ብለው ፡ ያንድ ፡ ትንሽ ፡ ልጅ ፡ ፍለጋ ፡ አገኙና ፡ ተከታተሉ ፤ ትንሽ ፡ እንደ ፡ ሄዱ ፡ በዝናቡ ፡ ምክንያት ፡ ፍለጋው ፡ ጠፋባቸው ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ግራ ፡ ገብቷቸው ፡ ወዲህና ፡ ወዲያ ፡ ተበታትነው ፡ ሲፈልጉ ፡ አንደኛው ፡ ሰው ፡ ሕፃኑን ፡ ከፈፋ ፡ ውስጥ ፤ ወድቆ ፡ ሞቶ ፡ አገኘው ። ሰውዬውም ፡ ደንግጦ ፡ ጮኸ ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እናቱ ፡ በኀዘን ፡ ልብዳ ፡ ልጄ ፡ ልጄ ፡ እያለች ፡ እጅዋን ፡ ዘርግታ ፡ እንደ ፡ ደረሰች ፡ እልጅዋ ፡ ላይ ፡ ወድቃ ፡ አእምሮዋን ፡ አጥታ ፡ አፉን ፡ እየሳመች ፡ ከላዩ ፡ ላይ ፡ ትንከባለል ፡ ነበር ። ጎረቤቶቿም ፡ የመረረ ፡ ኀዘኗን ፡ ስላዩ ፡ ችቧቸውን ፡ ይዘው ፡ ተሰብስበው ፡ ያለቅሱ ፡ ነበር ፤ ወዲያው ፡ ሬሳውን ፡ አንሥተው ፡ እናቱንም ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ደግፈው ፡ ወደ ፡ ቤት ፡ ወሰዷቸው ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ አዬ ፡ ጉድ ፡ እንዴት ፡ ያሳዝናል ፡ ምን ፡ ይሆን ፡ መጨረሻው ፡ እባክኽ ፡ ቀጥልልኝ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ልዑል ፡ ሆይ ፡ የሚያሳዝን ፡ ጨዋታ ፡ በማጫወቴ ፡ ይቅር ፡ በለኝ ፡ ነገር ፡ ግን ፡ «ወደ ፡ ሠርግ ፡ ቤት ፡ ከመሄድ ፡ ወደ ፡ ልቅሶ ፡ ቤት ፡ መሄድ» ፡ ይሻላል ፡ ተብሏል ፡ አሁንስ ፡ ጊዜው ፡ ሳይመሽ ፡ የዚህን ፡ ሰው ፡ ታሪክ ፡ ልጨርስልኽ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ እኔም ፡ የዚህን ፡ ሰው ፡ ታሪክ ፡ ለመስ ማት ፡ ቸኵያለሁና ፡ አጫውተኝ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጎረቤቶቿ ፡ የልጅዋን ፡ ሬሳ ፡ ባልጋ ፡ ላይ ፡ አድርገው ፡ አጥበው ፡ ገንዘው ፡ እሷንም ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ደግፈው ፡ አብረው ፡ ያለቅሱ ፡ ነበር ፤ እናቱ ፡ ልጄ ፡ ልጄ ፡ እያለች ፡ የመረረ ፡ ልቅሶ ፡ ስታለቅስ ፡ ስንኳን ፡ ለጎረቤት ፡ ለማያ ውቃት ፡ ሰው ፡ ታሳዝን ፡ ነበር ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ያ ፡ ጋሪ ፡ ነጂ ፡ ለወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈር ፡ መታሰቢያ ፡ ሰንደል ፡ ሽቱ ፡ ገዝቶ ፡ በቀጠሮው ፡ ቢሄድ ፡ መሳፍንቱና ፡ መኳንንቱ ፡ ተሰብስበው ፡ ከወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈር ፡ ጋራ ፡ ሲጫወቱና ፡ ሲዘፍኑ ፡ ጋሪ ፡ ነጂው ፡ አዲስ ፡ ልብሱን ፡ ለብሶ ፡ መታሰቢያውን ፡ በእጁ ፡ ይዞ ፡ አሮጌ ፡ ጫማውን ፡ አድርጎ ፡ በሩን ፡ መቶ ፡ ከፍቶ ፡ ገባ ፤ በረኛውም ፡ ደንግጦ ፡ አንድ ፡ ጊዜ እግሩን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ራሱን ፡ ካየ ፡ በኋላ ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ ተሳስተኻል ፡ ይህ ፡ ሥፍራ ፡ የመሳፍን ትና ፡ የመኳንንት ፡ ቦታ ፡ ነው ፡ አለው ። ያም ፡ ጋሪ ፡ ነጂ ፡ አልተሳሳትኩም ፡ ዛሬ ፡ ከዚሁ ፡ እንድመጣ ፡ ከወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈር ፡ ቀጠሮ ፡ አለኝ ፤ ብሎ ፡ የጻፈችለትን ፡ ወረቀት ፡ አሳ የው ፤ በረኛውም ፡ ተገርሞ ፡ አንተ ፡ ከዚህ ፡ ቈየኝ ፡ ወረቀ ቱን ፡ ላሳይልኽና ፡ ልምጣ ፡ በኋላ ፡ አገናኝኻለሁ ፡ ብሎት ፡ ወረቀቱን ፡ ተቀብሎት ፡ ሄደ ፤ ያም ፡ ጋሪ ፡ ነጂ ፡ አላቅሙ ፡ የጕመረው ፡ ፍቅር ፡ ስላሳበደው ፡ በኋላ ፡ በኋላው ፡ እየተከተለ ፡ ሄደ ። በረኛውም ፡ ለወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈር ፡ ወረቀቱን ፡ ሰጥቶ ፡ ሰው ፡ ከዚህ ፡ ይጠብቃል ፡ ብሎ ፡ ሲናገር ፡ እሱ ፡ በረኛውን ፡ ቀድሞ ፡ ያመጣውን ፡ ሰንደል ፡ ሽቱ ፡ ለመስጠት ፡ እጁን ፡ ሲዘረጋ ፡ መኳንንቱም ፡ መሳፍንቱም ፡ ልብሱንና ፡ ጫማ ውን ፡ የሱንም ፡ አኳኋን ፡ እያዩ ፡ ይሥቁበት ፡ ጀመር ፤ እሱም ፡ ደንግጦ ፡ ሲንቀጠቀጥ ፡ ያመጣው ፡ ሽቱ ፡ ከጁ ፡ ወድቆ ፡ ተሰ በረ ። ይልቁንም ፡ የሽቱው ፡ መሰበርና ፡ የሰውዬው ፡ መፍራት ፡ መንቀጥቀጥ ፡ ሣቃቸውን ፡ አበዛው ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ያ ፡ ችግረኛ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ዕብድ ፡ ሮጦ ፡ በሩን ፡ ከፍቶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ይበር ፡ ጀመር ። ወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈርም ፡ ምን ፡ ዕብድ ፡

ሰው ፡ ነው ፡ ያስገባችሁት ፡ ብላ ፡ እንደማታውቀው ፡ ሰው ፡ ከመኳንንቱና ፡ ከመሳፍንቱ ፡ ጋራ ፡ ትስቅበት ፡ ዠመር ። እሱም ፡ ተከትለው ፡ ያዘው ፡ እያሉ ፡ የሚያሳድዱት ፡ መስሎት ፡ እየተገ ላመጠ ፡ ከቤቱ ፡ ቢደርስ ፡ ቤቱ ፡ በኀዘን ፡ ጨለማ ፡ ተውጦ ፡ ሚስቱ ፡ ከመሬት ፡ ወድቃ ፡ ስታለቅስ ፡ የሚወደው ፡ ልጁ ፡ ሞቶ ፡ በመድረሱ ፡ እንደ ፡ ዕብድ ፡ ይጮኽ ፡ ዠመር ፡ እንደ ፡ ሰከረም ፡ ሰው ፡ እየተነጣ ፡ ይወድቅ ፡ ነበር ። ወዲያው ፡ ሚስቱ ፡




አቶ ፡ ጫን ፡ ያለው ፡ ዐቅሙን ፡ ባለማወቅ ፡ የደረሰበት ኀዘን ።

ተነሥታ ፡ እንግዴህ ፡ ዕረፈው ፡ ስንኳን ፡ ላንተ ፡ ለመኳንንትና ፡ ለመሳፍንት ፡ ለማትሆን ፡ ለዓለም ፡ ሴት ፡ ስትል ፡ ቤትኽን ፡

ንብረትኽን ፡ ልጅኽን ፡ እኔን ፡ አጠፋኽን ፤ ወይ ፡ ቤቴ ፡ ንብ
ረቴ ፡ ባሌ ፡ ጠፋን ፡ እያለች ፡ ታለቅስ ፡ ነበር ፤ ባሏም ፡
ልጁን ፡ ሚስቱን ፡ ጕዝጕውን ፡ ትኵር ፡ ብሎ ፡ አይቶ ፡ እንግ
ዴህ ፡ ለኔ ፡ ለነፍሰ ፡ ገዳዩ ፡ ንብረት ፡ አይገባኝም ፤ ያችን ፡
የጥፋት ፡ ምክንያት ፡ የሆነችብኝን ፡ ሴት ፡ ገድዬ ፡ እሞታለሁ ፡
ያለዚያ ፡ ራሴን ፡ እገድላለሁ ፡ ብሎ ፡ ሚስቱንና ፡ ልጁን ፡
እንደ ፡ ወደቁ ፡ ራሳቸውን ፡ ሳመና ፡ በቍጣ ፡ በሩን ፡ ዘግቶ ፡ ወጣ ፡

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጋሪውን ፡ ጭኖ ፡ የብርድ ፡ ልብሱን ፡ ለብሶ ፡
ፊቱ ፡ እንዳይታወቅ ፡ ተሸፍኖ ፡ ወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈር ፡ ወዳለ
ችበት ፡ የዘፈን ፡ ቤት ፡ ይጋልብ ፡ ዠመር ፤ እንዳጋጣሚ ፡ ሲዘፍ
ኑና ፡ ሲጫወቱ ፡ አምሽተው ፡ ከሌሊቱ ፡ በ፲ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡
ከመኳንንቱና ፡ ከመሳፍንቱ ፡ ጋራ ፡ ስትወጣ ፡ ደረሰ ፡ ያም ፡ ጋሪ ፡
ነጂ ፡ ቀስ ፡ ብሎ ፡ ሰውነቱን ፡ ሳያስታውቅ ፡ ጋሪውን ፡ ጠጋ ፡
አድርጎ ፡ ይጠብቅ ፡ ዠመር ። እሷንም ፡ አንዱ ፡ መስፍን ፡ አብረን ፡
እንሂድ ፤ ሌላውም ፡ መኰንን ፡ አይሆንም ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ነው ፡
የምትሄድ ፡ እየተባባሉ ፡ ሲጨቃጨቁ ፡ እሷም ፡ አይሆንም ፡ ከማ
ንም ፡ ጋራ ፡ አልሄድም ፡ ብላ ፡ ተቈጥታ ፡ ከቀረበላት ፡ ጋሪ ፡
ላይ ፡ ወጣችና ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ ሂድ ፡ አለችው ። ያም ፡ ጋሪ ፡
ነጂ ፡ የሚፈልገውን ፡ በማግኘቱ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ፈረሱን ፡ እየገ
ረፈ ፡ ያለመጠን ፡ ያሮጠው ፡ ዠመር ፤ መኳንንቱና ፡ መሳፍንቱ ፡
ያለልክ ፡ ፈረሱን ፡ እየገረፈ ፡ በማሮጡ ፡ ገርሟቸው ፡ ከተመለ
ከቱ ፡ በኋላ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ የጤንነት ፡ አይደለም ፡ ይህ ፡ ሰው ፡
ሰክሯል ፡ ወይም ፡ አብዷልና ፡ ይህችን ፡ ሴት ፡ ገደል ፡ ሳያገባት ፡
እንከተለው ፡ ብለው ፡ ከየጋሪያቸው ፡ ወጥተው ፡ ተከተሉት ፤
ነገር ፡ ግን ፡ እሱ ፡ የሚጋልበው ፡ ሞቱን ፡ ለመፈለግ ፡ ነውና ፤
የነሱ ፡ ፈረስ ፡ የማይደርስበት ፡ ሆነ ። አንዳንድ ፡ ፈረስ ፡ እንኳ ፡
ቢጠጋው ፡ ይልቁንም ፡ ከኋላው ፡ የፈረስ ፡ ኰቴ ፡ በመስማቱ ፡
የፈረሱ ፡ ሩጫ ፡ እየጨመረ ፡ ይሄድ ፡ ዠመር ፤ መኳንንቱም ፡
ከጨለማው ፡ ጋራ ፡ ላይናቸው ፡ ስለ ፡ ራቃቸው ፡ አደጋውንም ፡
ስለ ፡ ፈሩ ፡ ቀስ ፡ ብለው ፡ ይከተሉ ፡ ዠመር ፤ ጋሪ ፡ ነጂ
ውም ፡ እንዳበደ ፡ ሰው ፡ ፈረሱን ፡ እየገረፈ ፡ ከጣና ፡ ባሕር ፡
ዳር ፡ ደንቀዝ ፡ ከሚባለው ፡ ደረሰ ፤ ገልመጥ ፡ ብሎ ፡ ቢያይ ፡

የሚያሳድዱት ፡ ሰዎች ፡ የሉም ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ጥምጥሙን ፡ ፈቶ ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ ጥሎ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ ዕወቂኝ ፡ አንቺ ፡ የጥፋቴ ፡ ሁሉ ፡ ምክንያት ፡ ካንቺ ፡ ጋራ አሁን ፡ ሕይወቴ ፡ ታልፋለች ፡ አላት ፤ እሷም ፡ በየችው ፡ ጊዜ ፡ ደንግጣ ፡ ማረኝ ፡ ማረኝ ፡ ብላ ፡ አንገቱ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተጠመጠመች ፡ ፈረሱን ፡ ከመ


ጫንያለው ፡ ወይዘሮ የውብ ፡ ሠፈርን ፡ ከጣና ፡ ባሕር ፡ እንደጣላት ።

ንገድ ፡ አውጥቶ ፡ ወደ ፡ ባሕሩ ፡ አጥብቆ ገረፈው ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ፈረሱ ፡ ደንብሮ ፡ ዘሎ ፡ ሁለቱንም ፡ ይዟቸው ፡ ከባሕር ፡ ውስጥ ፡ ሰጠመ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ የተገናኙበት ፡ ቀን ፡ እንዴት ፡ የተረገመ ፡ ነው ፤ እንደዚሁ ፡ ሞተው ፡ ቀሩ ፤ በምን ፡ አለቀ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈርና ፡ ያ ፡ ያልበደለው ፡ ጋሪ ፡ የሚስበው ፡ ፈረስ ፡ ሰጥመው ፡ ቀሩ ፤ እሱ ፡ ግን ፡ እርግጠኛ ፡ ሞት ፡ ሲመጣበት ፡ ጊዜ ፡ አብሬ ፡ እሞታለሁ ፡ ያለውን ፡ ዛቻ ፡ ረስቶ ፡ ለመውጣት ፡ ይጥር ፡ ዠመር ፤ ሰውዬውም፡ በጣም ፡ ዋና ፡ የሚያውቅ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ በብዙ ፡ ድካም ፡ ጣና ፡ ቂርቆስ ፡ ከምትባል ፡ ደሴት ፡ ወጣ ፡ በዝናብና ፡ በነፋስ ፡ በውርጭ ፡ ምክንያት ፡ ከባሕር ፡ ዳር ፡ አንገቱን ፡ ከጕልበቱ ፡ መካከል ፡ አድርጎ ፡ እየተንቀጠቀጠ ፡ የቤቱን ፡ ጥፋት ፡ የልጁንና ፡ የወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈርን ፡ በሱ ፡ ምክንያት ፡ መሞት ፡ እያሰበ ፡ ከብርድ ፡ ይልቅ ፡ የጸጸት ፡ ብርድ ፡ እያንዘፈዘፈው ፡ የሚያደርገውን ፡ አጥቶ ፡ ይቃትት ፡ ነበር ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ፺ ፡ ቀን ፡ ሲሆን ፡ ከወንዙ ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ አንዲት ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ እኽል ፡ ሳይበላ ፡ ውሃ ፡ ብቻ ፡ እየጠጣ ፡ ተቀመጠ ።

## ምዕራፍ ፡ ፳ ።

በሰባተኛውም ፡ ሱባኤ ፡ አንድ ፡ የስሜን ፡ መነኵሴ ፡ በሕርመትና ፡ በመከራ ፡ የከሱ ፡ ገርጥተው ፡ ብጫ ፡ የሚመስሉ ፡ ጢማቸው ፡ ከደረታቸው ፡ በታች ፡ የወረደ ፤ የመንፈሳቸው ፡ ግርማና ፡ ብርታት ፡ እጅግ ፡ የሚያስፈራ ፡ ከወገባቸው ፡ በታች ፡ የድኩላ ፡ ቄዳ ፡ ሌጦ ፡ ያሸረጡ ፡ በእጃቸው ፡ አንዲት ፡ ጕባጣ ፡ በትር ፡ የውሃ ፡ ቅል ፡ ያንጠለጠለች ፡ ይዘው ፡ ወደሱ ፡ መጡ ፤ ያም ፡ ጋሪ ፡ ነጂ ፡ እንደዚህ ፡ ያሉ ፡ የሚገርሙ ፡ ከዓለም ፡ መልክ ፡ የተለዩ ፡ የብርታት ፡ ደም ፡ ግባት ፡ ያላቸው ፡ ሰው ፡ በማየቱ ፡ ደንግጦ ፡ ወደሱ ፡ እስቲቀርቡ ፡ ይጠብቃቸው ፡ ነበር ።

መነኵሴውም ፡ ወደሱ ፡ ቀርበው ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ ምን ፡ ታደርጋለኽ ፡ በምንስ ፡ ምክንያት ፡ ወደዚህ ፡ መጣህ ፡ ብለው ፡ ጠየቁት ፡ ሰውዬውም ፡ አባቴ ፡ እኔ ፡ አንድ ፡ ሳልታመም ፡ ያበድኩ ፡ ሰው ፡ ነኝ ፡ የመጣሁበትም ፡ ምክንያት ፡ ሚስቴን ፡ ልጄን ፡ ቤቴን ፡ ደግሞ ፡ አንዲት ፡ ሀብታም ፡ ሴት ፡ የገደልኩ ፡ ዋና ፡ ኀጢአተኛ ፡ ነኝ ፤ መነኵሴውም ፡ ታዲያ ፡ ከዚህ ፡ ምን ፡ ታደርጋለኽ ።

ጋሪ ፡ ነጂው ፤ ከዚህ ፡ መምጣቴ ፡ ለኔም ፡ በጣም ፡ ገርሞኛል ፡ የኔ ፡ ሐሳብ ፡ ከጠላቴ ፡ ጋራ ፡ አብሬ ፡ ለመሞት ፡ ነበር ፤ ነገር

ግን ፡ ሞት ፡ ተፍቶኝ ፡ እነሆ ፡ በሠራሁት ፡ ሥራ ፡ ጸጸት ፡ ልቤን ፡ እየፋቀኝ ፡ እቃትታለሁ ።

መነኰሴው ፤ ልጄ ፡ ሆይ ፡ እነዚያ ፡ የገደልካቸው ፡ ሰዎች ፡ ባንተ ፡ ምክንያት ፡ ተጠቀሙ ፤ አንተ ፡ ግን ፡ በማይጠፋ ፡ እሳት ፤ በማይተኛ ፡ ትል ፡ በጸጸት ፡ እስከ ፡ ዕድሜ ፡ ልክኽ ፡ ትቃጠላለኽ ። ኋላም ፡ ከመቃብር ፡ ወደ ፡ ሥቃይ ፡ ትወርዳለኽ ፡ የገደልካቸው ፡ ሰዎች ፡ ደም ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ስለሚጮኽ ፡ ለኅሊናኽ ፡ ይሰማታልና ፡ ዕረፍት ፡ የሌለኽ ፡ ዘወተር ፡ የኰበለልክና ፡ የተቅበዘበዝክ ፡ ትሆናለኽ ።

ጋሪ ፡ ነጂው ፤ አባቴ ፡ እባክዎ ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡ ይሻላል ።

መነኰሴው ፤ የሚሻልኽ ፡ ሌላ ፡ መንገድ ፡ የለም ፡ ይኸውም ፡ ራስኽን ፡ በራስኽ ፡ በጽኑ ፡ በብርቱ ፡ ንስሐ ፡ መግደል ፡ ነው ።

ጋሪ ፡ ነጂው ፤ ራስን ፡ በራስ ፡ መግደል ፡ ማለት ፡ በገደል ፡ ወይም ፡ በባሕር ፡ ወደቄ ፡ መሞት ፡ ነውን ።

መነኰሴው ፤ አይደለም ፡ ራስኽን ፡ በራስኽ ፡ ማለት ፡ በመከራ ፡ መጣሪያ ፡ ደመኛው ፡ እንደሚገድለው ፡ ሰው ፡ አንተም ፡ እራስኽን ፡ በራስኽ ፡ በንስሓ ፡ በብርቱ ፡ መከራ ፡ መግደል ፡ ነው ።

ጋሪ ፡ ነጂው ፤ ይህንን ፡ መከራ ፡ የማገኘው ፡ ከዚህ ፡ ሆኜ ፡ ነውን ፡ ወይስ ፡ ከሌላ ፡ ሥፍራ ፡ ነው ።

መነኰሴው ፤ ከዚህ ፡ አይደለም ፡ ቦታውን ፡ እኔ ፡ አመለክትኻለሁ ። ደኅና ፡ አድርገኽ ፡ ስማኝ ፡ ስሜን ፡ ከተራራው ፡ ጫፍ ፡ ቧሒት ፡ አጠገብ ፡ አባ ፡ ያሬድ ፡ ከሚባለው ፡ ሥፍራ ፡ ሂደኽ ፡ ውደቅ ከዚያው ፡ እንደ ፡ ደረስኽ ፡ የተሰወሩ ፡ መነኰሳት ፡ በዜማ ፡ ሲያዜሙ ፡ መንፈሳዊ ፡ ድምፅ ፡ ትሰማለኽ ፤ ከዚያም ፡ ፫ ፡ ቀን ፡ ካደርክ ፡ በኋላ ፡ ያችን ፡ ሴት ፡ በሚያሳዝን ፡ ሥቃይ ፡ እንደ ፡ ገደልካት ፡ ያለ ፡ አሣሣት ፡ በመንፈስ ፡ ይደርስብኻል ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ደም ፡ በደም ፡ ይነጻል ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ አንተ ፡ በሥጋ ፡ በጕልሕ ፡ እንደ ፡ ገደልካት ፡ እሷም ፡ በርቀት ፡ በመንፈስ ፡ ትገድልኻለች ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ እውነተኛውን ፡ ሥርየት ፡ ታገኛለኽ ።

ጋሪ ፡ ነጂው ፤ አባቴ ፡ በጣም ፡ የረቀቀ ፡ ነገር ፡ ስለ ፡ ሆነብኝ ፡ ምንም ፡ አልገባኝም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ከዚህ ፡ ተቀምጬ ፡

ጸጸት ፡ ልቤን ፡ ከሚፍቀኝ ፡ አባቴ ፡ እንደ ፡ መከሩኝ ፡ ወደ ፡ ስሜን ፡ ብሄድና ፡ ብሞት ፡ የተሻለ ፡ ነው ። እንሆ ፡ አራት ፡ ቀኔ ፡ ነው ፤ ከውሃ ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ አልቀመስኩም ፤ ስለዚህ ፡ በጣም ፡ ደክሞኛልና ፡ እደርስ ፡ አይመስለኝም ።

መነኵሴው ፡ ከበትራቸው ፡ ላይ ፡ ቅላቸውን ፡ አውርደው ፡ እንሆ ፡ ከዚህ ፡ ውሃ ፡ ጠጣ ፡ ይህ ፡ ውሃ ፡ የተቀደሰ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ እስከምትደርስበት ፡ ቦታ ፡ ኃይልና ፡ ጽንዕ ፡ ይሆንኻል ፡ ብለው ፡ ሰጡት ፡ እሱም ፡ ሁለት ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ከተጐነጨ ፡ በኋላ ።

መነኰሴው ፡ ስምኽ ፡ ማነው ፡ ብለው ፡ ጠየቁት ፡ እሱም ፡ ስሜ ፡ ጫን ፡ ያለው ፡ ይባላል ፤ አገሬም ፡ ጋይንት ፡ ነው ፡ አላቸው ።
መነኵሴው ፤ የውነተኛውን ፡ ስምኽን ፡ ስሜን ፡ ቧሒት ፡ ከሚባለው ፡ ተራራ ፡ ሥር ፡ በደረስኽ ፡ ጊዜ ፡ ሚስትኽ ፡ ትነግርኻለች።

ጋሪ ፡ ነጂው ፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡ ከዚያ ፡ ትመጣለችን ።

መነኵሴው ፡ አዎን ፡ ትመጣለች ፡ ብለውት ፡ ከፊቱ ፡ ተሰወሩበት ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጋሪ ፡ ነጂው ፡ አገጩን ፡ ይዞ ፡ ጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ከተገረመና ፡ ከተጨነቀ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ስሜን ፡ ጉዞውን ፡ ገሠረ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ወይ ፡ ግሩም ፡ ይህነን ፡ የረቀቀ ፡ የመንፈሳዊ ፡ ኑሮ ፡ ግዙፍ ፡ የሆነ ፡ የሥጋዊ ፡ ዐይን ፡ ሳያየው ፡ በመቅረቱ ፡ በጣም ፡ ያሳዝናል ፤ ስለዚህ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ከንቱ ፡ በሆነ ፡ ዓለም ፡ ጨለማ ፡ ውስጥ ፡ በዳሰሳ ፡ ይኖራል ። እንግዴህ ፡ ከፍ ፡ ያለው ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ ይህነን ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ሰማያዊ ፡ ኑሮ ፡ ካላየ ፡ ከእንስሳ ፡ ምን ፡ ይበልጣል ፤ ወንድሜ ፡ እባክኽ ፡ ታሪክኽን ፡ ጨርስልኝ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ርግጥ ፡ ነው ፡ የሰው ፡ ባሕርይ ፡ ዘወትር ፡ «በዱር ፡ ካሉ ፡ ዐሥር ፡ ወፎች ፡ በእጅ ፡ የተያዘ ፡ አንድ ፡ ወፍ ፡ ይሻላል » ፡ የተባለውን ፡ ምሳሌ ፡ ስለሚመርጥ ፡ ልዑል ፡ ቅድም ፡ እንዳልከው ፡ ከፍ ፡ ያለውን ፡ ረቂቁን ፡ ነገር ፡ ባለማየት ፡ በእጁ ፡ የያዛትን ፡ ትንሽ ፡ ዓለም ፡ ለማግኘት ፡ ርስ ፡ በርሳቸው ፡ ይተናነቁባታል ፤ ስለዚህ ፡ ማር ፡ ይስሐቅ ፡ "ዓለም ፡ ሆይ ፡ ሌቦችና ፡ ቀማኞች ፡ የሚካፈሉሽ" ፡ ይላል ፤ እንግዴህ ፡ የዓለምን ፡ ከንቱነት ፡ እንተውና ፡ ወደ ፡ ታሪካችን ፡ እንመለስ ።

ይህ ፡ ጫን ፡ ያለው ፡ ስምንት ፡ ቀን ፡ ያኽል ፡ ወደ ፡ ስሜን ፡ ከተጓዘ ፡ በኋላ ፡ ከጢቱ ፡ ባንድ ፡ ሰዓት ፡ ቢሒት ፡ ከሚባለው ፡ ተራራ ፡ ሥር ፡ ደረሰ ፤ ወዲያው ፡ አባ ፡ ያሬድ ፡ ከሚባለው ፡ ሸለቆ ፡ ሥር ፡ ተቀምጦ ፡ በዙሪያው ፡ ያለውን ፡ አገር ፡ ፀማየት ፡ የአንክሮ ፡ ጸሎት ፡ ያደርግ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ ከዚያው ፡ እንዳደረ ፡ በበረዶውና ፡ በውርጩ ፡ ምክንያት ፡ ሰውነቱ ፡ እንደ ፡ በረዶ ፡ ቀዘቀዘ ፡ እጁም ፡ እግሩም ፡ ለመላወስ ፡ አልቻለም ። በውርጩ ፡ ምክንያት ፡ መንቀጥቀጥ ፡ እንኳ ፡ የማይችል ፡ ሆነ ፤ ይኸውም ፡ እሱ ፡ ራሱ ፡ በረዶ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ነው ፤ ዕንባም ፡ ጠፋ ፤ ብቻ ፡ በዕብነ ፡ በረድ ፡ እንደ ፡ ተሠራ ፡ ሐውልት ፡ በገላው ፡ ላይ ፡ በረዶ ፡ ፈልቶበት ፡ ነጭ ፡ ሆኖ ፡ አንገቱን ፡ በጕልበቱ ፡ መካከል ፡ አድርጎ ፡ ሚስቴ ፡ መቼ ፡ ትመጣ ፡ ይሆን ፡ እያለ ፡ ሲያስብ ፡ በሩቁ ፡ ወደ ፡ ውሃ ፡ ምንጭ ፡ እንደሚናፍቅ ፡ ዋሊያ ፡ አቤቱ ፡ ነፍሴ ፡ ወዳንተ ፡ ትናፍቃለች ፡ የሚል ፡ ድምፅ ፡ ሰማ ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ የመንፈስ ፡ ኀዘን ፡ ተሰምቶት ፡ ለማልቀስ ፡ ቢሞክር ፡ አልሆነለትም ፤ ወዲያው ፡ ቀጥሎ ፡ በግዕዝ ፡ ቋንቋ ፡

ከመ ፡ ያፈቅር ፡ ኀየል ፡ ኀበ ፡ አንቅዕተ ፡ ማያት ፡
ከማሁ ፡ ታፈቅር ፡ ነፍስየ ፡ ኀበ ፡ እግዚአብሔር ፡
ጸምአት ፡ ነፍስየ ፡ ኀበ ፡ አምላኪየ ፡ ሕያው ፡

የሚል ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ በጣም ፡ ተነክቶ ፡ እየተንከባለለ ፡ ወይኔ ፡ ኀጢአተኛው ፡ ሰው ፡ መጨረሻዬ ፡ ምን ፡ ይሆን ፡ እያለ ፡ ደረቅ ፡ ልቅሶ ፡ እያለቀሰ ፡ ከተንፈራፈረ ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ሰመመን ፡ እንቅልፍ ፡ ሽልብ ፡ አደረገው ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ እባክ ፡ ወንድሜ ፡ መጨረሻው ፡ ምን ፡ ይሆን ። ስንኳን ፡ እሱ ፡ እኔም ፡ ተጨነቅሁ ፡ እያለ ፡ ያለቅስ ፡ ገርመር ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ እንግዲህ ፡ መጨረሻውን ፡ ልሰማው ፡ ነውና ፡ አትጨነቅ ፡ አታልቅስ ፡ ላንተም ፡ ትልቅ ፡ ትምህርት ፡ ስለሆነ ፡ ደህና ፡ አድርገኽ ፡ ስማኝ ። ይህ ፡ ሰው ፡ በጠለቀ ፡ እንቅልፍና ፡ በብርቱ ፡ ድካም ፡ ተውጦ ፡ ሲያንጐላጅ ፡ ከተራራው ፡ ጫፍ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ አንድ ፡ ሕፃን ፡ ልጅ ፡ በቀኝ ፡ እጅዋ ፡ ይዛ ፡ በብርቱ ፡ ድምፅ ፡ አቶ ፡ ዐቅሙን ፡ አያውቅ ፤ አቶ ፡ ዐቅሙን ፡ አያውቅ ፡ እያለች ፡ ስትጠራ ፡ በሕልሙ ፡ አየ ፤ እሱም ፡ በሕልሙ ፡ አቶ ፡ ዐቅሙን ፡ አያውቅ ፡ ማነው ፤ አንቺስ ፡ ማነሽ ፡ ብሎ ፡ ጠየቃት ፡

እሷም ፡ አቶ ፡ ዐቅሙን ፡ አያውቅ ፡ አንተ ፡ ነኽ ፡ እሔም ፡ ሚስትኽ ፡ ነኝ ፡ አለችው ።

ጋሪ ፡ ነጂው ፤ እኔ ፡ ደክሞኛል ፡ እባክሽ ፡ አንቺ ፡ ልጄን ፡ ይዘሽ ፡ ወደኔ ፡ ነዪልኝ ።

ሚስቱም ፡ እኔ ፡ ልጅኽን ፡ ይዤ ፡ ወዳንተ ፡ ለመምጣት ፡ አልችልም ። ስለ ፡ ምን ፡ በኔና ፡ ባንተ ፡ መከከል ፡ ትልቅ ፡ ተራራ ፡ አለ ፡ ብላ ፡ መለሰችለት ። ያን ፡ ጊዜ ፡ በሕልሙ ፡ እያለቀሰ ፡ ተራራውን ፡ ለመውጣት ፡ ሲቧጥጥ ፡ ወደ ፡ ሚስቱም ፡ ቈዩኝ ፡ አትሂጂ ፡ መጣሁ ፡ እያለ ፡ ሲጮኽ ፡ አንድ ፡ ዳለቻ ፡ ፈረስ ፡ ጋሪ ፡ እየሳበ ፡ በንቃትና ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡ እርምጃ ፡ ወደሱ ፡ ሲመጣ ፡ አየ ። ጋሪ ፡ ነጂው ፡ ግን ፡ ተሸፍኖ ፡ መልኩ ፡ አይታይም ፡ ነበር ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ጫን ፡ ያለው ፡ ጋሪ ፡ ነጂውን ፡ እባክኽ ፡ ጌታዬ ፡ ሚስቴና ፡ ልጄ ፡ ካፋፍ ፡ ሆነው ፡ ይጠሩኛልና ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ አድርሰኽኝ ፡ ተመለስ ፡ እያለ ፡ ይለምነው ፡ ዠመር ። ጋሪ ፡ ነጂውም ፡ በቃሉ ፡ ሳይመልስለት ፡ ራሱን ፡ እያነቃነቀ ፡ በእጁ ፡ መቀመጫውን ፡ እያሳየ ፡ መፍቀዱን ፡ በምልክት ፡ አሳየው ፤ ጫን ፡ ያለውም ፡ ደስ ብሎት ፡ በችኰላ ፡ እየተንፏቀቀ ፡ ከጋሪው ፡ ላይ ፡ ወጣ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ የሚገርም ፡ ሕልም ፡ ነው ። እስቲ ፡ እባክኽ ፡ አውጋኝ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ያ ፡ ፈረስ ፡ ቀጥ ፡ ያለውን ፡ በበረዶ ፡ የተሸፈነውን ፡ ተራራ ፡ በሚያስደንቅ ፡ አወጣጥ ፡ እየጋለበ ፡ ይወጣ ፡ ዠመር ፤ ጋሪ ፡ ነጂውም ፡ ፍጥነቱ ፡ እንዳያቋርጥ ፡ ይገርፈው ፡ ነበር ። በብዙ ፡ ድካምና ፡ ጭንቅ ፡ ከተራራው ፡ ጫፍ ፡ ከሚስቱና ፡ ከልጁ ፡ አጠገብ ፡ ሲደርስ ፡ ጋሪ ፡ ነጂው ፡ የተከናነበበትን ፡ ጨርቅ ፡ አንሥቶ ፡ ቢጥለው ፡ ያች ፡ የጐንደር ፡ ዘፋኝ ፡ ወይዘሮ ፡ የውብ ፡ ሰፈር ፡ ከጣና ፡ ባሕር ፡ ወስዶ ፡ የጣላት ፡ ሆና ፡ ታየችው ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ጫን ፡ ያለው ፡ እሷን ፡ በማየቱ ፡ ደንግጦ ፡ እኅቴ ፡ ማሪኝ ፡ አጥፍቻለሁ ፡ እያለ ፡ ከጋሪው ፡ ውስጥ ፡ እጁን ፡ አሾልኮ ፡ አንገቷን ፡ ይዞ ፡ ሲለምናት ፡ ሴቲቱም ፡ አንተ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ባንተ ፡ ዐቅምህን ፡ ባለማወቅ ፡

በኋም ፡ ማዋረድ ፡ ምክንያት ፡ በሥቃይ ፡ እንደ ፡ ገደልከኝ ፡ አን ተም ፡ በሥቃይ ፡ መሞት ፡ ይገባኻል ፡ ብላ ፡ የፈረሱን ፡ አንገት ፡ በልጓም ፡ ስባ ፡ ወደ ፡ ቍልቍል ፡ መለሰችው ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ እንደ፡ ናዳ ፡ እየተንከባለሉ ፡ ወረዱና ፡ አባ ፡ ያሬድ ፡ ከሚባለው ፡ ሸለቆ ፡ በታች ፡ ሲወድቁ ፡ ደንግጦ ፡ ከእንቅልፉ ፡ ብንን ፡ አለ ። ይህ ፡ በኀ ዘን ፡ በጸጸት ፡ በችግርና ፡ በመከራ ፡ ሥጋው ፡ ተፍቆ ፡ በኸማቱና ፡ በዐ፥ሙ ፡ የቆመ ፡ ችግረኛ ፡ በሕልሙ ፡ በደረሰበት ፡ ጽኑ ፡ ሥቃይ ፡ ምክንያት ፡ በፈረስ ፡ ሆኖ ፡ ባለጋራው ፡ እንዳሳደደው ፡ ሰው ፡ ደክ ሞት ፡ እየቃተተ ፡ የድካም ፡ ትንፋሽ ፡ ከተነፈሰ ፡ በኋላ ፡ ሞተ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ እንደ ፡ ምን ፡ የሚሳዝን ፡ ነገር ፡ ነው ፡ እባ ክኽ ፡ ወንድሜ ፤ ይህ ፡ ሰው ፡ በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ሥቃይ ። ካረፈ ፡ በኋላ ፡ ንስሓ ፡ ይሆንለታልን ፡ እንዴታ ፡ ቀድም ፡ እንዳጫወትኩኽ ፡ ጣና ፡ የተገናኘቸው ፡ መነኰሴ ፡ ፍጹም ፡ ንስሓ ፡ እንደሚሆነው፡ ነግረውታል ፤ ምክንያቱም ፡ ይህ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ተመልሶ ፡ በማይታወቅበት ፡ ዓለም ፡ ውስጥ ፡ በደስታ ፡ አልኖረም ፤ ወይም፡ ጸዱር ፡ በገደል ፡ ኰብሎ ፡ በዘበኛ ፡ ተይዞ ፡ አልተደበደበም ፤ ራሱን ፡ በራሱ ፡ በመከራ ፡ አስጨንቆ ፡ በመንፈሱ ፡ ደበኛው ፡ እንደሚገድለው ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ በሰፈረበት ፡ ቍና ፡ በፈቃዱ ፡ ተሰፈረ ፡ ስለዚህ ፡ በእግዚአብሔር ፡ ፊት ፡ በፍጹም ፡ የተመሰ ገነ ፡ መሥዋዕት ፡ መሆኑን ፡ ይህነን ፡ የመከሩት ፡ መነኰሴ ፡ ነግ ረውኛል ፤ እንግዴህ ፡ ልዑል ፡ ሆይ ፡ ቀኑም ፡ መሸ ፡ ወደ ፡ ጐን ደር ፡ እንመለስ ፡ ደግሞ ፡ ፀሌላ ፡ ጊዜ ፡ ተገናኝተን ፡ እንጨ ዋወታለን ።

ልዑል ፡ ያዕቆብና ፡ ልጅ ፡ መስፍን ፡ ወደ ፡ ጐንደር ፡ ከተማ ፡ ተመለሱ ።

## ምዕራፍ ፯ ።

ነገር ፡ ግን ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ የቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ኑሮና ፡ የሱ ፡ ሐሳብ ፡ በጣም ፡ የተራራቀና ፡ በጎሊና ፡ ውስጥ ፡ የመንፈስ ፡ ጦርነት ፡ የሚያስነሣ ፡ በመሆኑ ፡ ብርቱ ፡ ደዌ ፡ ወደቀበትና ፡ ከቤት፡ ዋለ ። ሕመሙም ፡ እየጠነከረ ፡ ሄደ ፤ ዕለት ፡ በዕለት ፡ እየከሳና ፡ እየገረጣ ፡ እየደከመ ፡ ሲሄድ ፡ የግድ ፡ ባልጋው ፡ ላይ ፡ የሚያስ ተኛው ፡ ሆነ ። አሁንም ፡ ቢሆን ፡ ብርቱ ፡ የመንፈስ ፡ ኀዘን ፡ ስላለበት ፡ እንደ ፡ ተጋደመ ፡ ዕንባውን ፡ ያፈስ ፡ ነበር ።

ምክንያቱም ፡ አባቱ ፡ በከንቱ ፡ ውዳሴና ፡ በዘፈን ፡ በማደና ገር ፡ ሰው ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነና ፡ ደስታ ፡ በሽታ ፡ መሆኑን ፡ ባለማወቁ ፡ ነው ። ይልቁንም ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ በጣም ፡ ዋና ፡ ኀዘኑ ፡ የዚህን ፡ ዓለምም ፡ ኑሮ ፡ ያስጠላው ፡ ዐፄ ፡ ዳዊት ፡ ሃይ ማኖቱ ፡ ቅባት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፤ በጕርጕራ ፡ ያሉትን ፡ የተዋሕዶ ፡ ሃይማኖት ፡ ሊቃውንትና ካህናት ቀሳውስት ፡ በጭካኔ ፡ በአረመኔ ነት ፡ ጃዊ ፡ በሚባል ፡ የዘበኛ ፡ አለቃው ፡ እጅ ፡ በሥቃይ ፡ ንጹሕ ፡ ደም ፡ በማፍሰሱ ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ኀዘን ፡ ነበረበት ።

ዐፄ ፡ ዳዊትና ፡ ንግሥቲቱ ፡ በልጃቸው ፡ ሕመም ፡ በጣም ፡ ተጨንቀው ፡ ከየሀገሩ ፡ ባለመድኀኒት ፡ እያስመጡ ፡ሞከሩት ፤ ግን ፡ ምንም ፡ የተሻለው ፡ ነገር ፡ የለም ።

በመጨረሻው ፡ ቀን ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ደወል ፡ ይደውላል ።
አሽከር ፡ ይገባል ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ እባክኽ ፡ ልጅ ፡ መስፍንን ፡ ጥራልኝ ።
ልጅ ፡ መስፍን ፡ ይገባል ።
ልጅ ፡ መስፍን ፡ ተቀመጥ ።
ልጅ ፡ መስፍን ፡ ካጠገቡ ፡ በወንበር ፡ ይቀመጥና ፡ ጌታዬ ፡
እንደ ፡ ምንድነኽ ፡ በጎ ፡ ነኽን ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ በጣም ፡ አሞኛል ። እኔ በጽኑ ፡ ሕመሜና ፡ ኀዘኔ ፡ ምክንያት ፡ በሰዓት ፡ በደቂቃ ፡ በሰኮ ንድ ፡ እየደከምኩ ፡ ሄድኩ ። ሰው ፡ በሕመም ፡ በኀዘን ፡ እየበራ ፡ እየቀለጠ ፡ የሚያልቅ ሻማ ፡ ነው ፤ እንግዴህ ፡ እኔ ፡ የምጠብ ቀው ፡ የሕይወቴ ፡ መብራት ፡ የምትጠፋበትን ፡ ቀን ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ለመኖር ፡ ተስፋ ፡ የለኝም ።

ልጅ ፡ መስፍን ፡ አገጩን ፡ በጁ ፡ ይዞ ፡ ዕንባው ፡ እየፈሰሰ ፡ ወዳጄ ፡ ያዕቆብ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ የፍቅር ፡ ብርሃን ፡ ሳትጨልም ፡ እኔን ፡ ወዳጅኽን ፡ ይደናገረኛልና ፡ በጊዜ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ተራራ ፡ ልሂድ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፤ ወዳጄ ፡ አትሂድ ፡ እኔም ፡ ብሞት ፡ ላባ ባና ፡ ለማማ ፡ አደራ ፡ እላቸዋለሁ ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ ልዑል ፡ ሆይ ፡ እኔ ፡ ላባትና ፡ ለናት ፡ በደራ ፡ የምትላለፍ ፡ ዕቃ ፡ አይደለሁም ፤ አንተን ፡ ስወድኽ ፡ የደስታዬ ፡ ሁሉ ፡ መጨረሻ ፡ እንድትሆነኝ ፡ አስቤ ፡ ቈርጨ ፡ ነው ። አንተን ፡ ወዳጄን ፡ ሳጣ ፡ የጐንደርን ፡ ከተማ ፡ ዘወር ፡ ብዬ ፡ ባያት ፡ እንደ ፡ ሎጥ ፡ ሚስት ፡ የጨው ፡ ዐምድ ፡ እንደምሆን ፡ አይጠረጥርም ። እንግዴህ ፡ የደስታዬ ፡ ሁሉ ፡ መጨረሻ ፡ ያዕቆብ ፡ ወዳጄ ፡ ደኅና ፡ ሰንብት ፡ ብሎ ፡ እያለቀሰ ፡ አፉን ፡ ስሞት ፡ ተነሣ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ምነው ፡ ወዳጄ ፡ ሳልሞት ፡ ጥለኸኝ ፡ ትሄዳለኽ ፡ እያለ ፡ ያለቅስ ፡ ዠመር ።

ልጅ ፡ መስፍን ፤ መብራቴ ሳትጠፋ ፡ ሲታየኝ ፡ እሄዳለሁ ፤ እንግዴህ ፡ በሰማይ ፡ እንገናኝ ፡ ብሎት ፡ እያለቀሰ ፡ ወጣ ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ካልጋው ፡ ላይ ፡ ተጋድሞ ፡ የመረረ ፡ ልቅሶ ፡ ያለቅስ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ በብዙ ፡ አተኰሰው ፤ በትኵሳቱም ፡ ምክንያት ፡ ራሱ ፡ ዞሮ ፡ ይቃዥ ፡ ዠመር ። ልዑል ፡ ያዕቆብን ፡ የሚያስታምመው ፡ አሽከር ፡ ገብቶ ፡ ቢያየው ፡ እየተወራጨ ፡ እንደ ፡ ቅዠት ፡ ይናገራል ፤ ደረቱን ፡ በእጁ ፡ ቢዳብሰው ፡ ትኵሳቱ ፡ ከልክ ፡ ያለፈ ፡ ሆኖ ፡ ልቡም ፡ በጣም ፡ ይመታል ። አስተማሚውም ፡ ጌታዬ ፡ ምን ፡ ሆንኽ ፡ እያለ ፡ በሽታውን ፡ ለማወቅ ፡ ቢጠይቀው ፡ ዐይኑ ፡ እየተንከራተተ ፡ እንደ ፡ መሣቅ ፡ እንደ ፡ ማልቀስም ፡ ይል ፡ ዠመር ፤ አስታማሚው ፡ ደነገጠና ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ሮጦ ፡ በሩን ፡ ከፍቶ ገባ ።

ንጉሡና ፡ ንግሥቲቱም ፡ ከነፍስ ፡ አባታቸው ፡ ከመምህር ፡ ደስታ ፡ ጋራ ፡ የልዑል ፡ ያዕቆብን ፡ በሽታ ፡ ነገር ፡ ሲያወጡ ፡ ሲያወርዱ ፡ በድንገት ፡ በሩን ፡ ከፍቶ ፡ ስለ ፡ ገባ ፡ ደንግጠው ፡ ንጉሡ ፡ ልጄ ፡ ምን ፡ ሆነ ፡ ብለው ፡ ጠየቁት ።

አስታማሚው ፤ ግርማዊ ፡ ሆይ ፡ ጥቂት ፡ አተኵሶት ፡ አሞታል ፤ በትኵሳቱም ፡ ምክንያት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አላውቅም ፡ ዐይኑን ፡ እያንከራተተ ፡ እንደ ፡ ቅዠት ፡ ይሞክረዋል ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ዐፄ ፡ ዳዊትና ፡ ንግሥቲቱ ፡ መምህር ፡ ደስታም ፡ በፍጥነት ፡ ወደ ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ሄዱ ፤ እንደ ፡ ገቡም ፡ ከራስጌው ፡ ቆመው ፡ እየተመለከቱት ፡ ያለቅሱ ፡ ነበር ። ወዲያው ፡ ዐፄ ፡ ዳዊት ፡ የልጃቸውን ፡ እጅ ይዘው ፡ የተወደድኽ ፡ ልጄ ፡

ሆይ ፡ ምን ፡ አገኘኽ ፡ እያሉ ፡ እየዳበሱ ፡ እያለቀሱ ፡ ሲስሙት ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ካንገቱ ፡ ቀና ፡ አለና ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ትኵር ፡ ብሎ ፡ እያየ ፡ እንደ ፡ ቅዠት ፡ አባባ ።

በሩቅ ፡ ይታየኛል ፡ ዙፋኑን ፡ ዘርግቶ ፡
ደመና ፡ ከስሩ ፡ ተጅመልምሎ ፡ ወጥቶ ፡
አይቼ ፡ አላውቅም ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ከቶ ።

ንጉሥ ፡ በግ ፡ ተቀምጧል ፡ በክብሩ ፡ መንበር ፤
እልፍ ፡ አእላፋት ፡ ቅዱሳን ፡ ይሰግዱ ፡ ዠመር ፤
እየጮኹ ፡ አሉ ፡ ይገባል ፡ ለበጉ ፡ ምስጋናና ፡ ክብር ።

የሚገርም ፡ ነገር ፡ አያለሁ ፡ በሩቅ ፤
አደባባዩ ፡ በወርቅ ፡ የሚያንጸባርቅ ።

በውነት ፡ ያስገርማል ፡ ያዳራሹ ፡ ሥራ ፤
መብራቱም ፡ እሱ ፡ ነው ፡ የብርሃኑ ፡ ጮራ ።

ቸር ፡ ነው ፡ ደግ ፡ ነው ፡ አዛኝም ፡ ነው ፡ እውነተኛ ።
ፈራጅ ፡ ነው ፡ ሀዋቂ ፡ ነው ፡ አይሳሳትም ፤
እኛ ፡ የሰው ፡ ልጆች ፡ ሩኅች ን ፡ ከንቱ ፡ አንደርስበትም ።

ለሚፈልገው ፡ ሰው ፡ በውነት ፡ ለሚሻው ፡
እሱ ፡ የሚገኘው ፡ ከድኾች ፡ ጋር ነው ።

ጽድቅ ፡ ቸርነት ፡ ፍቅር ፡ ፍርድ ፡ ናቸው ፡ ያልጋው ፡ ሸንኮሮች ፡
አባባ ፡ ምነው ፡ ባንከፋ ፡ ምነው ፡ ባንሰንፍ ፡ ምነው ፡ ባንሰለች ።

ከዚያ ፡ ቀንና ፡ ሌት ፡ አይለዋወጡም ፤
ኀዘንና ፡ ተድላ ፡ አይፈራረቁም ።

ከዚያ ፡ ሥሥት ፡ የለም ፡ ሰውን ፡ የሚያጣላ ፤
ከዚያ ፡ ሕመም ፡ የለም ፡ በላዩ ፡ አያርፍም ፡ ክፉ ፡ የሞት ፡ ጥላ ።

አባባ ፡ የሞት ፡ ወንዝን ፡ ባሕር ፡ ተሻግረን ፡ ስንወጣ ፡ ኀዘን ፡ ልቅሶ ፡ ጸጸት ፡ ችግር ፡ ወደኛም ፡ አይመጣ ፡ እያለ ፡ ዕቃ ፡ እንደሚፈልግ ፡ ሰው ፡ ዐይኑ ፡ ይቅበዘበዝ ፡ ነበር ። ንግሥቲቱ ፡ የልጅዋን ፡ በግጥም ፡ መቃዠትና ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ አዲስ ፡ የሆነ ፡ የሚያስጨንቅ ፡ ነገር ፡ በማየቷ ፡ የከበደ ፡

ኀዘን ፡ ወድቆባት ፡ በጕልበቷ ፡ ተንበርክካ ፡ የልጅዋን ፡ እጅ ፡ ይዛ ፡ ልጄ ፡ ያዕቆብ ፡ ምን ፡ አገኘኽ ፡ ይህነን ፡ ያንተን ፡ ሥቃይ ፡ ከማየት ፡ ምነው ፡ እኔ ፡ ሞቼ ፡ በሆነ ፡ እያለች ፡ የመረረ ፡ ልቅሶ ፡ ስታለቅስ ፡

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ወደ ፡ እናቱ ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ እማማ ፡
እዩ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ከደመናው ፡ ላይ ፡

ድንግል ፡ ትታያለች ፡ ቆማ ፡ ከጨረቃው ፡ ላይ ፡
እጆቿን ፡ አጣምራ ፡ ዐይኗ ፡ ዕንባ ፡ ሞልቶ ፡ ሰቅላ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡
ትለምናለች ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ሁሉ ፡ ማንንም ፡ ሳትለይ ።

ስለምን ፡ ነው ፡ እማማ ፡ የምትኖሪው ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ጨለማ ፡
ከፊትሽ ፡ እያየሽ ፡ እንዲህ ፡ የምታምር ፡ የብርሃን ፡ ዓላማ ።

አትከተይም ፡ ወይ ፡ አንቺስ ፡ እምቤትሽን ፡
ስለ ፡ ምን ፡ አልተውሽም ፡ ባል ፡ ማግባትሽን ።

እኔም ፡ ባልወለድ ፡ ይሻለኝ ፡ ነበረ ፤
ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ኑሮ ፡ እንዲህ ፡ ከመረረ ።

አባባና ፡ እማማ ፡ እንዴት ፡ ብርቱ ፡ ናቸው ።

የዚህ ፡ ዓለም ፡ ክብደት ፡ የማይሰማቸው ።
መንግሥት ፡ አሳብ ፡ ጭንቀት ፡ ምጥ ፡ ሞት ፡ ነግሠው ፡ ከቤታቸው ፡
ያለባብሱታል ፡ ሰው ፡ እንዳያውቅባቸው ።
ብሎ ፡ እጅና ፡ እግሩን ፡ ዘርግቶ ፡ የድካም ፡ ትንፋሽ ፡ ይተነፍስ ፡ ዠመር ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ንግሥቲቱ ፡ ደንግጣ ፡ መምህር ፡ ምነው ፡ ዝም ፡ ብለው ፡ ያያሉ ፡ ልጄ ፡ መሞቱ ፡ አይደለም ፡ እባክዎ ፡ ኪዳን ፡ እየደገሙ ፡ በእጅዎ ፡ ይዳብሱት ፡ እያለች ፡ ታለቅስ ፡ ዠመር ።

መምህር ፡ ደስታም ፡ ኪዳን ፡ እየደገሙ ፡ ሰውነቱን ፡ በእጃቸው ፡ ይዳብሱት ፡ ነበር ።

ከጥቂት ፡ ደቂቃ ፡ በኋላ ፡ ብንን ፡ ብሎ ፡ መምህር ፡
እጅዎን ፡ ያንሡልኝ ፡ ደም ፡ ደም ፡ ይሸተኛል ፤
ተባብረው ፡ የሠሩት ፡ ኃጢአት ፡ ያለ ፡ ይመስለኛል

ክብርዎን ፡ ለገንዘብ ፡ ከለወጡ ፡ ወዲህ ፡
አባቴ ፡ አይረቡም ፡ እርስዎ ፡ እንግዴህ ።

ጕርጕራ ፡ ከሚዳው ፡ የፈሰሰው ፡ ደም ፡
ይጮኻል ፡ ወደግዜር ፡ ዝምም ፡ አይልም ።

አባቴ ፡ ይመስልዎታል ፡ ወይ ፡ እሱን ፡ ሊያታልሉ ፡
የወንድሜ ፡ ጠባቂ አይደለሁም ፡ ሊሉ ።

መምህር ፡ ሆይ ፡ አይታይዎም ፡ ወይ ፡ ዙፋን ፡ ተዘርግቶ ፡
በሰማይ ፡ በምድር ፡ መላእክት ፡ ሞልቶ ።

በጉ ፡ ማጭድ ይዞ ፡ ቆሞ ፡ ይመለከታል ፡
ስንዴውን ፡ ከንክርዳድ ፡ ሊለየው ፡ ይመስላል ።

በሩቅ ፡ ይሰማኛል ፡ ሕፃናት ፡ ሲጮኹ ፡ ፍርድ ፡ ሲጠይቁ ።
ተቀላቅለው ፡ አየሁ ፡ ጕርጕራ ፡ ከሚዳው ፡ በግፍ ፡ የወደቁ ።

አባቴ ፡ ሆይ ፡ ዴማስ ፡ በሩቅ ፡ ሆኖ ፡ ይጠራዎታል ፤ ይተዉኝ ፡ ይሂዱ ፡ ከፊቴ ፡ የዚህ ፤ ዓለም ፡ ገንዘብ ፡ ያመልጥዎታል፡ ብሎ ፡ ከልጋው ፡ ላይ ፡ በዠርባው ፡ ተጋድሞ ፡ የጭንቅ ፡ ትንፋሽ ፡ ይተነፍስ ፡ ዠመር ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ አባቱና ፡ ወደ ፡ እናቱ ፡ ዐይኑን ፡ አቅንቶ ፡ አባባ ፡ እማማ ፤

አይሸታችሁም ፡ ወይ ፡ ይህ ፡ ግሩም ፡ የሆነ ፤ የሚያስደንቅ ፡ ሽታ ፤
ለካ ፡ በሱ ፡ ኖሯል ፡ የሚርቅ ፡ በሽታ ።

ነፍስን ፡ ከሥጋ ፡ ይለያል ፡ የመዐዛው ፡ ጣም ፡
እፎይ ፡ እፎይ ፡ ዐረፍኩኝ ፤ ወደቀ ፡ ከላዬ ፡ ያ ፡ ከባድ ፡ ሸክም ፤
ብሎ ፡ ከልጋው ፡ ላይ ፡ ተጋደመና ፡ የሞት ፡ እንቅልፍ ፡ አንቀላፋ ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሥ ፡ አባቱና ፡ ንግሥት ፡ እናቱ ፡ ልጄ ፡ ልጄ ፡
እያሉ ፡ ይጮኹ ፡ ዠመር ።

ከውጭ ፡ የልዑል ፡ ያዕቆብን ፡ ሕመም ፡ የሚጠባበቁ ፡ መኳንንትና ፡ መሳፍንት ፡ ወይዛዝር ፤ በሩን ፡ ከፍተው ፡ ገቡና ፡ ንጉሡንና ፡ ንግሥቲቱን ፡ በግድ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ክፍል ፡ ወሰዷቸውና ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብን ፡ አጥበው ፡ ገንዘው ፡ የያድባራቱ ፡ ካህናት ፡ ተጠርተው ፡

የፍታቱን ፡ ሥርዐት ፡ ከጨረሱ ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ሕገ ፡ መንግሥቱ ፡ ደንብ ፡ በመንግሥት ፡ ሠረገላ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ወስደው ፡ ካባቶቹ ፡ ቦታ ፡ አሳረፉት ።

ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ከድኾች ፡ ወንድሞቹ ፡ ጋራ ፡ ሕዝባዊ ፡ በመሆኑ ፡ በስጦታም ፡ በርዳታም ፡ ስለማይለያቸው ፡ በጐንደር ፡ ያሉ ፡ ድኾች ፡ ተሰብስበው ፡ ልጃችን ፡ ረዳታችን ፡ እኛን ፡ ለማን ፡ ጥለኽ ፡ ሄድክ ፡ እያሉ ፡ የመረረ ፡ ልቅሶ ፡ ያለቅሱ ፡ ነበር ፡

መኳንንቱና ፡ መሳፍንቱም ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ በነሱ ፡ ጥቅም ፡ ውስጥ ፡ ባለመግባቱና ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ እሽቅድድም ፡ ውስጥ ፡ ተወዳዳሪ ፡ ባለመሆኑ ፡ ምክንያት ፡ ያለቂም ፡ ወዳጃቸው ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በጣም ፡ አዘኑ ። የጐንደር ፡ ከተማ ፡ በመላው ፡ በኀዘን ፡ ጠቈረ ፡ ያ ፡ የዘፈንና ፡ የደስታ ፡ ከተማ ፡ በኀዘን ፡ ጥቍር ፡ ልብስ ፡ ተሸፈነ ።

ዐፄ ፡ ዳዊትና ፡ ንግሥቲቱም ፡ ከልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ዕረፍት ፡ ወዲህ ፡ ዘፈንና ፡ ደስታን ፡ እንደ ፡ ልጃቸው ፡ ገዳይ ፡ ከደመኛ ፡ ስለ ፡ ቈጠሩት ፡ ፈጽሞ ፡ በጐንደር ፡ ከተማ ፡ ተከለከለ ።

ነገር ፡ ግን ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ በልጃቸው ፡ ኀዘን ፡ ምክንያት ፡ ዘፈንን ፡ ቢተውም ፡ በታሪክ ፡ ውስጥ ፡ ዘፋኙ ፡ ዳዊት ፡ መባል ፡ አልቀረም ።

ዐፄ ፡ ዳዊትም ፡ ከልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ ዕረፍት ፡ ወዲህ ፡ ምንም ፡ ደስ ፡ የሚል ፡ ኑሮና ፡ ጤና ፡ አላገኘም ።

ይልቁንም ፡ ልዑል ፡ ያዕቆብ ፡ እንደ ፡ ልጅ ፡ ሳይፈራ ፡ እንደ ፡ ታላቅ ፡ ወንድም ፡ ከሰውና ፡ ከእግዚአብሔር ፡ የሚያጣላውን ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ በድፍረት ፡ ይመክረው ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ሌትም ፡ ቀንም ፡ ልጄ ፡ መካሬ ፡ እያለ ፡ ሲያለቅስ ፡ በኀዘን ፡ ምክንያት ፡ ታሞ ፡ ዐረፈ ።



# አሳብና ፡ ሰው ።

## ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ

ባ፲፱፻፵፫ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡

ከራስ ፡ ቢ. ፡ መኰንን ፡ እንዳልካቸው ፡ ተጻፈ ።

ታርሞ ፡ አራተኛ ፡ ታተመ ።

## መ ቅ ድ ም ።

ይህ ፡ አሳብና ፡ ሰው ፡ የተባለው ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ ሰው ፡ ካሳቡ ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ እንደሚታገልና ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ አሳብ ፡ ከራሱ ፡ ጉልበት ፡ ይልቅ ፡ ያንድ ፡ ፈረስ ፡ ጉልበት ፡ ያኽል ፡ እንደ ሚበረታ ፡ ጐትቶ ፡ በግድ ፡ ይዘትም ፡ እንደሚሄድ ፡ ገልጾ ፡ ያሰየናል ።

ይህነን ፡ ካቅማችን ፡ በላይ ፡ የሆነውን ፡ አሳብ ፡ መድኀኒታ ችን ፡ በነፉስና ፡ በጐርፍ ፡ መስሎታል ፤ ብርቱ ፡ ኀሊናንም ፡ በጭ ንጫ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተመሠረተ ፡ ቤት ፤ ደካማ ፡ ሰነፍ ፡ ኀሊናንም ፡ በሸዋ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተመሠረተ ፡ ቤት ፡ መሆናቸውን ፡ አስታውቆ ናል ። ቅዱስ ፡ ጳውሎስም ፡ በሰልፍ ፡ ተጋጥመው ፡ እንደሚዋጉ ፡ አርበኞች ፡ መስሎ ፡ በልቡናዬ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሕግ ፡ ማለፊያ ፡ ነው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ በሰውነቴ ፡ ውስጥ ፡ ሌላ ፡ የኀ ጢአት ፡ ሕግ ፡ አገኘሁ ፡ በልቡናዬ ፡ ውስጥ ፡ ካለ ፡ ከእግዚአብ ሔር ፡ ሕግ ፡ ጋራ ፡ ተሳልፈው ፡ ተዋጉ ። በሰውነቴ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ የኀጢአት ፡ ሕግ ፡ ድል ፡ ነሥቶ ፡ ወስዶ ፡ ማረከኝ ፤ እኔ ፡ ወራዳ ፡ ሰው ፡ ከዚህ ፡ ከሞት ፡ ሰውነቴ ፡ ፈቃድ ፡ ማን ፡ በዳነኝ ፡ ይላል ። ደግሞ ፡ ነቢዩ ፡ ዳዊት ፡ በማዕበልና ፡ በሞገድ ፡ መስሎ ፡ አቤቱ ፡ ማዕበልኽና ፡ ሞገድኽ ፡ በላዬ ፡ አለፈ ፡ ይላል ። እኔም ፡ ባንድ ፡ ሰውና ፡ ባንድ ፡ ፈረስ ፡ ጉልበት ፡ ብመስለው ፡ ያው ፡ ዞሮ ፡ ዞሮ ፡ ለሰው ፡ ልጆች ፡ ካቅማቸው ፡ በላይ ፡ የሆነ ፡ ብርቱ ፡ ያሳብ ፡ ጦርነ ትና ፡ ጽኑ ፡ የፈቃድ ፡ ውጊያ ፡ እንዳለባቸው ፡ ገልጾ ፡ ያሳያል ።

ሰው ፡ ዘወትር ፡ በኀሊና ፡ ጦርነት ፡ ውስጥ ፡ ነው ፤ ውጊያውም ፡ ከሥጋና ፡ ከደም ፡ ጋራ ፡ መሆኑ ፡ የታወቀ ፡ ነው ።

ለምሳሌ ፤ አንድ ፡ ሰው ፡ ለራሱና ፡ ለባልንጀራው ፡ በጎች ፡ ገዝቶ ፡ ከገበያ ፡ ሲመለስ ፡ ለራሱ ፡ የገዛው ፡ በግ ፡ ከባልንጀራው ፡ በግ ፡ ያነሰ ፡ የከሳ ፡ ስለ ፡ ሆነበት ፡ የኀሊና ፡ ጦርነቶች ፡ ተሳልፈው ፡ ይዋጉበት ፡ ዠመር ።

ክፉው ፡ አሳብ ፤ ለጓደኛዬ ፡ የገዛሁት ፡ በግ ፡ ትልቅ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፤ የሱን ፡ ወስጄ ፡ የኔን ፡ እለውጠዋለሁ ፡ የኔን ፡ በግ ፡ በፊት ፡ መግዛቴን ፡ የባልንጀራዬን ፡ በግ ፡ በኋላ ፡ መግዛቴን ፡ ከኔ ፡ በቀር ፡ ማንም ፡ ያየ ፡ የለም ፡ ብሎ ፡ አሰበ ።

የውነተኛው ፡ ጎሊና ፤ አይሆንም ፡ አትለውጥ ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ ባያይኽ ፡ እግዚአብሔር ፡ አይቶኻል ፤ የወንድምኽን ፡ ዕድል መስረቅ ፡ ትልቅ ፡ ኃጢአት ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።

ክፉው ፡ አሳብ ፤ ይህ ፡ ዋና ፡ ስንፍና ፡ ነው ፡ ሰው ፡ ዕድል ፡ ብሎ ፡ ስም ፡ ያወጣለት ፡ ብልጠትን ፡ ነው ፤ በብልጠታችን ፡ ዕድልን ፡ ልናገኝ ፡ እንችላለን ፡ ስለ ፡ ምንድነው ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ አጋጣሚ ፡ ሲገኝ ፡ ስርቆት ፡ ነው ፡ እያልን ፡ የማንጠቀምበት ፡ ብሎ ፡ መለሰ ።

የውነተኛው ፡ ጎሊና ፤ ተው ፡ እባክኽ ፡ በብልጠት ፡ ዕድል ፡ የሚገኝ ፡ ከሆነ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሥራ ፡ ፈታ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ በብልጠት ፡ የተገኙ ፡ ዕድሎች ፡ ቶሎ ፡ ብለው ፡ እንደሚጠፉ ፤ አታውቅምን ፤ ነቢዩ ፡ ዳዊትም ፡ ኀጢአተኛ ፡ እንደ ፡ ደጋ ፡ ዛፍ ፡ ገኖ ፡ ትልቅ ፡ ሆኖ ፡ አየሁት ፤ ብመለስ ፡ ግን ፡ አጣሁት ፡ ቦታውንም ፡ ብፈልግ ፡ አላገኘሁትም ፡ ብሏል ፤ በሐሰት ፡ ብዙ ፡ ከማግኘት ፡ በውነት ፡ ጥቂት ፡ ማግኘት ፡ ይሻላል ፤ እየተባባሉ ፡ ሁለት ፡ የሐሳብ ፡ ሰልፈኞች ፡ ሲዋጉበት ።

አንድ ፡ የሁለቱም ፡ ሰዎች ፡ ጎረቤት ፡ የሆነ ፡ ሰውዩ ፡ እሱም ፡ ሚስቱም ፡ ልጆቹም ፡ ሲሄዱ ፡ ከመንገድ ፡ ተገናኙና ፡ ጎረቤቶቼ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ውላችኋል ፡ ካለ ፡ በኋላ ፡ በጎቼን ፡ ብቅ ፡ አድርጎ ፡ ይኸውላችሁ ፡ ይኸነን ፡ ትልቁን ፡ በግ ፡ ለጓደኛዩ ፡ ገዛሁለት ፡ ይህችን ፡ ትንሿን ፡ ለኔ ፡ ገዛሁ ፡ እማኞቼ ፡ ናችሁ ፡ ብሸፍጥም ፡ እንድትመሰክሩብኝ ፡ ብሎ ፡ አስታወቃቸውና ፡ ወደ ፡ ፊቱ ፡ ሄደ ።

እነዚያም ፡ ሰዎች ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ ስለ ፡ ሰሙ ፡ ገርሟቸው ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ተጓዙ ፤ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ክፉው ፡ ጎሊና ፡ እማኝ ፡ ከተቈጠረበት ፡ ወዲያ ፡ ጥሎት ፡ ሸሸ ። ወዲያው ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ እንደ ፡ ደረሰ ፡ ለጓደኛው ፡ የገዛለትን ፡ በግ ፡ ይዞ ፡ ሄደ ፤ የተወደድኽ ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ እንሆ ፡ ይህነን ፡ በግ ፡ ከጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ተዋግቼ ፡ አመጣሁልኽ ፡ ብሎ ፡ በገንዘቡ ፡ የገዛለትን ፡ ትልቁን ፡ በግ ፡ ሰጠው ፡ ይባላል ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ እኛም ፡ የጎሊና ፡ ጦሮች ፡ ተሰልፈው ፡ በተዋጉብን ፡ ጊዜ ፡ ሰው ፡ አያየኝም ፡ ብሎ ፡ በክፉ ፡ ፈቃድ ፡ እጅ ፡ ተማርከ ፤ ከመሄድ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እማኝ ፡ አድርጎ ፡ ክፉ ፡ ፈቃድን ፡ ማሸነፍ ፡ ዋና ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ መሆኑን ፡ እንዳንረሳ ፡ ያሳስበናል ፤ ሰው ፡ ባያይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያያል ።

ከዕለታት ፤ አንድ ፡ ቀን ፡ የእሥራኤል ንጉሥ ፡ ዳዊት ፤ በሰገ ነት ፡ ሲመላለስ ፡ በመስኰቱ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ የኦርዮንን ፡ ሚስት ፡ ካታክልት ፡ ውስጥ ፡ ገላዋን ፡ ስትታጠብ ፡ አይቶ ፡ በውበቷና ፡ በደም ፡ ግባቷ ፡ ይልቁንም ፡ በተፈጥሮዋ ፡ ቅርጽ ፡ ሾጤነት ፡ ምክን ያት ፡ በፍቅር ፡ ፍላጻ ፡ ተወጋ ።

አሳቡን ፡ ለመግታት ፡ እሷን ፤ ላለማየት ፡ ቢሞክር ፤ ፊቱንም ፡ ቢያዞር ፡ እንኳ ፡ አልሆነለትም ። ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በውበቷ ፡ ምክ ንያት ፡ የሳቡ ፡ ጌታ ፡ ለመሆን ፡ አልቻለም ፤ ስለዚህ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ፊቱን ፡ ወደ ፡ ግንቡ ፡ እየዞረ ፡ አቤቱ ፡ ዐይኔን ፡ መልስ ፡ ከንቱ ፡ ነገርን ፡ ከማየት ፤ እያለ ፡ ይጸልይ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ ወዲያው ፡ አሳቡ ፡ እየጐተተው ፡ በመስኮት ፡ ብቅ ፡ እያለ ፡ ይመለከት ነበር ።

ያንድ ፡ ፈረስ ፡ ጕልበት ፡ ካንድ ፡ ሰው ፡ ጉልበት ፡ በጣም ፡ እንደሚበረታ ፡ እንደዚሁም ፡ የንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ የፍትወቱ ፡ አሳብ በጎ ፡ ፈቃድን ፡ አሸንፎ ፡ እንደ ፡ አጥባቂ ፡ ፈረስ ፡ ልጓሙን ፡ እየጐተተ ፡ ወደ ፡ ጥፋት ፡ ጕድጓድ ፤ ይዞት ፤ ይሄድ ፡ ዠመር ።

ንጉሥ ፡ ዳዊትም ፡ ምንም ፡ ቢታገል ፡ ልጓሙን ፡ በበጎ ፤ ፈቃድ ፡ ዕዛብ ፡ ይዞ ፡ ቢጐትት ፡ እንኳ ፡ አሳብ ፡ ልጓም ፡ ነክሶ ፡ ስላጠበቀ ፡ የማይመለስ ፡ ሆነ ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ደወል ፡ ይደውላል ።
አሽከር ፡ ይገባል ።
ንጉሥ ፡ ዳዊት ፤
ና ፡ አንተ ፡ ብላቴና ፡ ከሩቅ ፡ ተመልከት ።
የማነች ፡ ያች ፡ ልጅ ፡ የምታንጸባርቅ ፡ እንደ ፡ መስተዋት ።
መልኳ ፡ የተዋበ ፡ እጅግ ፡ የምታምር ፡
ቅርጿ ፡ ደም ፡ ግባቷ ፡ ልብ ፡ የሚሰውር ፡
እንዲህ ፡ ያለች ፡ ቈንዡ ፡ ትልቅ ፡ ባለግርማ ፡
አይቼ ፡ አላውቅም ፡ ከእሥራኤል ፡ ከተማ ።
ያቻት ፡ ካታክልት ፡ ውስጥ ፡ ቆማ ፡ በስተግራ ፡
ታበራለች ፡ በጣም ፡ እንደ ፡ ንጋት ፡ ጮራ ፤
ሂድ ፡ የማን ፡ መሆኗን ፡ መርምረኽ ፡ አጣራ ።
አሽከር ፡ ወጣ ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ግን ፡ በጣም ፡ አዝኖ ፡ ተክዞ ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡
አሳብ ፡ ያስብ ፡ ነበር ።
አሽከር ፡ ተመልሶ ፡ ይገባና ፡
ግርማዊ ፡ ሆይ ፤
እንሆ ፡ እኔ ፡ ባሪያኽ ፡ ጠይቄ ፡ መጣሁ ፡
የኦሪዮን ፡ ሚስቱ ፡ መሆኗን ፡ ሰማሁ ።

የዚያን ፡ ጊዜ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በጣም ፡ ደነገጠ ፤ ምክንያቱም ባሏ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ስላገሩና ፡ ስለ ፡ ንጉሡ ፡ ክብር ፡ ሲዋጋ ይህቺን ፡ የተዋበች ፡ ሴት ፡ በማየቱና ፡ ከቅሙ ፡ በላይ ፡ የሆነ ፡ ኀይለኛ ፡ ፍቅር ፡ ስላጋጠመው ፡ ነው ፤ ይልቁንም ፡ በእሥራኤል ፡ ሕዝብ ፡ ፊት ፡ የሚያስነውርና ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ከወዳጁ ፡ የሚያጣላ ፤ ስለ ፡ ሆነ ፡ የመረረ ፡ ኀዘን ፡ ሆነበት ።

አሁንም ፡ ቢሆን ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ የተቻለውን ፡ ያኽል ፡ አሳቡን ፡ ለመግታት ፡ መድከሙ ፡ አልቀረም ፤ ራሱን ፡ ከጕልበቱ ላይ ፡ አድርጎ ፡ አዝኖ ፡ ተክዞ ፡ እንደዚህ ፡ ይል ፡ ነበር ።

ከማየት ፡ የመጣ ፡ ትልቅ ፡ ስሕተት ።
ልወድቅ ፡ ተንገደገድሁ ፡ ከጠለቀ ፡ ዐዘቅት ።
አሳቤን ፡ ለመግታት ፡ ዐቅም ፡ ስላጣሁ ፡
ስቦኝ ፡ ጥሎኝ ፡ ሄደ ፡ በመሬት ፡ ወደቅሁ ።
አሳብ ፡ ካጠበቀ ፡ ልጓም ፡ ከነከሰ ፡
ማንም ፡ አይመልሰው ፡ ደም ፡ ካልፈሰሰ ።
አሳብን ፡ የገታ ፡ በብርቱ ፡ ልጓም ፡
አርበኛ ፡ እሱ ፡ ነው ፡ በውነት ፡ የሚገርም ።

በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ አኳኋን ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በጣም ፡ ይጨነቅ ፡ ያዝን ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ በፍቅር ፡ ወይም ገንዘብ ፡ በመውደድ ፡ በሌሎችም ፡ ኃጢአቶች ፡ ሁሉ ፡ ፍላጻ ፡ ከተወጋ ፡ ወዲህ ፡ የዓለም ፡ ፍልስፍና ፡ ሁሉ ፡ ተሰብስቦ ፡ ስለ ዓለም ፡ ከንቱነት ፡ ለማስረዳት ፡ ቢቀርም ፡ ያመነበትን ፡ ኃጢአት ፡ ብርቱ ፡ መከራ ፡ ካላሳሰበው ፡ መጽሐፍና ፡ ፍልስፍና ፡ ሊያስረዳው ፡ አይችልም ።

ስለዚህ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ደወል ፡ ይደውላል ፤
አሽከር ፡ ይገባል ።
ንጉሥ ፡ ዳዊት ፤
ና ፡ አንተ ፡ ብላቴና ፡ ልንገርኽ ፡ ምሥጢር ፤
ለማንም ፡ እንዳትነግር ፡ በከንቱ ፡ እንዳትሞት ፡ እንዳትቀበር ።
ሂድና ፡ ያቺን ፡ ልጅ ፡ አስገባት ፡ ከልፍኝ ፡
ተጠንቀቅ ፡ በጣሙ ፡ ሰው ፡ እንዳይገኝ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ወደ ፡ ዕልፍኝ ፡ ገባ ፡ ከር ሷም ፡ ጋራ ፡ ተገናኘ ። ቤርሳቤሕም ፡ ከግዳጅዋ ፡ የምትነጻበት ፡ ጊዜ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ወዲያው ፡ ፀነሰች ፡ እሷም ፡ ወደ ፡ ቤቷ ፡ ተመልሳ ፡ ነበርና ፡ የመፅነሷን ፡ ወሬ ፡ ለንጉሡ ፡ ለመንገር ፡ አንድ ፡ የታመነ ፡ አሽከር ፡ ላከች ።

አሽከር ፡ ወደ ፡ ንጉሥ ፡ ይገባል ።
ግርማዊ ፡ ሆይ ፤
ከቤርሳቤሕ ፡ ዘንድ ፡ አሽከር ፡ ተልኳል ።
በቃል ፡ የሚነገር ፡ ምሥጢር ፡ ነው ፡ ይላል ፤
በፊቱም ፡ ላይ ፡ ኀዘን ፡ ይታይበታል ።
ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ አስገባው ።
መልክተኛው ፡ ይገባል ።
ንጉሥ ፡ ሆይ ፤
ወዳጅኽ ፡ ቤርሳቤሕ ፡ ወዳንተ ፡ ላከችኝ ፤
እኔ ፡ እንኳን ፡ ብፈራ ፡ አደፋፈረችኝ ።
መልክቷም ፡ ይኸ ፡ ነው ፡ የሚያስጨንቀኝ ፡
መፅነሷን ፡ ለመንገር ፡ ስለ ፡ ላከችኝ ።
አርበኛኽ ፡ ሲታገል ፡ ከጠላት ፡ ግንባር ።
ሚስቱ ፡ ካንተ ፡ መፅነስ ፡ እጅግ ፡ የሚመር ።
አስብበት ፡ በጣም ፡ ሕዝብህ ፡ እንዳይሰማ ።
እጅግ ፡ ያስነውራል ፡ በእስራኤል ፡ ከተማ ።

ንጉሥ ፡ ዳዊትም ፡ በመፅነሷ ፡ ምክንያት ፡ በጣም ፡ አዘነ ፡ ይልቁንም ፡ ካንድ ፡ አሽከር ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ዘለፋና ፡ ምክር ፡ በመስማቱ ፡ እንግዴህ ፡ በእግዚአብሔርና ፡ በእስራኤል ፡ ሕዝብ ፡

ፊት ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ፍርድ ፡ ሊደርስብኝ ፡ ይሆን ፡ በማ ለት ፡ ነው ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ እንዳይታወቅ ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡ ይሻላል ፡ በማለት ፡ ብርቱ ፡ ሐሳብ ፡ ወደቀበት ። ነገር ፡ ግን ፡ በምክንያት ፡ ለመሸፈን ፡ ምን ፡ ይሻላል ፡ እያለ ፡ ሲያወጣ ፡ ሲያ ወርድ ፡ አንድ ፡ አሳብ ፡ ተገለጠለት ፤ አሳቡም ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ኦርዮንን ፡ ከጦር ፡ ሜዳ ፡ አስጠርቼ ፡ ከሚስቱ ፡ ጋራ ፡ እንዲያ ድር ፡ አደርገዋለሁ ። በዚህ ፡ እኺኻን ፡ ፅንሱን ፡ ለማሳሳት ፡ የሱ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ለማሰኘት ፡ ይቻላል ፤ በማለት ፡ ከቈረጠ ፡ በኋላ ፡

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡
መሸፈኛ ፡ እሚሆን ፡ ለዚህ ፡ ኀጢአት ፡
አሰብኩ ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ሊሆን ፡ ምክንያት ።
ኦርዮንን ፡ ጠርቶ ፡ ማሳደር ፡ ከቤቱ ፡
ወዲያው ፡ እንዲጫወት ፡ ከሚወዳት ፡ ሚስቱ ።
ፅንሱም ፡ እንዲሳሳት ፡ ሕዝቡም ፡ እንዳይሰማ ፡
ከዚህ ፡ የበለጠ ፡ ምንም ፡ አይገኝም ፡ ላሰብኩት ፡ ዐላማ ።
ኦርዮን ፡ ወዳጄም ፡ አይጠረጥረኝ ፡
ለኔም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ሆኖ ፡ ልጄ ፡ ቢያድግልኝ ።
የእንጀራ ፡ አባት ፡ ሞግዚት ፡ ከሁሉም ፡ ይሻላል ።
ልጄም ፡ ከናቱ ፡ ጋር ፡ በድሎት ፡ ይኖራል ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በቶሎ ፡ ለጦር ፡ አለቃው ፡ ለኢዮአብ ፡ ወረቀት ፡ ለመላክ ፡ ወደ ፡ ጠረጴዛው ፡ ተጠግቶ ፡ ይጽፍ ፡ ዠመር ።

ይድረስ ፡ ከኢዮአብ ፡ ከታመንክ ፡ ወዳጄ ።
እኔው ፡ ራሴ ፡ ነኝ ፡ የጻፍኩልኽ ፡ በጄ ።
የጦር ፡ አለቆቹስ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ናቸው ።
የምሰማው ፡ ወሬ ፡ የሚገርም ፡ ነው ።
ኦርዮንን ፡ ላክልኝ ፡ እንድጠይቀው ።
እውነቱን ፡ የማገኝ ፡ ከሱ ፡ ብቻ ፡ ነው ።
ይመለስልኻል ፡ በፍጥነት ፡ ወዳንተ ፤
ዐውቀዋለሁ ፡ እኔም ፡ የታመነ ፡ አገልጋይ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ላንተ ።

ብሎ ፡ ከጻፈ ፡ በኋላ ፡ ደብዳቤውን ፡ በማኅደር ፡ አግብቶ ፡ በጣቱ ፡ ማኅተም ፡ አትሞ ፡

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ደወል ፡ ይደውላል ፡
አሽከር ፡ ይገባል ፤
ንጉሥ ፡ ዳዊት ፤
በፍጥነት ፡ ጥራልኝ ፡ አንድ ፡ ፈረሰኛ ፤
በፍጹም ፡ ኀሊናው ፡ የታመነ ፡ ለኛ ።
አሽከር ፡ ይወጣል ፤
አሽከር ፡ ተመልሶ ፡ ይገባል ።
ግርማዊ ፡ ሆይ ፡ የሚላከው ፡ ባሪያኽ ፡ መጥቷል ።
ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ አስገባው ።
መልክተኛው ፡ ይገባል ።
ይህነን ፡ ደብዳቤ ፡ ስጠው ፡ ለኢዮአብ ፤
አስቸኳይ ፡ መሆኑን ፡ በውል ፡ አስገንዝብ ።
ለኦርዮንም ፡ አስታውቅ ፡ እንዳይውል ፡ እንዳያድር ፡ እንዲገሠግሥ ፡
ወደ ፡ ጓደኞቹ ፡ ቶሎ ፡ እንዲመለስ ።

ኢዮአብም ፡ የንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ደብዳቤ ፡ እንደ ፡ ደረሰው ፡ ለኦርዮን ፡ ትእዛዙን ፡ አስታውቆት ፡ በግሥጋሤ ፡ ባራት ፡ ቀን ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ከዳዊት ፡ ከተማ ፡ ደረሰ ።

አሽከር ፡ ይገባል ።
ግርማዊ ፡ ሆይ ፤
እንሆ ፡ ኦርዮን ፡ መጣ ፡ እየጋለበ ፡ በሚያስፈራ ፡ ግርማ ፤
ቸኵያለሁ ፡ ይላል ፡ ለመድረስ ፡ በቶሎ ፡ ላቀደው ፡ ዓላማ ።
ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ጥራው ፤

ኦርዮን ፡ ጋሻና ፡ ጦሩን ፡ እንደ ፡ ያዘ ፡ ገብቶ ፡ በጕልበቱ ፡ ተንበርክኮ ፡ እጅ ፡ ይነሣል ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡
ወዳጄ ፡ ኦርዮን ፡ እንደ ፡ ምንድን ፡ ነኽ ።
ላስጠራኽ ፡ ፈቀድኩኝ ፡ ወሬ ፡ ልጠይቅኽ ፡
ኢዮአብ ፡ እንዴት ፡ ነው ፡ የጦር ፡ ጓደኛኽ ።
ያርበኞቹ ፡ ምግባር ፡ ጠንክሯል ፡ ማለትን ፡ እየሰማሁኝ ፡
ባንተ ፡ በወዳጄ ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ አለኝ ።
የምታጽናናቸው ፡ አንተ ፡ ነኽ ፡ የሚሉ ፡ እየሰማሁኝ ።
ወዳጄ ፡ ኦርዮን ፡ እንግዴህ ፡ ሂድና ፡ ከቤትኽ ፡ እደር ።
አጽናናት ፡ ሚስትኽን ፡ አሳያት ፡ ፍቅር ።
ኦርዮን ፤ ንጉሥ ፡ ሆይ ፡

የእስራኤል ፡ ታቦት ፡ በድንኳን ፡ ተቀምጣ ፡ እያለቀሰች ፡
ይሁዳ ፡ በምሽግ ፡ ሰፈሩን ፡ አድርጎ ፡ ለጦር ፡ ሲመቻች ፤
ኢዮአብ ፡ ጌታዬ ፡ ከጠላት ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ቀርቦ ፡ ሲፏከር ፤
እኔ ፡ ከሚስቴ ፡ ጋራ ፡ ከቤቴ ፡ ላድር ።
አይሆንም ፡ የሕይወትኽን ፡ የሰውነትህን ፡ በረከት ፡
ቤቴን ፡ አላየውም ፡ የሚስቴንም ፡ ውበት ።
አገር ፡ ስቃለቅስ ፡ ከሚስቴ ፡ ማደር ፤
ሰው ፡ ያለመሆን ፡ ነው ፡ ያለመፈጠር ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፤
ወዳጄ ፡ ኦርዮን ፡
እባክኽ ፡ ልንገርኽ ፡ ዋና ፡ ቁም ፡ ነገር ፤
ሴት ፡ ከባሏ ፡ በቀር ፡ የላትም ፡ አገር ፤
ተው ፡ አታሳዝናት ፡ ሂድ ፡ ተነጋገር ፤
ከሚስት ፡ ጋር ፡ ማደር ፡ አይሆንም ፡ ነውር ።

ኦርዮን ፤
ንጉሥ ፡ ሆይ ፡
አይሆንም ፡ አልገባም ፡ ከቤቴ ፡ ጠፈር ።
ሚስቴንም ፡ አላያት ፡ ልጆቼን ፡ ጭምር ፤
ላገሬ ፡ እሞታለሁ ፡ ያለጥርጥር ።

ንጉሥ ፡ ሆይ ፡
ፍቀድልኝ ፡ ልሂድ ፡ ከጦሩ ፡ ግንባር ፤
ቤቴን ፡ አላየውም ፡ በውነቱ ፡ በምር ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ በቈራጥነት ፡ መንፈስ ፡ ኦርዮን ፡ ሲናገር ፡ በመስማቱ ፡ በጣም ፡ አዝኖ ፡
ውጣና ፡ ተቀመጥ ፡ ከማረፊያው ፡ ቤት ፤
እስትጽፍ ፡ ለኢዮአብ ፡ የምሥጢር ፡ መልክት ።

ኦርዮን ፡ ወጥቶ ፡ ካዳራሽ ፡ ውስጥ ፡ ይቀመጣል ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በማዕበልና ፡ በሞገድ ፡ በጣም ፡ እንደምትሰ ጥምና ፡ እንደምትወጣ ፡ እንደምትንገላታ ፡ አንዳንዲት ፡ ትንሽ ፡ ጀልባ ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊትም ፡ ባሳብ ፡ ማዕበልና ፡ ሞገድ ፡ ሰጥሞ ፡ ያዝን ፡ ይተክዝ ፡ ነበር ።

ይልቁንምም ፡ ያርበኛ ፡ አሽከሩን ፡ የኦርዮንን ፡ ሚስት ፡ ቈርጦ፡ ለመተው ፡ ቢያስብ ፡ እንኳ ፡ የማርገዟ ፡ ነገር ፡ የማይወጣ ፡ ዐቀበት ፡ ሆኖበት ፡ ተጨነቀ ፤ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ፅንሱን ፡ ለማሳሳት ፡ ያሰበውን፡ ዘዴ ፡ ኦርዮን ፡ የባለጌ ፡ ሃይማኖት ፡ ከኹማት ፡ ይጠናል ፡ እንደተ ባለው ፡ ታቦተ ፡ ጽዮን ፡ በድንኳን ፡ የጦር ፡ ጓደኞቹ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ሆነው ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ከምስቴ አልገናኝም ፤ ከቤ ቴም ፡ አልገባም ፡ በማለት ፡ ጠነከረ ፤ ስለዚህ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በጨለማ ፡ አሳብ ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ የሚወጣበትን ፡ መንገድ ፡ በዳ በሳ ፡ ይፈልግ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ዘወትር ፡ በቀ ቢጸ ፡ ተስፋ ፡ ጨለማ ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ የሚያስበው ፡ አሳብ ፡ ወደ፡ ባሰ ፡ ጨለማ ፡ ኀጢአት ፡ ውስጥ ፡ ስለሚጥል ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በእ ስራኤል ፡ ሕዝብ ፡ እጅ ፡ ከመውደቅ ፡ በእግዚአብሔር ፡ እጅ ፡ መውደቅ ፡ ይሻለኛል ፡ በማለት ፡ በባሰ ፡ ኀጢአት ፡ ለመውደቅ ፡ አሰበ ፡ ቈረጠ ።

አሳቡም ፡ ይህ ፡ ነው ።

ወደ ፡ ታመነ ፤ አገልጋዬ ፡ ወደ ፡ ኢዮአብ ፡ በምሥጢር ፡ ደብ ዳቤ ፡ ጽፌ ፡ ኦርዮንን ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ አጋልጦ ፡ እንዲያስገ ድለው ፡ አደርጋለሁ ፤ ይህ ፡ ሲሆን ፡ የሞተ ፡ በጠላት ፡ እጅ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ማንም ፡ አያውቀው ፡ ኀጢአትም ፡ አይሆንብኝም ፡ እሷም ፡ የሙት ፡ ሚስት ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ ባገባት ፡ ነውር ፡ አይሆንብኝም ፡ በማ ለት ፡ ቈረጠ ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፤
እኔ ፡ ያቀድኹት ፡ ዘዴ ፡ ሳይፈጸም ፡ ቀረ ፤
ካርበኛዬ ፡ ጋራ ፡ ጥላችን ፡ መረረ ።
ይህ ፡ ነገር ፡ ተገልጦ ፤ ሕዝብ ፡ ከሚያቀል ፡
በምሥጢር ፡ በስውር ፡ ይሻላል ፡ መግደል ።
ኅሊና ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እውነተኛ ፡ ዳኛ ፡ ልብን ፡ የሚያስቸግር።
ሁልግዜ ፡ በጸጸት ፡ ዐጥንት ፡ የሚሰብር ።
ምን ፡ ይደረግ ፡ እንግዴህ ፡ በጣም ፡ ያሳዝናል ፤
ሃይማኖት ፡ ዘወትር ፡ እንዲህ ፡ ያስገድላል ።
ወዲያው ፡ ወደ ፡ ጽፈት ፡ ገበታ ፡ ተጠግቶ ፡ ይጽፍ ፡ ዠመር ።
ይድረስ ፡ ከኢዮአብ ፡ ከታመንክ ፡ ወዳጄ ፤

እኔው ፡ እራሴ ፡ ነኝ ፡ የጻፍኩልኽ ፡ በጄ ።
አርዮንን ፡ ጽኑ ፡ ሰልፍ ፡ ወዳለበት ፡ ግንባር ፡ በቶሎ ፡ አቁሙት ፤
ሽሹ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ እሱ ፡ ብቻ ፡ ይሙት ።

ወዳጄ ፡ ሆይ ።

እኔ ፡ እነግርኻለሁ ፡ ይህነን ፡ ምሥጢር ፤
በድል ፡ ስትመለስ ፡ ስትገባ ፡ ካገር ፡
እንዲህ ፡ ያስጨነቀኝ ፡ ከንቱ ፡ እንዳይመስልህ ፤
እኔው ፡ ሳሚሙትህ ፡ ትረዳዋለኽ ።
በቅጽበት ፡ አድርገው ፡ በቶሎ ፡ በፍጥነት ፤
አንድ ፡ አሽከር ፡ ላክብኝ ፡ ጽፈኽ ፡ በወረቀት ።
ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ይደውላል ፣
አሽከር ፡ ይገባል ።
አርዮንን ፡ ጥራው ፤
አርዮን ፡ ይገባል ።
ንጉሥ ፡ ዳዊት ፤
አርዮን ፡ ሆይ ፡
ሂድ ፡ እንግዴህ ፡ ቶሎ ፡ ደብዳቤ ፡ ይዘኽ ፤
ስጠው ፡ ለኢዮአብ ፡ ለጦር ፡ ጓደኛኽ ።
ተዋጋ ፡ በብርቱ ፡ እንዳይወድቅ ፡ ክብርኽ ፤
ስለ ፡ ጽኑ ፡ አሳብኽ ፡ አመሰግንኩኽ ፤
ቶሎ ፡ እንድትልክብኝ ፡ የጦሩን ፡ ሁናቴ ፤
ባንተ ፡ ላይ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ፍጹሙ ፡ እምነቴ ።

አርዮን ፡ ደብዳቤውን ፡ ከንጉሡ ፡ ተቀብሎ ፡ ጋሻና ፡ ጦሩን ፡ እንደ ፡ ያዘ ፡ በጒልበቱ ፡ ተንበርክኮ ፤ የንጉሡን ፡ ጫማ ፡ ከሳመ ፡ በኋላ ፡ ወጥቶ ፡ ሄደ ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አርዮን ፡ በግሥጋሤ ፡ ሌሊትና ፡ ቀን ፡ ስለ ፡ ሄደ ፡ በሦስት ፡ ቀን ፡ ከጦሩ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ከአርበኞች ፡ ወንድሞቹ ፡ ጋራ ፡ ተገናኘ ። ኢዮአብም ፡ የጦር ፡ ጓደኛውን ፡ አርዮንን ፡ በማየቱ ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ አንገቱን ፡ አቅፎ ፡ ሳመው ።

ወዲያው ፡ አርዮን ፡
ጌታዬ ፡ ኢዮአብ ፡ እንሆ ፡ ወረቀት ፡
የንጉሡ ፡ ትእዛዝ ፡ የሚፈጸምበት ።
ንጉሡ ፡ ሲያምነን ፡ እኛን ፡ ባሮቹን ፤
መሞት ፡ ይገባናል ፡ በፍጥነት ፡ አሁን ።

የኛ ፡ ደም ፡ አገሯን ፡ ያስከብራታል ፤
አርበኛም ፡ አይሞትም ፡ ታሪክ ፡ ያስነሣዋል ፡
ኢዮአብም ፡ የንጉሡን ፡ ደብዳቢ ፡ በትሕትና ፡ ተቀብሎ ፡ ካነበበው ፡ በኋላ ፡ በጣም ፡ አዘነ ፤ ኀዘኑንም ፡ ለመሰወር ፡ የማይቻለው ሆነ ። መራራ ፡ የሆነ ፡ የኀዘን ፡ ሐሞት ፡ በድንገት ፡ ከራሱ ፡ ላይ ፡ ስለመጣበት ፡ ፊቱ ፡ ጠቈረ ።

አርዮን ፡ የንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ደብዳቤ ፡ በቶሎ ፡ በጠላት ፡ ላይ ፡ ውደቁበት ፡ ቀን ፡ አትስጡት ፡ የሚል ፡ ስለ ፡ መሰለው ።

ኢዮአብ ፡ ጊታዬ ፡ ስለምን ፡ አዘንኽ ፡ ፊትኽም ፡ ጠቈረ ፤
አታውቅም ፡ ወይ ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ለሞት ፡ እንደ ፡ ተፈጠረ
ምንም ፡ ሞት ፡ ቢከፋ ፡ መልኩ ፡ ባያምር ፡
እንሆ ፡ ቆንጆ ፡ ሞት ፡ ተገልጦ ፡ ይታያል ፡ ከጠላት ፡ ግንባር ።
ኢዮአብም ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ ለብቻው ፡ ካለቀሰ ፡ በኋላ ፡ የምሥጢሩን ፡ ደብዳቤ ፡ ቀዳዶ ፡ ጥሎ ፡ ወደ ፡ ጦሩ ፡ ተመለሰና ፡
ወንድሜ ፡ አርዮን ፡ እንሂድ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ በጣም ፡ እንገሥግሥ ፤
ቀማሹ ፡ አንተ ፡ ነኽ ፡ ለዚህ ፡ ለድግስ ።
እንከተላለን ፡ አንቀርም ፡ እኛም ፡
የንጉሥ ፡ ቃል ፡ አንድ ፡ ነው ፡ አያጥር ፡ እይረዝም ፡
ብሎ ፡ የዳዊት ፡ አርበኞች ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ እንሂድ ፡ አንፍራ ፡ እያለ ፡ ካርበኞቹ ፡ ጋራ ፡ እጅ ፡ ለጅ ፡ ተያይዘው ፡ አርዮንን ፡ ወደ ፡ ፊት አስቀድመው ፡ በጠላት ፡ ጦር ፡ ላይ ፡ በኀይል ፡ ወደቁበት ፡ እጅ ፡ በጅ ፡ የጐራዴ ፡ ምክታ ፡ ዠምረው ፡ ጐራዴ ፡ ለጐራዴ ፡ ሲፋጭ ፡ አርዮንን ፡ አጋፍጠው ፡ ጥለውት ፡ ሸሹ ። እሱም ፡ ብቻውን ፡ ከጠላት ፡ ጋራ ፡ ከተከራከረ ፡ በኋላ ፡ በሰይፍ ፡ ከደረቱ ፡ ላይ ፡ በብርቱ ፡ ተወግቶ ወደቀ ። አርዮን ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ቢያይ ፡ አንድም ፡ የጦር ፡ ጓደኛ ባጠገቡ ፡ አጣ ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ በብስጭት ፡ እጁን ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ዘርግቶ ፡ እንደዚህ ፡ እያለ ፡ ይጮኽ ፡ ነበር ።

የዳዊት ፡ አርበኞች ፡ ወዴት ፡ ሸሻችሁ ፤
አገር ፡ ስታለቅስ ፡ እየሰማችሁ ።
ያገርን ፡ ኵራት ፡ ካፈር ፡ ላይ ጥላችሁ ፤
አትወቅሣችሁም ፡ ወይ ፡ መሬት ፡ እናታችሁ ።

ንጉሡ ፡ ሲሰማ ፡ እንዴት ፡ ይገርመው ፤
በኢዮአብ ፡ ሽሽት ፡ ባልተለመደው ።
ሚስቴ ፡ ደኅና ሰንብች ፡ ሳልልሽ ፡ ሞትኩኝ ፤
አንቺስ ፡ ሰው ፡ አታጭም ፡ እኔ ፡ ዐፈር ፡ ሆንኩኝ ።



የሚሞት ፡ ሰው ፡ ሲሞት ፡ ታሪኩ ፡ አይሞትም ፤
ባገሩ ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ይጻፋል ፡ በደም ፤

የሚሞት ፡ ሰው ፡ ሲሞት ፡ ታሪኩ ፡ አይሞትም ፤
ባገሩ ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ይጻፋል ፡ በደም ።

ብሎ ፡ በጦሩ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ወደቀና ፡ በጣቱ ፡ ደሙን ፡ እያጠቀሰ ፡ በሙ
ሬቱ ፡ ላይ ፡ ይጽፍ ፡ ነበር ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ደሙን ፡ በጁ ፡ ዘግኖ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ ረጨና ፡ በግንባሩ ፡ ወደቀ ፤ ሞተም ። ኢዮአብም ፡ ከደን ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ በት እዛዝ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ በመሆኑ ፡ የመረረ ፡ ልቅሶ ፡ እያለቀሰ ፡ ይጠባበ ቀው ፡ ነበርና ፡ ዝሎ ፡ ከመሬት ፡ ወድቆ ፡ ነፍሱን ፡ ወደ ፡ እግዚአብ ሔር ፡ ሲሰጥ ፡ ካርበኞች ፡ ጓደኞቹ ፡ ጋራ ፡ መጥቶ ፡ ሬሳውን ፡ አንሥ ተው ፡ ቀበሩትና ፡ ኢዮአብ ፡ ብቻውን ፡ ከደን ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፡ በጒ ልበቱ ፡ ላይ ፡ ብራናውን ፡ አድርጎ ፡ የኦርዮንን ፡ ሞት ፡ ለንጒሥ ፡ ዳዊት ፡ ጻፈለት ።

ኢዮአብ ፤

የእስራኤል ፡ ንጒሥ ፡ ግርማዊ ፡ ዳዊት ፡
አርበኛኽ ፡ ኦርዮን ፡ ሲዋጋ ፡ ከጠላት ፡ ቀድሞ ፡ ወደፊት ፡
የክብር ፡ ሞት ፡ ሞተ ፡ ላንተ ፡ ለዳዊት ።
በጣም ፡ አሳዘነኝ ፡ የሱን ፡ ቃል ፡ ስሰማ ፤
ተዉ ፡ አትመለሱ ፡ ኀፍረትን ፡ ለብሳችሁ ፡ ከእስራኤል ፡ ከተማ ፡
እንዴት ፡ ያዝንባችሁ ፡ ንጒሡ ፡ ሲሰማ ።
ንጒሥ ፡ ሆይ ፤
ከሁሉም ፡ ይልቅ ፡ የሚሳዝነኝ ፡
ሚስቴ ፡ ደኅና ፡ ሰንብች ፡ ሲላት ፡ ሰማሁኝ ።
ወዲያው ፡ ባፈሩ ፡ ላይ ፤ ይጽፍ ፡ ነበር ፡ ጣቱ ፡
ታሪክ ፡ ለማስቀረት ፡ በውድ ፡ መሬቱ ።
በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ዛለ ፡ ወደቀ ፡ ካፈር ፡
ደሙን ፡ ዘግኖ ፡ ረጨው ፡ እንዲመሰክር ።
እንዲያመለክት ፡ ጮኽ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡
የደም ፡ ድምፅ ፡ በቅጽበት ፡ ይደርሳል ፡ ከዙፋኑ ፡ ላይ ።
እንደ ፡ ምን ፡ ጽኑ ፡ ነው ፡ የንጒሥ ፡ ትእዛዝ ፡
ሰማሁት ፡ ወዳጄን ፡ ሲጮኽ ፡ ሲናዘዝ ፡
ሆንኩኝ ፡ እንደማልችል ፡ እሱን ፡ ለማገዝ ።
ሸሸሁ ፡ በትእዛዝ ፡ ወዳጄን ፡ ጥዬው ፡
የንጒሥ ፡ ትእዛዝ ፡ እናት ፡ አያስቀብር ፡ እንደ ፡ ተባለው ።

ንጒሥ ፡ ሆይ ፤

እኔ ፡ ያንተ ፡ እጅ ፡ ሆኜ ፡ ስለ ፡ ገደልኩት ፡
ከጣትኽ ፡ ደም ፡ ሲፈስ ፡ በሩቅ ፡ አየሁት ።

እዘን ፡ አንተ ፡ በዚህ ፡ በንጹሑ ፡ ደም ፡ በሚያሳዝን ፡ ድኻ ። እጅኽን ፡ ታጠበው ፡ በንስሐ ፡ ውሃ ።

ብሎ ፡ ለንጉሥ ፡ የጻፈውን ፡ ሰሌዳ ፡ ጠቅሎ ፡ በጣቱ ፡ ቀለበት ፡ አትሞ ፤ በላዩ ፡ ላይ ፡ ምሥጢር ፡ ብሎ ፡ ጽፎ ፡ በፍጥነት ፡ የሚያደርስ ፡ አንድ ፡ ፈረሰኛ ፡ ጠርቶ ፡ ደብዳቤውን ፡ ሰጥቶት ፡ ሄደ ፡ በግሥጋሚም ፡ በሦ ስት ፡ ቀን ፡ ከእስራኤል ፡ ከተማ ፡ ደረሰ ።

አሽከር ፡ ይገባል ፤

ግርማዊ ፡ ሆይ ፤ ከኢዮአብ ፡ ዘንድ ፡ አሽከር ፡ ተልኮ ፡ መጥቷል ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ጥራው ፤

መልእክተኛው ፡ ይገባና ፡ ደብዳቤውን ፡ ይሰጣል ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ተቀብሎ ፡ ካነበበ ፡ በኋላ ፡ አንገቱን ፡ ደፍቶ ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ኀዘን ፡ አዘነ ። ነገር ፡ ግን ፡ የኦርዮንን ፡ ሚስት ፡ መጀ መሪያ ፡ የተዳፈረ ፡ ጊዜ ፡ ያዘነውን ፡ ያኽል ፡ አላዘነም ። ስለ ፡ ምን ፡ ኀጢአት ፡ ጥቂት ፡ በጥቂት ፡ ሲለመድ ፡ ልብ ፡ ይደነዝዝና ፡ እንደ ፡ ጽድቅ ፡ ሆኖ ፡ ይቈጠራል ። በመዠመሪያ ፡ በሰው ፡ ልብ ፡ የተቃጠ ለው ፡ የኀዘን ፡ እሳት ፡ በጊዜ ፡ ማለፍ ፡ ምክንያት ፡ ይዳፈንና ፡ ይቀመ ጣል ። ንጉሥ ፡ ዳዊትም ፡ ደስታ ፡ በሽታ ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ቤርሳቤሕ ፡ የሙት ፡ ሚስት ፡ በመሆኗ ፡ እሷን ፡ ለመውደድ ፡ ነፃነት ፡ በማግኘቱ ፡ ደስ ፡ ቢለው ፡ እንኳ ፡ አርበኛውን ፡ በጅ ፡ አዙር ፡ በማስገደሉ ፡ የኀ ዘን ፡ ስሜት ፡ ነበረው ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ አርበኛው ፡ ኦርዮን ፡ ስለ ፡ ሞተ ፡ መሳፍንቱንና ፡ መኳንንቱን ፡ የጦር ፡ አለቆቹንም ፡ አስጠርቶ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ በክብር ፡ ስለ ፡ ሞተ ፡ ከፍ ፡ ያለ የክብር ፡ ኀዘን ፡ አስደረገለት ።

ወዲያው ፡ ሚስቱን ፡ አረዷትና ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ ኀዘን ፡ አዘነች ። ከጥቂት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ የእስራኤል ፡ ሕዝብ ፡ በመጥፎ ፡ እንዳይገምተውና ፡ ጕድ ፡ ድንቅ ፡ ብሎ ፡ እንዳያማው ፡ የሠራው ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ የኀጢአት ፡ መግለጫ ፡ ከተፈጸመለት ፡ በኋላ ፡ በሙሴ ፡ ሕግ ፡ ሴት ፡ ባሏ ፡ ከሞተ ፡ በኋላ ፡ ማንንም ፡ ለማግባት ፡ ነፃነት ፡ ስላ ላት ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በሕጉ ፡ መሠረት ፡ ወስዶ ፡ ከቤተ ፡ መንግ ሥቱ ፡ አስቀመጣት ።

የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ከኀጢአት ፡ ሁሉ ፡ የሚበልጡ ትን ፡ ሁለት ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያሉ ፡ በደሎች ፡ በቤርሳቤሕ ፡ ፍቅር ፡ ምክ

ንያት ፡ የሠራቸውን ፡ በሸዋ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ተጻፈ ፡ ጽሑፍ ፡ የፍት ወት ፡ ደስታ ፡ ነፋስ ፡ ከልቡ ፡ ላይ ፡ ጠርጎ ፡ ደመሰሳቸው ።

ከዕለታት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ሕዝቡ ፡ ሳያውቀው ፡ በተፈጸመለት ፡ ደስታ ፡ ደስ ፡ ስላለው ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ አዳራሽ ፡ ተቀመጠ ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ደወል ፡ ይደውላል ፤

አሽከር ፡ ይገባል ።

አንተ ፤ ብላቴና ፤ ወዳጄን ፡ ጥራልኝ ፡ እንድንጫወት ፤

አገኘሁ ፡ ደስታ ፡ በርሷ ፡ ነፃነት ።

ደንገጡሮች ፡ ይምጡ ፡ ተከትለዋት ፤

ዘፋኞችም ፡ ይግቡ ፡ እንዲያጫውቷት ።

አሽከር ፡ ይሄድና ፡ ቤርሳቤሕን ፡ ይጠራል ።

ቤርሳቤሕም ፡ ከደንገጡሮቿ ፡ ጋራ ፡ መጥታ ፡ ከንጉሡ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ቆማ ፡ እጅ ፡ ትነሣለች ። ንጉሥ ፡ ዳዊትም ፡ በትረ ፡ መንግሥቱን ፡ ከዙፋኑ ፡ ላይ ፡ አንሥቶ ፡ ይዘረጋላታል ፤ እሷም ፡ በትረ ፡ መንግሥቱን ፡ ይዛ ፡ ወደሱ ፡ ትጠጋለች ። በንጉሥ ፡ ዳዊትም ፡ በግራው ፡ በኩል ፡ ከዙፋኑ ፡ ላይ ፡ ትቀመጣለች ፤ ደንገጡሮቿም ፡ በዙፋኑ ፡ ደረጃ ፡ ላይ ፡ ይቀመጣሉ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የተዋቡ ፡ የእስራኤል ፡ ልጆች ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ዘፋኞች ፡ ዐዋቆች ፡ በገና ፡ ፒያኖ ፡ ቪዮሎ ፤ የሚጫወቱ ፡ ይገባሉ ።

ፕሮግራሙ ።

፩ ፤ አንዲት ፡ ውብ ፡ የሆነች ፡ ሴት ፡ ብቻዋን ፡ ቪዮሎ ፡ ትጫወታለች ።

፪ ፤ የፒያኖ ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ተጫዋች ፡ ልብን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ የፒያኖ ፡ ዜማ ፡ ታሰማለች ።

፫ ፤ በጣም ፡ ደስ ፡ የሚያሰኙ ፡ ሕፃናት ፡ ፒያኖውን ፡ ተከትለው ፡ ባሌት ፡ የሚባለውን ፡ ዳንስ ፡ ያደርጋሉ ።

፬ ፤ ሁሉም ፡ ዘፋኞች ፡ በፒያኖና ፡ በቪዮሎ ፡ እየተመሩ ፡ መልካም ፡ ዜማ ፡ እያዜሙ ፡ ከቤርሳቤሕና ፡ ከዳዊት ፡ አንገት ፡ ላይ ፡ አበባ ፡ ያደርጋሉ ።

አሽከር ፡ ይገባል ፤

ግርማዊ ፡ ሆይ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነቢይ ፡ ናታን ፡ መጥቷል ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በጣም ፡ ደንግጦ ፡

ሂዱ ፡ እናንተ ፡ ልጆች ፡ ከቤርሳቤሕ ፡ ጋራ ፤

በጣም ፡ ደነገጥሁኝ ፡ ምነው ፡ ልቤ ፡ ፈራ ።

የእግዚአብሔር ፡ ነቢይ ፤ አይመጣም ፡ ያላንዳች ፤
የልብ ፡ የሚያውቅ ፡ ነው ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በታች ።

ቤርሳቤሕም ፡ ደንገጡሮቿን ፡ አስከትላ ፡ ዘፋኞቹና ፡ ሕፃናቱም ፡ ተከትለዋት ፡ ወጡና ፡ ወደ ፡ ሌላው ፡ ክፍል ፡ ገቡ ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ አሽከር ፡ ይጠራል ፤
አሽከር ፡ ይገባል ።
የእግዚአብሔርን ፡ ነቢይ ፡ ናታንን ፡ ጥራው ፤
ነቢዩ ፡ ናታን ፡ ይገባል ።
ንጉሥ ፡ ዳዊትም ፡ በረከት ፡ ለመቀበል ፡ ከዙፋኑ ፡ ላይ ፡ ተነሥቶ ፡ ከጫማው ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፡ ናታን ፡ ነቢዩም ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊትን ፡ በጁ ፡ ከግሩ ፡ ላይ ፡ አንሥቶ ፡
ንጉሥ ፡ ሆይ ፡ ተነሣ ፡ ከልጋኽ ፡ ላይ ፡ ተቀመጥ ፡ ፍርድኽን ፡ ልበስ ፤
አንድ ፡ ነገር ፡ ሰማኹ ፡ በጣም ፡ የሚያስለቅስ ።
በእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ በእስራኤል ፤ ከተማ ፡
እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ግፍ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይሰማ ።
ንጉሥ ፡ ሆይ ፤
ጕዳዩም ፡ ይኸ ፡ ነው ፡ በጣም ፡ ተመልከት ፤
አንድ ፡ ድኻ ፡ አንዲት ፡ በግ ፡ ብትኖረው ፡ ከቤት ፡
እጅግ ፡ የሚወዳት ፡ እንደናት ፡ እንደት ።
አብራ ፡ የምትበላ ፡ ከማዕዱ ፡ እንጀራ ፡
ሲወጣ ፡ እምትወጣ ፡ እንደ ፡ ባልንጀራ ።
ዘጠና ፡ ዘጠኝ ፡ በግ ፡ ያለው ፡ ሀብታም ፡ ሰው ፡
ነጥቆ ፡ ወሰደበት ፡ ምንም ፡ ሳይለው ።
ሊገለው ፡ ስለ ፡ ፈለገ ፡ ሊያጠፋው ፡ ካገር ፡
ጥፋቱ ፡ እንዲሰወር ፡ እንዳይቸገር ።
ዳኛ ፡ ዳኛ ፡ ቢልም ፡ ዳኛ ፡ ካለም ጠፋ ፡
ሁሉም ፡ አጥፊ ፡ ሆነ ፡ የሰው ፡ አመል ፡ ከፋ ።
እኛም ፡ ባንዳድ ፡ ጦር ፡ ስለተወጋን ፡
በራስ ፡ ላይ ፡ ለመፍረድ ፡ እጅግ ቸገረን ።
ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በጣም ፡ ተቈጥቶ ፡
ይኸ ፡ ሰው ፡ እንዳለ ፡ በእስራኤል ፡ ከተማ ፡
የተቈረጠ ፡ ነው ፡ ለመሞት ፡ ወይም ፡ ለመታሰር ፡ በጽኑ ፡ ጨለማ ።

ሕያው ፡ እግዚአብሔርን ፡ ብዬ ፡ ምያለሁ ፤
ይህነን ፡ ግፈኛ ፡ ከዚህ ፡ ከመንግሥቴ ፡ አጠፋዋለሁ ።
ነቢዩ ፡ ናታን ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ በጣቱ ፡ እያመለከተ ፡
የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ አንተ ፡ ነኽ ፤
የቀባኽን ፡ አምላክ ፡ በውነት ፡ የበደልኽ ፤
እኔ ፡ ነኝ ፡ ይልኻል ፡ ከጠላት ፡ ያዳንኩኽ ፡ ጋሻና ፡ ጦርኽ ።
ኀጢአትን ፡ ሠራኽ ፡ ማንም ፡ ማን ፡ ሳይሰማ ፡
እኔ ፡ እገልጠዋለሁ ፡ በወገኖችኽ ፡ ፊት ፡ በእስራኤል ፡ ከተማ ።
ዳዊት ፡ ሆይ ፡
እንደዚህ ፡ ይልኻል ፡ የዓለሙ ፡ ጌታ ፤
ፍርድ ፡ ሲጐድል ፡ አልወድም ፡ ድኻ ፡ ሲንገላታ ።
እንግዴህ ፡ አድምጠኝ ፡ ስማኝ ፡ ልንገርኽ ፤
ኦርዮንን ፡ በሰይፍ ፡ በግፍ ፡ አስገደልኽ ፤
ሚስቱንም ፡ ወሰድካት ፡ ላንተ ፡ እንድትሆንኽ ።
በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ነቢይ ፡ ይህ ነን ፡ ብርቱ ፡ የሆነ ፡ ግሣጼ ፡ ቢሰማ ፡ በብርቱ ፡ ኀዘን ፡ በትር፡ ተመታ ። በደስታ ፡ ምክንያት ፡ ተዳፍኖ ፡ የነበረው ፡ የጸጸት ፡ እሳት ፡ በልቡ ፡ ውስጥ ፡ መንደድ ፡ ዠመረ ። ጸጸት ፡ ያንቀላፋል ፡ እንጂ ፡ አይሞትም ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ጸጸት ፡ ከእንቅልፉ ፡ ነቃ ። እግዚአብሔር ፡ ኀጢአትን ፡ ከመሥራታችን ፡ ይልቅ ፡ የሠራነውን ፡ ኀጢአት ፡ በመርሳታችን ፡ ስለሚያዝን ፡ ነቢዩን ልኮ ፡ ብርቱ፡ ኀጢአቱንና ፡ በደሉን ፡ እንዲያስታውስ ፡ ተዳፍኖ ፡ የነበረውን ፡ ጸጸት ፡ በወቀሣ ፡ ዘንግ ፡ ቈሰቈሰው ።

ንጉሥ ፡ ዳዊትም ፡ የዓለምን ፡ ከንቱነት ፡ መሸፈኛዎች ፡ ደስታና ፡ ከንቱ ፡ ውዳሴን ፡ ነቢዩ ፡ በወቀሣ ፡ በገፈፈው ፡ ጊዜ ፡ በደመና ፡ ተሸፍነው ፡ የነበሩ ፡ አገሮች ፡ ደመናው ፡ ሲገፈፍ ፡ ወለል ፡ ብለው ፡ እንደሚታዩ ፡ ለንጉሥ ፡ ዳዊትም ፡ በደሉና ፡ ኀጢአቱ ፡ ወለል ፡ ብለው ፡ ስለታዩት ፡

አቤቱ ፡ ይቅር ፡ በለኝ ፡ አንተ ፡ ቸር ፡ ጌታዬ ፤
በኀጢአት ፡ ክብደት ፡ ቈስሏል ፡ ትከሻዬ ፡

ብሎ ፡ ከዙፋኑ ፡ በታች ፡ ከመሬት ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ የመረረ ፡ ልቅሶ፡ ያለቅስ ፡ ዠመር ።

ነቢዩ ፡ ናታንም ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ የእግዚአብሔር ፡

ወዳጅ ፡ ዳዊት ፡ በኀጢአት ፡ ተሰናክሎ ፡ አዝኖ ፡ ከመሬት ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ በማየቱ ፡ እጅግ ፡ አዘነ ፤ ስለ ፡ ኀጢአቱ ፡ ስርየት ፡ እንዲያገኝ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ እየለመነ ፡ እጁን ፡ ይዞ ፡



የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ አንተ ፡ ነኽ ፡
የቀባኽን ፡ አምላክ ፡ በውነት ፡ የበደልኽ ።

ተነሣ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፡ ውጣ ፡ ከበደል ፡ ማጥ ፡ ኀጢአትን ፡ ተው ፡
የሚረዳኽ ፡ የለም ፡ የሚያድንኽ ፡ ሰው ።
እመን ፡ በወዳጅህ ፡ ልብኽ ፡ አያመንታ ፤
ነገር ፡ ግን ፡ ሕፃኑ ፡ ይሞታል ፡ በበደልኽ ፡ ፈንታ ።
ወደ ፡ ፊት ፡ ግን ፡ አለ ፡ ትልቅ ፡ ያለም ፡ ተስፋ ፡

ከዘርኽ ፡ የሚወርድ ፡ የዓለምን ፡ ኀጢአት ፡ በሞቱ ፡ እሚያጠፋ ፡ ብሎ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነቢይ ፡ ናታን ፡ ትንቢት ተናግሮ ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ውስጥ ፡ ወጥቶ ፡ ሄደ ።

የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ግን ፡ ሌሊቱን ፡ ሁሉ ፡ የማቅ ፡ ቀሚስ ፡ ለብሶ ፡ አንዲት ፡ ኬሻ ፡ ብቻ ፡ ከመሬት ፡ አንጥፎ ፡ ዘውዱን ፡ ከመሬት ፡ ላይ ፡ ጥሎ ፡ የንስሓ ፡ ዕንብ ፡ እንደ ፡ ጐርፍ ፤ ፊቱን ፡ እያለበሰው ፡ ይወድቅ ፡ ይነሣ ፡ ይጸልይ ፡ ይሰግድ ፡ ነበር ።

ዳዊት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ወዳጅ ።
አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ማረኝ ፡ እባክ፝ህ ፤
ኀጢአቴን ፡ ሁሉ ፡ ፋቅልኝ ፡ በቸርነትኽ ።
አቤቱ ፡ በአዛብ ፡ እፀበኝ ፡ አንጻኝ ፡ ከብዙ ፡ ኀጢአቴ ፤
ባንተ ፡ ፊት ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ የሚመረመረው ፡ ልቤ ፤ ኵላሊቴ ፤
ከናቴ ፡ ማሕፀን ፡ በተጣልኩኝ ፡ ዘመን ፤
ማነው ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ የረዳኝ ፡ እኔን ።
እኔ ፡ አንድ ፡ ጭንጋፍ ፡ ትል ፡ የሌለኝ ፡ ዘመድ ፤
ባንተ ፡ አይደለም ፡ ወይ ፡ ያገኘሁት ፡ ዘውድ ።
አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ከጠለቀ ፡ ጉድጓድ ፡ ወድቅሁ ፡ ተሰበርኩ ፤
እጅ፝ህ ፡ ካላወጣኝ ፡ ቀረሁ ፡ ተሸነፍኩ ።
ተሥረገረግሁ ፡ ሰጠምኩ ፡ ጭቃው ፡ እላዬ ፡ ወጣ ፤
ተጨነቅሁ ፡ ጐበጥሁ ፡ ሆንኩኝ ፡ እንዳንበጣ ።

ማዕበልና ፡ ሞገድ ፡ በላዬ ፡ ፈሰሰ ፤
ኀይሌም ፡ ተናደብኝ ፡ እንደ ፡ ቤት ፡ ፈረሰ ።
ተጣልኩ ፡ ተናቅሁ ፡ ወዳጅም ፡ አጣሁ ፤
ለመሸሽ ፡ ከዚህ ፡ ጭንቅ ፡ ሥፍራ ፡ ባገኘሁ ፤
አቤቱ ፡ እኔ ፡ በደለኛ ፡ ሰውም ፡ አይደለሁ ።
ዘመኔም ፡ በፊትኽ ፡ እንደ ፡ ምናምን ፡ ነው ፤
ሀብቴም ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ቶሎ ፡ የሚያልፍ ፡ ነው ፤
ክብሬም ፡ እንዳበባ ፡ በፍጥነት ፡ ይረግፋል ፡
መንግሥቴም ፡ ለባዕድ ፡ ለማላውቀው ፡ ያልፋል ።

አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ይቅር ፡ በለኝ ፡ በውነት ፡ በድያለሁ ፡
ለሚያልፍ ፡ ደስታ ፡ አንተን ፡ ለውጫለሁ ።
ይገባኝ ፡ ነበረ ፡ ሰው ፡ ክቡር ፡ መሆኑን ፡ ማወቅ ፡ መጠየቅ ፡
ለምለም ፡ ሣር ፡ በማየት ፡ ገደል ፡ ከመውደቅ ።
ልብ ፡ የሌላቸውን ፡ እንስሶች ፡ መሰልኩ ፡
ለምለም ፡ ሣር ፡ በማየት ፡ ከገደል ፡ ወደቅኩ ።

አቤቱ ፡ ልመናዬን ፡ ሰምተኽ ፡ ፈጥነኽ ፡ አድነኝ ።
ቸሩ ፡ ፈጣሪዬ ፡ መድኀኒት ፡ ሁነኝ ።
አቤቱ ፡ አንተን ፡ ቀና ፡ ብዬ ፡ ማየቱ ፡ ጨነቀኝ ፤
ኀፍረቴ ፡ እንደ ፡ ሸማ ፡ ፊቴንም ፡ ሸፈነኝ ።
አቤቱ ፡ ኀጢአቴ ፡ በዝቶ ፡ በውነት ፡ ተጨነኩ ፤
ስለ ፡ ሸክሙ ፡ ክብደት ፡ ወደቅሁ ፡ ተሰበርኩ ።

አቤቱ ፡ በመንግሥትኽ ፡ ውስጥ ፡ ማነው ፡ የሚኖር ፡
በጸጋኽስ ፡ ጥላ ፡ ውስጥ ፡ ማነው ፡ የሚያድር ።
አቤቱ ፡ ሰዎች ፡ ተበላሹ ፡ ወደቁ ፡ ካዘቅት ፡
ለማን ፡ ልትሆን ፡ ነው ፡ የእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ።
ብሎ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በግንባሩ ፡ ከመሬት ፡ ላይ ፡ ተደፍቶ ፡
ያለቅስ ፡ ነበር ።

የእግዚአብሔር ፡ ቅዱስ ፡ መልአክ ፡ ለማጽናናት ፡ ለጠየቀው ፡
መልስ ፡ ለመናገር ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ተልኮ ፡ ካጠገቡ ፡ ቆመ ።
ንጉሥ ፡ ሆይ ፡ ተነሣ ፡ ስማኝ ፡ ልንገርኽ ፡
ለጠየቅኸው ፡ ጉዳይ ፡ መጣሁ ፡ ላስረዳኽ ።

በእግዚአብሔር ፡ መንግሥት ፡ የሚኖረው ፡ በውነት ፡ የጸደቀ ፡
ልቡን ፡ ከቂም ፡ በቀል ፡ በፍጹም ፡ ያራቀ ።
ለድኻ ፡ ወንድሙ ፡ ገንዘቡን ፡ ባራጣ ፡ በብድር ፡ ያልሰጠ ፡
ኀጢአትን ፡ ትቶ ፡ ጽድቅን ፡ የመረጠ ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ የሚያጽናና ፡ መልአክ ፡ ድምፅ ፡ በመስማቱ ፡
ደስ ፡ ብሎት ፡
የእግዚአብሔር ፡ መልአክ ፡ ስማኝ ፡ ልንገርኽ ፡
መልክተኛም ፡ ብትሆን ፡ አማላጅም ፡ ነኽ ።
ኀጢአትን ፡ ሠራሁ ፡ ጌታዬን ፡ በደልኩ ፡
ለኔ ፡ ደስታ ፡ ስል ፡ ወንድሜን ፡ ገደልኩ ።

ጐበጥሁ ፡ በሰበስሁ ፡ ተበላሁ ፡ በኀጢአት ፡ ትል ፡
እጄም ፡ ተበላሽቷል ፡ ደም ፡ ደም ፡ ይሸታል ።
እኔ ፡ ኀጢአተኛ ፡ የጠፋሁ ፡ የረከስሁ ፡ የራቅሁ ፡ ካንተ ፡ ጸጋ ፡
ለመጣል ፡ የደረስኩ ፡ ከጠለቀ ፡ ዐዘቅት ፡ እንደ ፡ ገማ ፡ ሥጋ ፡
መልአክ ።

አይዞኽ ፡ ተስፋ ፡ አትቍረጥ ፡ እመን ፡ በእግዚአብሔር ፤
ጸሎትኽ ፡ ተሰምቷል ፡ ለቅሶኽም ፡ ጭምር ።
ዕንባኽ ፡ ኀጢአትኽን ፡ ስላጠበልኽ ፡
ነጽተኽ ፡ ትታያለኽ ፡ ከርኵሰትኽ ።

በውነት ፡ ላደፈ ፡ ሰው ፡ ለተጨማለቀ ፡ በብርቱ ፡ ኀጢአት ፡
ዕንባ ፡ የነፍስ ፡ ደም ፡ ያጥባል ፡ ርኵሰት ።
ንጉሥ ፡ ዳዊት ፤
ለኔ ፡ ተነገርኸኝ ፡ ያምላክን ፡ ምሕረት ፡
የምለምንኽን ፡ ርዳኝ ፡ በፍጥነት ።

እለምንኻለሁ ፡ አጥብቄ ፡ ያምላክ ፡ መልክተኛ ፡
ልትረዳኝ ፡ ተመጣኽ ፡ ከውነተኛው ፡ ዳኛ ፡
ልጄን ፡ አድንልኝ ፡ እንዳይሞት ፡ እንደ ፡ በደለኛ ።

አባት ፡ መጻጻ ፡ ምግብ ፡ ቢወስድ ፡ ለመብል ፡
የልጅ ፡ ጥርስ ፡ አይጠርስም ፡ ተብሎ ፡ ተነግሯል ፡ በነቢያት ፡ ቃል
ልጄ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይሙት እኔ ፡ በሠራሁት ፡ በራሴ ፡ በደል ።

መልአኩ ፤

ንጉሥ ፡ ሆይ ፤

መራራ ፡ ዛፍ ፡ ሆነኽ ፡ ያፈራኸው ፡ ልጅ ፡
መቈረጡ ፡ አይቀርም ፡ ለማንም ፡ አይበጅ ።
ብሎት ፡ መልአከ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተሰወረ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ነቢዩ ፡ ናታን ፡ እንደ ፡ ተናገረው ፡ የእስራ ኤል ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ከኦርዮን ፡ ሚስት ፡ የወለደው ፡ ልጅ፡ ሞተ ፤ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ኦርዮንን ፡ በግፍ ፡ በማስገደሉ ፡ የመረረ፡ የንስሓ ፡ ኀዘን ፡ እንኳ ፡ ቢያዝን ፡ ደግሞ ፡ በሱ ፡ ኃጢአት ፡ ምክንያት ፡ የሚወደውን ፡ ሕፃን ፡ ነቢዩ ፡ ናታን ፡ ይሞታል ፡ ስላለው ፡ ዕጥፍ ፡ ኀዘን ፡ ነበረበት ። ስለዚህ ፡ ሕፃኑ ፡ በሞተ ፡ ጊዜ ፡ መኳንንቱና ፡ መሳፍንቱ ፡ ለማርዳት ፡ ፈሩ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ስንኳን ፡ የንጉሥ ፡ ልጅ ፡ በብዙ ፡ ክብርና ፡ ማዕርግ ፡ የሚቀበርና ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ ቢሆን ፡ የመጨረሻ ፡ መሰናበቻ ፡ ክብር ፡ ስለሚደረግለት ፡ የለቅሶውን ፡ በዓል ፡ ለማደራጀት ፡ ሲሉ ፡ ለማርዳት ፡ ግዴታ ፡ ሆነባ

ቸው ፡ ሁለት ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ያሉ ፡ የክህነትና ፡ የምስፍና ፡ ማዕርግ ፡ ያላቸው ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ገብተው ፡

ንጉሥ ፡ ሆይ ፤

የምትወደው ፡ ሕፃን ሞተ ፡ በዚህ ፡ በሌሊት ፤
ከመቻል ፡ በስተቀር ፡ የለም ፡ መድኀኒት ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ አስቀድሞ ፡ ሕፃኑ ፡ ታሞ ፡ ሳለ ፤ እግዚአብ ሔር ፡ እንዲምርለት ፡ አዝኖ ፡ አልቅሶ ፡ ነበር ፤ ነገር ፡ ግን ፡ የእግዚ አብሔር ፡ አሳብና ፡ የሰው ፡ አሳብ ፡ ከሰማይና ፡ ከምድር ፡ የራቀ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ኦርዮን ፡ በግፍ ፡ ከጦር ፡ሜዳ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ንጉሠ ፡ ነገ ሥቱ ፡ ክብር ፡ ሲሞት ፡ ይህ ፡ የረቀቀ ፡ አገዳደል ፡ ለልዑል ፡ እግ ዚአብሔር ፡ በጣም ፡ ስላሳዘነው ፡ ይልቁንም ፡ ኦርዮን ፡ በእጁ ፡ ዘግኖ ፡ የዘራው ፡ ደም ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በግፍ ፡ ያበቀለውን ፡ ፍሬ ፡ እንዳያድግ ፡ በጨርቋው ፡ እንዲቀጠፍ ፡ አደረገው ። ስለ ዚህ ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ፈርዶ ፡ ለልጁ፡ ሞት ፡ ሳያዝን ፡ የክብሩን ፡ ልብስ ፡ እንዲያመጡለት ፡ አሽከር ፡ ይጠራል ።

ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ደወል ፡ ይደውላል ፤
አሽከር ፡ ይገባል ።
አምጣልኝ ፡ ካባዬን ፡ ደርብልኝ ፡ በላይ ፡
ዘውዴንም ፡ ጫንብኝ ፡ ከጎባኔዬ ፡ ላይ ።
ኀዘኔ ፡ ቢበዛ ፡ ልጄ ፡ አይመለስም ፤
የፈሰሰ ፡ ውሃ ፡ በጅ ፡ አይታፈስም ።
ጥራ ፡ መሳፍንቱን ፡ መኳንንቱን ፡ ጭምር ፡
በጣም ፡ ስለሚያውቁት ፡ የሕፃኑን ፡ ፍቅር ።

አሽከር ፡ መኳንንቱንና ፡ መሳፍንቱን ፡ ያስገባል ፤ መሳፍንቱና፡ መኳንንቱ ፡ ከንጉሡ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ቆመው ፡ እጅ ፡ ይነሡና ፤ በጣም ፡ ይደነቃሉ ፤ ምክንያቱም ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ከኦርዮን ፡ሚስት፡ የወለደው ፡ ሕፃን ፡ ታሞ ፡ ከልክ ፡ የተረፈ ፡ መራራ ፡ ኀዘን ፡ ሲያዝን፡ በማየታቸው ፡ የሞተ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሣችን ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይሰማዋል ፡ በማለት ፡ ተጨንቀው ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ንጉሡ ፡ ዳዊት ፡ የክብር ፡ልብስ፡ ለብሶ ፡ ኀዘኑን ፡ ትቶ ፡ በማየታቸው ፡ ነው ።

መኳንንቱ ፡ ተነሥተው ፡

ንጉሥ ፡ ሆይ ፤

የምትወደው ፡ ሕፃን ፡ መሞቱን ፡ ስትሰማ ፡
መስሎን ፡ ነበር ፡ ለኛ ፡ በጥቀኑር ፡ ይሸፈን ፡ የእስራኤል ፡ ከተማ ።
አንተን ፡ ከዙፋን ፡ ላይ ፡ በክብር ፡ ብናይኸ ፡
በጣም ፡ ተደነቅን ፡ ስለ ፡ ተለወጠ ፡ ጥንታዊ ፡ ሕግኽ ።

የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ለመሳፍንቱና ፡ ለመኳንንቱ ፡ እንደዚህ ፡ ብሎ ፡ ይመልስላቸዋል ።

እግዚአብሔር ፡ ሰጥቶ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቢነሣ ፡
ምንም ፡ አያስፈልግ ፡ በልቅሶ ፡ ወቀሳ ።
ሰው ፡ ኀጢአት ፡ ሠርቶ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ ሲጣላ ፡
ከመጨነቅ ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ የለው ፡ መላ ።

አካላቱ ፡ ሁሉ ፡ ይሆናል ፡ መራራ ፡
ፍሬውም ፡ ሳይቀር ፡ ከቅጠሉ ፡ ጋራ ።
ኀጢአት ፡ ጦር ፡ ሠርቶ ፡ በሚዋጋ ፡ ጊዜ ፡
መመከት ፡ ይገባል ፡ ሳይሰንፉ ፡ ሁልጊዜ ።
እንግዴህ ፡ እንተወው ፡ ኀዘናችንን ፤
ጥንቱን ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡ አለመሆን ።
ይልቅ ፡ ደስ ፡ ይበለን ፡ በሚመጣው ፡ ልጅ ፡
ይህን ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ በደም ፡ የሚዋጅ ።
ስለ ፡ ኀጢአታችን ፡ ተዋጋ ፡ ተብሎ ፡ የተነገረለት ፡ የዓለም ፡ ንጉሥ ፡
እንናፍቃለን ፡ ከዚያ ፡ ለመድረስ ።

ውሃ ፡ ጠማኝ ፡ ብሎ ፡ ሲለምን ፡ ሰምተው ፡
ሐሞት ፡ አመጡለት ፡ ከሞት ፡ የመረረ ፡ እንዲሆን ፡ ብለው ።
የሱን ፡ ድምፅ ፡ መስማት ፡ ሁሉንም ፡ ያስንቃል ።
ወደኔ ፡ ኑ ፡ እያለ ፡ በጣሙ ፡ ይጮኻል ።

ልጅ ፡ ነው ስላችሁ ፡ ጌታዬ ፡ እሱ ፡ ነው ፤
በአብ ፡ ቀኝ ፡ ተቀምጦ ፡ ዐይኔ ፡ የሚያየው ።
ማየት ፡ እናያለን ፡ አናስተውልም ፡ እኛ ፤
ዐውቀናል ፡ በማለት ፡ ይፈረድብናል ፡ እንደ ፡ ወንጀለኛ ።

እንግዴህ ፡ እንርሳው ፡ የኀዘንን ፡ በትር ፡ የሰውን ፡ መከራ ፤
ይህ ፡ ጽዋ ፡ ይደርሳል ፡ ለሁሉም ፡ በተራ ፡ በተራ ፡

ብሎ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፡ ስለ ፡ ክርስቶስ ፡ መምጣትና ፡ ስለ ፡ ዓለም ፡ ኀጢአት ፡ መሞቱን ፡ ትንቢት ፡ በተናገረ ፡ ጊዜ ፡ መሳፍንቱና ፡ መኳንንቱ ፡ በጣም ፡ ገርሟቸው ፡ እየተደነቁ ፡ እጅ ፡ ነሥተው ፡ ወጡ ።



# አልሞትኹም ፡ ብዬ ፡ አልዋሽም ።

ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ።

ባ፲፱፻፵፩ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ።

ከራስ ፡ ቢ. መኰንን ፡ እንዳልካቸው ፡ ተጻፈ ።

፩ ፡ ያቶ ፡ ተማቹና ፡ የወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡

ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ።

፪ ፤ ባጭሩ ፡ የማይ ፡ ጨው ፡ ጦርነትና ፡

የዓለም ፡ ፖለቲካ ።



እግዚአብሔር ፡ ሊረዳው ፡ የሚወደውን ፡

ማንም ፡ ተንኰል ፡ ሊጐዳው ፡ አይችልም ።

# መ ቅ ድ ም ።

ባ፲፱፻፳፫ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ በውጋዴ ፡ በኩል ፡ በተደረ ገው ፡ በውነተኛው ፡ ጦርነት ፡ ታሪክ ፡ ላይ ፡ ላንባቢዎች ፡ እን ዳይሰለች ፡ ያቶ ፡ ተማቹና ፡ የወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ ለማጣፈጫ ፡ ተጨምሮበታል ።

ምክንያቱም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ በጁ ፡ የያዘውን ፡ መጽሐፍ ፡ በጠቅላላ ፡ ልብ ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ ድረስ ፡ ለማንበብ ፡ በሺሕ ፡ የሚቈጠሩትን ፡ ያሳብ ፡ ወሮች ፡ በኅሊናው ፡ ላይ ፡ እንዳይሰፍሩ፡ ለማባረር ፡ የጣፈጠ ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ መጻፍ ፡ ያስፈልጋል ፡ ባለፈው ፡ ዘመን ፡ አሁንም ፡ ቢሆን ፡ የሰውን ፡ ልጅ ፡ አሳብ ፡ ባንድ፡ ላይ ፡ ጠቅሎ ፡ ለመምራት ፡ ብዙ ፡ ሊቃውንት ፡ ደክመውበታል ።

ለምሳሌ ፡ የሚያሳዝኑ ፡ መንፈሳዊ ፡ ዜማና ፡ የሙዚቃን ፡ ኖት ፡ (ሥረይ) ፡ ያከናወኑ ፡ አሉ ። ደግሞ ፡ የሰዎችን ፡ ችግርና፡ መከራ ፡ ኃዘንና ፡ ጭንቅ ፡ በፊታቸው ፡ ላይ ፡ ገልጸው ፡ በሥዕል፡ ለማሳየት ፡ የጣሩ ፡ አሉ ።

ይልቁንም ፡ ያልተደረገውን ፡ እንደ ፡ ተደረገ ፡ እያስመሰሉ፡ አሳዛኝ ፡ ምክንያት ፡ የሚሆኑትን ፡ ነገሮች ፡ እየመረጡ ፡ የሰውን ፡ ልብ ፡ የሚነኩና ፡ ያሳብን ፡ ወሮች ፡ የሚያባርሩ ፡ ልብ ፡ ወለድ፡ ታሪክ ፡ የጻፉ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ይገኛሉ ።

ነገር ፡ ግን ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ወፍ ፡ በኅሊናው ፡ ላይ ፡ የሚ በሩትን ፡ አሳቦች ፡ ለመከላከል ፡ ሥልጣን ፡ አጣ ። ለምሳሌ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ላንድ ፡ ሊቅ ፡ ለሆነ ፡ ወዳጁ ፡ ማሰብ ፡ ዋና ፡ ኀጢ አት ፡ ነው ፡ ተብሏል ፤ የሰው ፡ ልጅ ፡ አሳቡን ፡ ለመከላከል ፡ ዐቅም፡ የለውም ፤ ስለዚህ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ከኀጢአት ፡ ንጹሕ ፡ ለመ ሆን ፡ ይችላል ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ።

ያም ፡ ሊቅ ፡ ለወዳጁ ፡ በሰማይ ፡ የሚበሩትን ፡ ወፎች ፡ ከራ ስኽ ፡ በላይ ፡ እንዳይበሩ ፡ ለመከላከል ፡ ትችላለኽን ፡ ብሎ ፡ ጠየ ቀው ።

እሱም ፡ ይህስ ፡ አይቻልም ፡ ብሎ ፡ መለሰለት ።

ሊቁም ፡ እንግዲያውስ ፡ በራስኽ ፡ ላይ ፡ ወፎች ፡ ጐጐ ፡ እንዳ ይሠሩብኽ ፡ ተጠንቀቅ ፡ እንጂ ፤ በላይኽ ፡ ላይ ፡ የሚበሩት ፡ ወፎች ፡ ካቅምኽ ፡ በላይ ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ አይፈረድብኽም ፡ አለው ፡ ይባላል ።

አንድ ፡ ሊቅ ፡ ያሳብን ፡ ነገር ፡ ከዚህ ፡ በታች ፡ ባለው ፡ በመ
ወድስ ፡ ቅኔው ።

ኢየዐርፍ ፡ ልብ ፡ ለተምኔተ ፡ ሥጋ ፡
እመኒ ፡ ይረክብ ፡ መንግሥተ ፡ ዕብራዊ፡ ዳዊት ።
ወለተምኔቱ ፡ ርሑቅ ፡ ፍና ፡ ሰማያት ፡
ኢይቴስንዎ ፡ ምስፍና ፡ ወሀብት ።

ከመ ፡ ይሡዕዎ ፡ ነቢያት ፡
ለምሳሌሁ ፡ ብግዕ ፡ እጐዝ ፡ ክልኤ ፡ አቅርንት ።
ለአዳምሂ ፡ ድኅረ ፡ አንገሦ ፡ በላዕለ ፡ ኵሉ ፡ ፍጥረት ፡
መንግሥቶ ፡ ለፈጣሪሁ ፡ ተመነየ ፡ በገነት ።
ወከዊነ ፡ አምላክ ፡ ፈተወ ፡ ልቡና ፡ ሔዋን ፡ ንግሥት ፡
ኵሉ ፡ ለእመ ፡ ሞተ ፡ አምጣነ ፡ ልቡና ፡ ኢይመውት ።
ብሎ ፡ እንዳስረዳን ፡

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ የሰው ፡ አሳብ ፡ የማይያዝ ፡ የማይጨበጥና ፡ ወደ
አየር ፡ የሚወጣ ፤ ወደ ፡ ቀላይ ፡ የሚወርድ ፡ እንደ ፡ ወፍ ፡ የሚበር ፡
ለመከልከል ፡ የማይቻልም ፡ ቢሆን ፡ እንኳ ፡ በላይኽ ፡ ጕገሮውን ፡
ሠርቶ ፡ እንዳያደነዝዝኽ ፡ መጽሐፍ ፡ አንብብ ። መንፈሳዊን ፡ ዜማና ፡
ሙዚቃ፡ ስማ፤ ስጦታ፡ እንዳለኽ፡ ሥዕል፡ በመሣል፡ ጊዜኽን፡ አሳልፍ ።



## ምዕራፍ ፡ ፩ ።

ባ፲፱፻፲፱ ፡ ዓ፡ ም፡ በደብረ ፡ ብርሃን ፡ ከተማ ፡ ውስጥ ፡ አንድ አቶ ፡ ተማቹ ፡ የሚባል ፡ ሰው ፡ ነበር ። ቤቱም ፡ ወደ ፡ ተጉለት ፡ ከሚወስደው ፡ መንገድ ፡ አጠገብ ፡ ካንድ ፡ ትልቅ ፡ ዛፍ ፡ በላይ ፡ ነው ። አቶ ፡ ተማቹ ፡ በንጹሕ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ መኖር ፡ ስለሚ ወድ ፡ ለሥራ ፡ ከተሠሩት ፡ ከሁለት ፡ ሰቀላ ፡ ቤቶች ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ የመኝታና ፡ የመጽሐፍ ፡ ማንበቢያ ፡ ሁለት ፡ ክፍል ፡ ያላት ፡ አን ዲት ፡ አራት ፡ ማዕዘን ፡ የምታምር ፡ ቤት ፡ ነበረችው ፡ እነዚሁም ፡ ሁለት ፡ ሰቀላ ፡ ቤቶች ፡ አንዲቱ ፡ ማድ ፡ ቤትና ፡ ፀጥ ፡ ቤት ፡ ሁለተኛዪቱ ፡ የከብቶች ፡ ማጎሪያ ፡ በረት ፡ ናት ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከብት ፡ ማርባት ፡ ስለሚወድ ፡ የቀንድ ፡ ከብ ቶችና ፡ የጋማ ፡ ከብቶች ፡ ዶሮዎችም ፡ በብዙ ፡ ነበሩት ። ሁለት ፡ ወንዶችና ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ አሽከሮች ፡ አሉት ፡

ከቤቱ ፡ ጥቂት ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ ቡሎ ፡ ወርቄ ፡ ከሚባለው ፡ ገበያ ፡ አጠገብ ፡ ሦስት ፡ የገባር ፡ መሬቶች ፡ ስላሉት ፡ ጊዜውን ፡ በርሻና ፡ በሥራ ፡ ያሳልፍ ፡ ነበር ። ከዚህም ፡ በቀር ፡ አቶ ፡ ተማቹ፡ አውሬ ፡ ማደንና ፡ የጦር ፡ ታሪክ ፡ ማንበብ ፡ ይወዳል ። ይልቁንም በዱር ፡ ጊዜ ፡ በተፈጥሮ ፡ ጕልበታቸው ፡ የሚገርም ፡ የአርበኝነ ትና ፡ የኀይል ፡ ሥራ ፡ የሠሩትን ፡ ለምሳሌ ፤ እንደ ፡ ሶምሶን ፡ አን በሳውን ፡ በቡጢ ፡ መቶ ፡ የገደለውንና ፡ ባህያ ፡ መንጋጋ ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ ፈጅቶ ፡ ጠላቶቹን ፡ ያሸነፈውን ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፡ ባንድ ፡ ድንጋይ ፡ በወንጭፍ ፡ ጎልያድን ፡ ጥሎ ፡ ለወገኑ ፡ መመኪ ያና ፡ ታዳጊ ፡ እንደ ፡ ሆነው ፡ ያለ ፡ ያርበኝነት ፡ ታሪክ ፡ ነው ።

ይልቁንም ፡ ያገሩ ፡ የኢትዮጵያ ፡ አርበኞች ፡ በፈረስ ፤ በጦ ርና ፡ በጐራዴ ፡ በጋሻ ፡ አመካከት ፡ መቀልጠፍ ፡ ራሳቸውን ፡ አድ ነው ፡ ጠላታቸውን ፡ ያጠቁትን ፡ የጀግንነት ፡ ወሬ ፡ መስማት ፡ ከሁሉ ፡ የበለጠ ፡ ደስታው ፡ ነው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ አንድ ፡ ውዥግራ ፡ ጠመንዣ ፡ አንድ ፡ ጦርና፡ ጋሻ ፡ አንዲት ፡ ጩቤ ፡ ነበሩት ። ዕድሜውም ፡ ኻያ ፡ አምስት ፡ ዓመቱ ፡ ነበር ። ከዕለታት ፡ ፩ ፡ ቀን ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ እንደ ፡ ተለ መደው ፡ በማለዳ ፡ ጎሕ ፡ ሲቀድ ፡ ጦሩን ፡ ይዞ ፡ ጋሻውን ፡ አን ግቦ ፡ ከቤቱ ፡ አጠገብ ፡ ካለው ፡ ዱር ፡ ውስጥ ፡ እየተሹለከለከ ፡ የሚበላ ፡ አውሬ ፡ ሲያድን ፡ በድንገት ፡ አንድ ፡ ነብር ፡ በጣም ፡ ከቀረበ ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ አጋጠመው ።

አቶ ፡ ተማቹም ፡ ዘወትር ፡ የሚመኘው ፤ አንድ ፡ ያርበኝነት ሥራ ፡ የሚያሳይበትንና ፡ የችግርን ፡ ጠባብ ፡ በር ፡ ተፍጨርጭሮ ፡ የሚወጣበትን ፡ ትግል ፡ ስለሆነ ፡ በድፍረት ፡ ጋሻውን ፡ መክቶ ፡ ወደፊቱ ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ተራምዶ ፡ በኀይል ፡ ጦሩን ፡ ወርውሮ ፡ ነብሩን ፡ ከሽንጡ ፡ ላይ ፡ ወጋው ።

ያም ፡ እልከኛው ፡ ነብር ፡ ውጊው ፡ ስለተሰማው ፡ በኀይል ፡ ተወርውሮ ፡ ያቶ ፡ ተማቹን ፡ ራስ ፡ ለመፈጥፈጥ ፡ ሲጣጣር ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ራሱን ፡ ለማዳን ፡ ጋሻውን ፡ ሲመክት ፡ ነብሩ ፡ ጭንቅላ ቱን ፣ ያገኘ ፤ መስሎት ፡ በኀይል ፡ ጋሻውን ፡ ቢነክሰው ፡ ጥርሱ ፡

ከጋሻው ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ምስማር ፡ ስለ ፡ ተቀበቀበ ፡ በኀይል ፡ ካቶ፡ ተማቹ ፡ ክንድ ፡ ነጥቆ ፡ ጋሻውን ፡ ወሰደው ።

አቶ ፡ ተማቹም ፡ ቀኝ ፡ እጁን ፡ በጥፍሩ ፡ አጥብቆ ፡ ስለ ፡ ያዘው ፡ ክንዱ ፡ በብርቱ ፡ ቈሰለ ።



አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከነብር ፡ ጋራ ፡ ሲታገል ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ጦሩ ፡ ከጠላቱ ፡ ላይ ፡ ተቀብ ቅቦ ፡ ስለቀረ ፡ ጋሻውን ፡ ከክንዱ፡ላይ፡ ስለ ፡ ተነጠቀ፡ በተረፈችው ፡ መሣሪያ ፡ በጩቤው ፡ እየተዛወረ ፡ እልከኛውን፡ ነብር ፡ ይወጋው፡ ዠመር ። በኀይል ፡ የተነጠቀው ፡ ጋሻው ፡ የነብሩን ፡ ዓይኑንና ፡ አፉን ፡ ዘግቶ ፡ ስለ ፡ ያዘለት ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ጠላቱን ፡ ለማጥ ቃት ፡ በጣም ፡ ተመቸው ። በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ብርቱ ፡ ትግልና ፡ ውጊያ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ከተፈታተኑ ፡ በኋላ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከጡንቻው ፡ ላይ ፡ በቈሰለው ፡ ብርቱ ፡ ቍስል ፡ ምክንያት ፡ ነብ ሩም ፡ በጩቤ ፡ ከብዙ ፡ ላይ ፡ ስለቈሰለ ፡ ሁለቱም ፡ ደም ፡ አንዝዟ ቸው ፡ ለየብቻ ፡ ወደቁ ።

ከተለመደው ፡ ጊዜ ፡ ስላለፈ ፡ ሁለቱ ፡ አሽከሮቹ ፡ ጌታችን ፡ ምን ፡ ሆኖ ፡ ይሆን ፡ በማለት ፡ ለመፈለግ ፡ ዘወትር ፡ አውሬ ፡ ከሚያድን በት ፡ ደን ፡ ውስጥ ፡ ቢሄዱ ፡ አቶ ፡ ተማቹና ፡ እልከኛው ፡ ነብር ፡ በደም ፡ ተለውሰው ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ወድቀው ፡ ሲያቃስቱ ፡ ደረሱ ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ሁለቱም ፡ አሽከሮች ፡ በድንጋጤ ፡ ከግር ፡ እስከ ፡ ራሳቸው ፡ ድረስ ፡ ተንቀጠቀጡ ። ወዳፋፍ ፡ ብቅ ፡ ብለው ፤ የጐበዝ ፡ ያለኽ ፡ ኡ ፡ ኡ ፤ ድረሱልን ፡ እያሉ ፡ ይጮኹ ፡ ዠመር። የተጐለት ፡ ሕዝብ ፡ ጩኸት ፡ ሲሰማ ፡ ጋሻውን ፡ አንግቦ ፡ ጦሩን ፡ ይዞ ፡ መውጣት ፡ ዋና ፡ የተለመደ ፡ ተግባሩ ፡ ስለሆነ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ በፍጥነት ፡ ለርዳታ ፡ ደረሰ ። ወዲያው ፡ እየተኳከሩ ፡ እልከኛውን ፡ ነብር ፡ በጦር ፡ ወግተው ፡ ከጨረሱ ፡ በኋላ ፡ አቶ ፡ ተማቹንና ፡ እልከኛውን ፡ ነብር ፡ በቃሬዛ ፡ ተሸክመው ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ወሰዱ ትና ፡ ቍስሉን ፡ አጥበው ፡ ተኰሰው ፡ አስረውለት ፡ ካልጋው ፡ ላይ አስተኝተውት ፡ ሄዱ ። ነብሩንም ፡ አሽከሮቹ ፡ ቈዳውን ፡ እንዲገ ፉት ፡ በውጭ ፡ ከበሩ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ አጋድመውት ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ የጠላቱን ፡ ሬሳ ፡ ከውጭ ፡ ተጋድሞ ፡ እያየ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ለሰው ፡ ልጅ ፡ የሚገባው ፡ እውነተኛው ፡ ትግል ፡ በመ ቍሰሌ ፡ ምንም ፡ አላዝንም ፡ በታሪክ ፡ ሳነበው ፡ የነበረውን ፡ የሶም ሶንን ፡ አርበኝነት ፡ አሳሰበኝ ።

ስለዚህ ፡ ምኞቴ ፡ ስለተፈጸመ ፡ ብርቱ ፡ ቍስሌ ፡ አይሰማ ኝም ፡ እንግዲህ ፡ የምትቀረኝ ፡ ፍጹሚቱ ፡ ትግል ፡ ስላገሬ ፡ ከጠ ላት ፡ ጋራ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ታግሎ ፡ መውደቅ ፡ ብቻ ፡ ናት ።

ይህችም ፡ ቈንዠዪቱ ፡ ሞት ፡ የምትባለው ፡ ናት ፡ እያለ ፡ በጠለቀ ፡ አሳብ ፡ ተውጦ ፡ ሳለ ፡ ሌላ ፡ ኀዘን ፡ ተሰማው ። ኀዘኑም ይህ ፡ ነው ። ከጨካኝ ፡ አውሬ ፡ ጋራ ፡ ብርቱ ፡ ትግል ፡ በማድረግ ፡ ቈስዬ ፡ በደም ፡ ተነክሬ ፡ ዝዬ ፡ ወድቄ ፡ በጩኸት ፡ አገር ፡ ተሰ ብስቦ ፡ እኔን ፡ አርበኛውንም ፡ ነብር ፡ በቃሬዛ ፡ ይዘውን ፡ ወደቤቴ ሲወስዱኝ ፡ ስለምንድነው ፡ ቤቴ ፡ እልል ፡ ያላለች ፡ ወይም ፡ በጩ ኸትና ፡ በልቅሶ ፡ ያልተቀበለችኝ ፤ እንደዚሁ ፡ በራድ ፡ ሆና ፡ የቈ የችኝ ፡ እያለ ፡ ሲያስብ ፡ ከቈየ ፡ በኋላ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ አሁንስ ፡ ዐወቅሁት ፡ በጣም ፡ ገባኝ ። ቤት ፡ ያለሴት ፡ ሥጋ ፡ ያለነፍስ ፡ ምንም እንዳይረቡ ፡ የታወቀ ፡ ነው ። ሚስት ፡ ብትኖረኝ ፡ በመግደሌ ፡ እልል ፡ ትል ፡ ነበር ። ወይም ፡ በመቍሰሌ ፡ ኡ.. ኡ.. ትል ፡ ታለቅስም ፡ ነበር ።

ልጅም፡ቢኖረኝ ፡ ያግዘኝ ፡ ነበር ። በውነት ፡ ሰሎሞን ፡ አንድ፡ ከመሆን ፡ ሁለት ፡ መሆን ፡ ይሻላል ፡ ያለው ፡ እውነተኛ ፡ ጠቃሚ፡ ምክር ፡ ኖሯል ፡ እያለ ፡ በቤቱ ፡ በራድነት ፡ በጣም ፡ አዘነ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከዚያች ፡ ቀን ፡ ዠምሮ ፡ የምትረዳው ፡ ሚስት ፡ ለማግባት ፡ ቈረጠ ።

ሦስት ፡ ወር ፡ ያኽል ፡ በተቧጠጠው ፡ ቊስል ፡ ምክንያት ፡ ካልጋው ፡ ላይ ፡ ከተኛ ፡ በኋላ ፡ ጥቂት ፡ እንደ ፡ ተሻለው ፡ ለዘ መድ ፡ ለወዳጅ ፡ ጠባየ ፡ መልካም ፡ የሆነች ፡ ሴት ፡ እንዲፈልጉ ለት ፡ አስታወቀ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ልበ ፡ ቅንና ዕድለኛ ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ወዲ ያው ፡ ዘመድ ፡ ወዳጅ ፡ አስበው ፡ ተስማምተው ፡ አንዲት ፡ ቈንዦ፡ የተዋበች ፡ ጠባይዋ ፡ ቀና ፡ የሆነ ፡ የጨዋ ፡ ሰው ፡ ልጅ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ የምትባል ፡ ልጃ ፡ ገረድ ፡ አጩለት ።

አቶ ፡ ተማቹም ፡ ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳን ፡ ባያት ፡ ጊዜ ፡ በውበ ቷና ፡ በደም ፡ ግባቷ ፡ በጣም ፡ ተነካ ። በጠባይዋም ፡ እንደዚህ ፡ ከተዋበች ፡ ዕድለኛ ፡ ነኝ ፡ አለ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳም ፡ አቶ ፡ ተማቹን ፡ ባየችው ፡ ጊዜ ፡ በቁመቱና ፡ በመልኩ ፡ ይልቁንም ፡ የወታደርነቱን ፡ ቅልጥፍና ፡ የሥራ ፡ መውደዱን ፡ ጠባይ ፡ ትሰማ ፡ ነበርና ፡ በውነት ፡ ደካማ ፡ ባሕርዬን ፡ የሚያግዝ ፡ ጓደኛ ፡ አገኘሁ ፡ እያለች ፡ በኅሊናዋ ፡ ውስጥ ፡ ደስ ፡ አላት ።

ካምስት ፡ ወር ፡ በኋላ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ በ፳፰ ፡ ዓመቱ ፡ ወይ ዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ባ፲፱ ፡ ዓመቷ ፡ እንደ ፡ ሕጉ ፡ በቤተ ፡ ክርስ ቲያን ፡ ተጋቡ ። አንድ ፡ ዓመት ፡ ከሁለት ፡ ወር ፡ ከተቀመጡ ፡ በኋላ፡ አንድ ፡ ወንድ ፡ ልጅ ወለደች ፤ ስሙን ፡ ክንዴ ፡ ብሎ ፡ አባቱ፡ አወጣለት ። በቤተ ፡ ዘመዶቻቸውና ፡ በነሱም ፡ መካከል ፡ ወንድ፡ ልጅ ፡ በመገኘቱ ፡ ብዙ ፡ ደስታ ፡ ሆነ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በሁለት ፡ ዓመት ፡ ተከል ፡ ደግሞ ፡ አንድ ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፤ ስሙን ፡ ጋሻው ፡ በዛ ፡ ብሎ ፡ አወጣ ለት ። ጋሻው ፡ በዛን ፡ ከወለዱ ፡ ወዲህ ፡ ዐሥር ፡ ዓመት ፡ ያኽል፡ ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ሳትወልድ ፡ ቈየች ። ባሥራ ፡ አንደኛው ፡ ዓመት ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፤ ስሟንም ፡ ተዋበች ፡ ብላ ፡ አወጣችላት ። ደግሞ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ያኽል ፤ ሳትወልድ፡ ከረፈች ፡ በኋላ ፡ የመጨረሻ ፡ ልጅዋን ፡ አሸብር ፡ የሚባለውን ፡ ወለደች ።

አቶ ፡ ተማቹም ፡ የተመኘው ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ ስለ ፡ ተፈጸመለት ፡ በቤቱም ፡ በውጭም ፡ ደስ ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ ሆነ ። ዕድሜውም ፡ ዓርባ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡ ሆነው ።

ስለዚህ ፡ አሳቡ ፡ ሁሉ ፡ የበሰለና ፡ በሩቅ ፡ የሚያይ ፡ ሙሉ ፤ ሰው ፡ ሆነ ። ቢሆንም ፡ የጥንታዊ ፡ አርበኞችን ፡ ታሪክ ፡ ማንበቡንና ፡ አውሬ ፡ ማደኑን ፤ በርሻና ፡ በሥራ ፡ ላይ ፡ ጊዜውን ፡ ማሳለፉን ፡ አልተወም ፡ ነበር ።

ይልቁንም ፡ በጕልምስናው ፡ ጊዜ ፡ ከነብሩ ፡ ጋራ ፡ የታገለው ትዝ ፡ እያለው ፡ እኔ ፡ በገዛ ፡ እጄ ፡ ቈስቍሼ ፡ ጋሻዬን ፡ ከክንዴ ፡ ላይ ፡ አስነጠቅሁ ። ወይኔ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ተደፈርኹ ፡ ከመሣሪያዬ ፡ ሁሉ ፡ ከእጄ ፡ ላይ ፡ ቀርታ ፡ ጠላቴን ፡ ያጠቃችልኝ ፡ ጩቤዬ ፡ ብቻናት ፤ ጦሬም ፡ ተወርውራ ፡ ከጠላቴ ፡ ሽንጥ ፡ ላይ ፡ ቆማ ፡ ቀረች ፡ እያለ ፡ የልክና ፡ ያርበኝነት ፡ ጸጸት ፡ ይሰማው ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ሁለት ፡ ወንዶች ፡ ልጆቹ ፡ ዐቅመ ፡ አዳም ፡ ስላደረሱ ፡ ዘወትር ፡ ልጆቹ ፡ ለሰው ፡ የዕድሜውን ፡ መጨረሻ ፡ የሚያሳምረው ፡ ስላገሩ ፡ በጦር ፡ሜዳ ፡ ላይ ፡ ከጠላት ፡ ጋራ ፡ ሲታገል ፡ በመሬቱ ፡ ላይ ፡ የወደቀ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እያለ ፡ ያሳስባቸው ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ሚስቱን ፡ ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳን ፡ ያለልክ ፡ ስለ ፡ ወደዳት ፡ እንደ ፡ ዐይን ፡ ብሌንና ፡ እንደሚሰበር ፡ ብርጭቆ ፡ ይሣሣላት ፡ ነበር ።

በውነትም ፡ ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ በውበቷና ፡ በደም ፡ ግባቷ ይልቁንም ፡ በመልካም ፡ ጠባይዋ ፡ ደስ ፡ የምታሰኝ ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ የሚሣሡላት ፡ ነበረች ። ልጃቸውም ፡ ተዋበች ፡ በመልኳም ፡ በመኋም ፡ እናቷን ፡ ስለ ፡ መሰለች ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከልጆቹ ፡ ሁሉ ፡ አብልጦ ፡ ለሷ ፡ ያስብ ፡ ነበር ።

ምዕራፍ ፡ ፪ ።

ባ፲፱፻፳፫ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ ጥቅምት ፡ ፩ ፡ ቀን ፡ አቶ ፡ አስጨናቂ ፡ የሚባል ፡ ያቶ ፡ ተማቹ ፡ ወዳጅ ፡ ካዲስ ፡ አበባ ፡ መጥቶ በር ፡ መታ ።

አቶ ፡ ተማቹም ፡ ተነሥቶ ፡ በር ፡ ከፍቶ ፡ አስገባውና ፡ ወንድሜ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ሰነበትኽ ፡ ከወዴት ፡ መጣኽ ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ አላየሁኽም ።

አቶ ፡ አስጨናቂ ፤ አሁን ፡ ገና ፡ ካዲስ ፡ አበባ ፡ መጣሁ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ብርጩማ ፡ አመጣለትና ፡ ተቀመጥ ፡ ወንድሜ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ያየኸውንና ፡ የሰማኸውን ፡ ወሬ ፡ አጫውተኝ ።

አቶ ፡ አስጨናቂ ፤ ምኑን ፡ እቀመጣለሁ ፡ ምንስ ፡ አጫውትኻለሁ ፡ ዓለም ፡ ስታልፍ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ዓለም ፡ ለማነው ፡ የምታልፈው ፡ እባክኽ ፡ ይህን ፡ የሚገርም ፡ ነገር ፡ ተቀምጠን ፡ እንጫወት ፡ ብሎ ፡ ሁለቱም ፡ ከብርጩማ ፡ ላይ ፡ ተቀመጡ ።

አቶ ፡ አስጨናቂ ፤ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ ትላንት ፡ ማለዳ ፡ ካዲስ ፡ አበባ ፡ ተነሥቼ ፡ እንሆ ፡ በቀጥታ ፡ ወዳንተ ፡ መጣሁ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ተሸብሯል ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ከዐቅመ ፡ አዳም ፡ ከደረሰ ፡ ብረትና ፡ ጥይት ፡ ይቀበላል ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ምክንያቱ ፡ ምንድነው ፡ ብሎ ፡ ከብርጩማው ፡ ላይ ፡ ብድግ ፡ አለ ።

አቶ ፡ አስጨናቂ ፤ እባክኽ ፡ ወንድሜ ፡ አትቸኵል ፡ አትቄጣ ፡ በትዕግሥት ፡ ስማኝ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ እሺ ፡ በትዕግሥት ፡ እሰማኻለሁ ፡ ብሎ ፡ ተቀመጠ ።

አቶ ፡ አስጨናቂ ፤ የዘር ፡ ጠላታችን ፡ ጣሊያን ፡ ፋሺስት ፡ በሐማሴን ፡ በመቃዲሾ ፡ በሉክ ፡ በኩል ፡ ኢትዮጵያን ፡ ለመውረር ፡ ጦር ፡ አከማችቷል ፡ ይባላል ።

የዓለምም ፡ መንግሥታት ፡ ኢትዮጵያን ፡ መውረር ፡ ከሕግ ፡ መውጣትና ፡ የተዋዋልነውን ፡ ውል ፡ መጣስ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ቢያስታውቁት ፡ የፋሺሽቶች ፡ መሪ ፡ ሙሶሊኒ ፡ በግልጽ ፡ ለዓለም ፡ ሁሉ ፡ የፋሺስትን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መንግሥት ፡ እስክናረጋግጥ ፡ ድረስ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ መራመድ ፡ ያስፈልገናል ፤ የጣሊያንን ፡ መስፋፋት ፡ ጉዳይ ፡ ማንም ፡ በለሥልጣን ፡ ሊከለክለን ፡ አይችልም ፤ ምክንያቱም ፡ መልካም ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በጣም ፡ አስቸኳይ ፡ ነው ።

ጣሊያን ፡ ብርቱ ፡ ሠራተኛ ፡ መንግሥት ፡ ስለ ፡ ሆነችና ፡ ፋብሪካዋ ፡ እያደገ ፡ ስለ ፡ ሄደ ፡ ከመሬት ፡ የሚገኙ ፡ የመገጠሚያ ፡ ሀብቶች ፡ በጣም ፡ ያስፈልጓታል ። ይልቁንም ፡ አንድ ፡ መውጫ ፡ በር ፡ ለሕዝቧ ፡ መተናፈሻ ፡ ማግኘት ፡ ዋና ፡ ጉዳይዋ ፡ ነው ፡ የሚል ፡ የእብሪትና ፡ ያጥቂነት ፡ ቃል ፡ ተናገረ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥታችን ፡ ምን ፡ ብለው ፡ መለሱለት ።

አቶ፡ አስጨናቂ ፤ ንጉሠ ፡ ነገሥታችንማ ፡ በዓለም ፡ መን ሥታት ፡ ጕሮ ፡ እንዲደርስና ፡ ሕዝባቸውም ፡ እንዲያውቀው ፡ እን ዲህ ፡ በለው ፡ ፍርድን ፡ የተመረኰዘ ፡ ቊርጥ ፡ ቃል ፡ ተናገሩ ።

የዓለም ፡ ነገሥታትና ፡ እኛም ፡ ስለ ፡ ሰላም ፡ ስንል ፡ የደከ ምነው ፡ ከንቱ ፡ ሆኖ ፡ ከቀረ ፡ የሰይጣን ፡ ኀይል ፡ ይኸንን ፡ ምክ ንያት ፡ አድርጎ ፡ ጦርን ፡ ለማስነሣት ፡ መከራን ፡ ለመዝራት ፡ ዕፍ ረትንና ፡ ችግርን ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ እንዲነግሡ ፡ ከደረገ ፤ ከብዙ ፡ መቶ ፡ ዘመን ፡ ጕምሮ ፡ የጦርና ፡ የድፍረት ፡ ዋጋ ፡ ያላቸውን ፡ በብዙ ፡ ሺሕ ፡ የሚቈጠሩ ፡ አርበኞቿን ፡ ይዛ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥ ቷን ፡ በላይ ፡ መሪ ፡ አድርጋ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ትነሣለች ። የእግዚ አብሔርን ፡ ከንድ ፡ ተደግፋ ፡ መለኮት ፡ በቸርነቱ ፡ ምሽግ ፡ አድ ርጎ ፡ ከሰጣት ፡ ተራራዋና ፡ በረሓዋ ፡ ላይ ፡ ሆና ፡ ትዋጋለች ፡ የሚል ፡ ነው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ያሳድጋቸው ፡ እንዴት ፡ አንገቴን ፡ አራ ሱኝ ፡ ከዚህ ፡ በኋላስ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ሆን ።

አቶ ፤ አስጨናቂ ፤ ከዚህ ፡ በኋላማ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ባንድነት ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ጠብታ ፡ ድረስ ፡ ደማችንን ፡ ላገራችንና ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥታችን ፡ ክብር ፡ እናፈሳለን ፡ ብሎ ፡ በደ ስታ ፡ ተነሣ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ዕሠይ ፡ ያገሬ ፡ ልጅ ፡ እባክኽ ፡ ወንድሜ ፡ ጦሩ ፡ ጨርሶ ፡ ከቷልን ።

አቶ ፡ አስጨናቂ ፤ ምን ፡ ትናገራለኽ ፡ በሙሉ ፡ ጦሩን ፡ ከቶ ፡ ወደ ፡ ጦር ፡ ግንባር ፡ ተጕዟል ።

አሁን ፡ እኔ ፡ ስነሣ ፡ የወለጋና ፡ የይሉባቦር ፡ ጦር ፡ ብቻ ፡ አዲስ ፡ ዓለም ፡ ላይ ፡ ሰፍሯል ፡ ይባል ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ዕሠይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይክበር ፡ ይመስገን ፡ እኔም ፡ ከይሉባቦር ፡ ጦር ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ ግንባር ፡ እኼዳለሁ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ፊታውራሪ ፡ ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴ ፡ የሚባለው ፡ የጦር ፡ አለቃ ፡ የቅርብ ፡ ዘመዴ ፡ ነው ፡ የቀሩትንም ፡ የይሉባቦር ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ ዐውቃቸዋለሁ ፡ ከማውቃቸውም ፡ ሰዎች ፡ ጋራ ፡ የክብር ፡ ሞት ፡ መሞት ፡ ትልቅ ፡ ዕድል ፡ ነው ፤ ከልጅነቴ ፡ ስመ ኘው ፡ የነበረውን ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ መሞትን ፡ ላገኘው ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ወዳጇ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ወዳጇ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ እያለ ፡ ተጣራ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳም ፡ ምነው ፡ ወዳጄ ፡ ያለወትሮኽ ፡ በእንደ ዚህ ፡ ያለ ፡ ችኰላ ፡ ትጠራኛለኽ ፡ አለችው ።

በዚያ ፡ ጊዜ አቶ ፡ አስጨናቂ ፡ ካቶ ፡ ተማቹ ፡ ተሰናብቶ ፡ ወጣ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ በሩን ፡ ዘግቶ ፡ አዎን ፡ ወዳጄ ፡ ቸኵያለሁ ፡ ወደ ፡ ሠርግ ፡ ቤት ፡ ለመሄድ እጣደፋለሁ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ በጣም ፡ ደነገጠች ፡ ፊቷም ፡ ደም፡ መሰለ ። ቀልድ ፡ ነው ፡ እንዳትል ፡ የባሏ ፡ ፊት ፡ ጠቍር ፡ የሲ ቃና ፡ የጋለ ፡ መንፈስ ፡ ይታይበታል ። የውነት ፡ ነው ፡ እንዳትል ፡ እሷን ፤ ትቶ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ሙሽራ ፡ እንደማይሄድ ፡ ታውቃለች ።

ስለዚህ ፡ ስትፈራ ፡ ስትቸር ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ እኔን ፡ ትተህ፡ ሌላ ፡ ሴት ፡ ልታገባ ፡ ነውን ።

አቶ ፡ ተማቹም ፡ ሚስቱን ፡ አቅፎ ፡ እየሳመ ፡ ወዳጄ ፡ ጽጌ፡ ረዳ ፡ አንቺን ፡ ትቼ ፡ ማነን ፡ ላገባ ፡ ነው ፡ ይኽን ፡ ያሰብሽ ፤ ወደ ፡ ሠርግ ፡ ቤት ፡ እሄዳለሁ ፡ ያልኩት ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ፡ ስላገሬ ፡ ከጦር ፡ ግንባር ፡ ለመሄድ ፡ ስለ ፡ ቈረጥኩ ፡ ነው ።

ምክንያቱም ፡ ኢትዮጵያን ፡ የዘር ፡ ጠላታችን ፡ ፋሺስት ፡ ሊወራት ፡ ነው ፡ የሚሉ ፡ ሰማሁ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፤ ይኽን ፡ ነገር ፡ ከወዴት ፡ ሰማኽ ፡ እው ነት ፡ አይደለም ፡ አትበሳጭ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ርግጥ ፡ የታመነ ፡ ወሬ ፡ ነው ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፤ ከማን ፡ ሰማኽ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ርግጥ ፡ ነው ፡ የታመነ ፡ ወዳጄ ፡ አቶ ፡ አስ ጨናቂ ፡ ከዚያው ፡ ካዲስ ፡ አበባ ፡ በገሮው ፡ የሰማውን ፡ ባይኑ፡ ያየውን ፡ ነው ፡ የነገረኝ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፤ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ አቶ ፡ አስጨናቂ ፡ ዘወትር ፡ የሚያስጨንቅ ፡ ነገር ፡ ሲናገር ፡ እሰማለሁና ፡ አትመነው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ እርግጥ ፡ ነው ፡ አትጠራጠሪ ፡ እኔንም ፡ አታውኪኝ ፡ ይልቁንስ ፡ ቶሎ ፡ ብለሽ ፡ ሥንቄን ፡ አደራጂልኝ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ዕንባዋ ፡ እንደ ፡ ጐርፍ ፡ በፊቷ ፡ ላይ ፡ እየፈሰሰ ፡ ወዳጄ ፡ ወንድሜ ፡ እባክኽ ፡ እውነትም ፡ ቢሆን፡ ስለኔና ፡ ስለ ፡ ልጆችኽ ፡ ስትል ፡ ቅርልን ፡ የኔ ፡ ደስታ ፡ እኔን ፡ ደካማ ፡ ወዳጅኽን ፡ ለማን ፡ ጥለኽ ፡ ትሄዳለኽ ፡ እያለች ፡ ከግሩ ፡ ላይ ፡ ወደቀች ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ወዳጄ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ተነሽ ፡ ጊዜዬን ፡ በከንቱ ፡ አታጥፊብኝ ፡ ካንቺ ፡ ጋራ ፡ ደስታ ፡ ከልጆቹ ፡ ጋራ ፡ ፍቅር ፡ ቤት ፡ ንብረት ፡ ከነፃነት ፡ ጋራ ፡ የተያያዙ ፡ ነገሮች ፡ ናቸው ፤ ነፃነት ፡ ከሌለ ፡ ቤትና ፡ ደስታ ፡ የሉም ።

ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ ማናኛውንም ፡ ደስታና ፡ ክብር ፡ ቢሆን ፡ ላንቺና፡ ለልጆቹ ፡ እንደምለውጠው ፡ ታውቂያለሽ ።

ላገሬ ፡ ግን ፡ ሁላችሁም ፡ ምንም ፡ አይደላችሁ ፡ ሚስት ፡ ብት ሞት ፡ ሚስት ፡ ትተካለች ፤ ልጅ ፡ ቢሞት ፡ ልጅ ፡ ይተካል ። አገር ፡ ከሞተች ፡ ወዲያ ፡ ግን ፡ መተኪያ ፡ የላትም ፡ ይልቅስ ፡ ተነሽና፡ ሥንቄን ፡ አሰናጂልኝ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ እያለቀሰች ፡ ወደ ፡ ጓዳ ፡ ገባች ።

አራቱም ፡ ልጆቹ ፡ ያባትና ፡ የናታቸውን ፡ ልቅሶና ፡ መታ ወክ ፡ ስለ ፡ ሰሙ ፡ ምን ፡ ነገር ፡ አገኛቸው ፡ በማለት ፡ ደንግጠው ፡ እየሮጡ ፡ ወዳባታቸው ፡ ዘንድ ፡ ገቡ ።

ወዲያው ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፤ ታላቁን ፡ ልጁን ፡ ክንዴ ፡ እንግ ዴህ ፡ እንደ ፡ ነብሩ ፡ ጊዜ ፡ ብቻዬን ፡ ከጠላቴ ፡ ጋራ ፡ አልታገልም፡ ብወድቅም ፡ ታነሣኛለህ ፡ ብትወድቅም ፡ አነሣኻለሁ ። ልጄ ፡ ሆይ ፡ ወደ ፡ ጦር ፡ ሜዳ ፡ ልሄድ ፡ ነውና ፡ ተከተለኝ ።

ክንዴ ፤ አባባ ፤ በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ብቻ ፡ መሣሪያ ፡ የለኝ ምና ፡ ግዛልኝ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ መሣሪያ ፡ ከዚያው ፡ ታገኛለኽ ።

ወደ ፡ ሁለተኛው ፡ ልጁ ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ልጄ ፡ ጋሻው ፡ በዛ፡ እንግዴህ ፡ ስም ፡ ተሸካሚ ፡ ብቻ ፡ ሳትሆን ፡ ጋሻኽን ፡ ላገርኽ፡ መከት ፡ እኔና ፡ ወንድምኽም ፡ በወደቅን ፡ ጊዜ ፡ አንሣን ።

ልጄ ፡ ሆይ ፡ ጋሻኽን ፡ አንግተኽ ፡ ተከተለኝ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ የሚወዳት ፡ ልጁን ፡ ተዋበ ችን ፡ አታልቅሽ ፡ ይልቁንስ ፡ እናትሽን ፡ አጽናኛት ፡ አሽብርንም ፡ አሳድጊልኝ ፡ ብሎ ፡ ሲናገር ፡ አሽብር ፡ ሰምቶ ፡ አባባ ፡ ጠመንጃ፡ ግዛልኝና ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ልሂድ ፡ አለው ።

አቶ ፡ ተማቹም ፡ አሽብርን ፡ ታቅፎ ፡ እየሳመ ፡ የምወድኽ፡ ልጄ ፡ አንተስ ፡ የሚመጣውን ፡ ትውልድ ፡ መከራ ፡ ወደፊት ፡ ተጠባባቂ ፡ ነኽ ፡ ዛሬ ፡ የኛ ፡ ፈንታ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ዕንባው ፡ አቀረረ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በሁለተኛው ፡ ቀን ፡ ትንሽ ፡ በሶና ፡ ቋንጣ፡ ባህያው ፡ ጭኖ ፡ ጋሻና ፡ ጦሩን ፡ ይዞ ፡ ሰይፉን ፡ ታጥቆ ፡ ውኸ ግራውን ፡ ለትልቁ ፡ ልጁ ፡ ለክንዴ ፡ ሰጥቶ ፡ ልጄ ፡ ጋሻው ፡ በዛ፡ እንካ ፡ ይህችን ፡ ማለፊያ ፡ ዱላ ፡ ልብ ፡ ካለኽ ፡ ብዙ ፡ ሥራ ፡ ልትሠራባት ፡ ትችላለኽ ።

ሁላችሁም ፡ ይኸንን ፡ በጣም ፡ እንድትረዱት ፡ እወዳለሁ ። ድል ፡ የሚገኘው ፡ በመሣሪያ ፡ አይደለም ፡ በሃይማኖትና ፡ በምግ ባር ፡ መጠንከር ፡ ብቻ ፡ ነው ።

የሰው ፡ ልጅ ፡ ምግባሩ ፡ ሲወድቅ ፡ ዐሥሩ ፡ ሰው ፡ ሺውን ፡ ይማርከዋል ። በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ የወደቀው ፡ ሰው ፡ ትንሽ ፡ ሆኖ ፡ ሲታይ ፡ በፍርሀት ፡ የሚማረከው ፡ ሰውና ፡ መሣሪያ ፡ ከልክ፡ ያለፈ ፡ ሆኖ ፡ ይገኛል ።

አንዱ ፡ ባለመቻል ፡ የመመታቱ ፡ ቊስል ፡ ተሰምቶት ፡ ቶሎ፡ ባይወድቅ ፡ ባላጋራው ፡ ከሱ ፡ የበለጠ ፡ ቁስሎ ፡ ደክሞ ፡ ነበር ፤ ሰነፍ ፡ ሰው ፡ ጥቂት ፡ ባለመቻሉ ፡ ምግባሩ ፡ በመውደቁ ፡ በመኸ በሩ ፡ ሊወድቅ ፡ ጥቂት ፡ የቀረውን ፡ ጠላቱን ፡ ባወዳደቁ ፡ ያበረታዋል።

ስለዚህ ፡ ልጆቼ ፡ ሆይ ፡ በርትታችሁ ፡ እንድትታገሉ ፡ ጠላ ታችሁም ፡ እንደናንተ ፡ ድካም ፡ ተሰምቶታል ፤ እንግዴህ ፡ ግራና፡ ቀኝ ፡ ሆናችሁ ፡ ተከተሉኝ ፡ እንሂድ ፡ አላቸው ።

ጽጌ ፡ ረዳ ፡ አታልቅሽ ፡ እግዚአብሔር ፡ ደኅና ፡ ያገናኘን ፡ ብቻ ፡ አጥብቀሽ ፡ የምታዝኚልኝ ፡ በብርቱ ፡ ቁስዬ ፡ በጠላት ፡ እጅ፡ እንዳልወድቅ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ በጠላት ፡ እጅ ፡ መታከምና ፡ በጠላት፡ ቢላዋ ፡ መቀደድ ፡ እግዚአብሔር ፡ አይጣል ።

እንግዴህ ፡ ደኅና ፡ ሁኚ ፤ ተጽናኚ ፡ ብሎ ፡ ሳማት ፤ ወዲያው ፡ ትንሹን ፡ ልጁን ፡ አሸብርን ፡ ብድግ ፡ አድርጎ ፡ ከንገቱ ፡ ላይ ፡ አቅፎ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ዕድልኽ ፡ ምን ፡ ይሆን ፡ ብሎ ፡ ሳመውና ፡ አለቀሰ ።

አሸብርም ፡ አባባ ፡ ስትመለስ ፡ ሱኳር ፡ ይዘኽልኝ ፡ እንድት መጣ ፡ አለው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ባሁኑ ፡ ጊዜ ፡ ባንተ ፡ ዕድሜ ፡ ላይ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ምን ፡ ፈቀረኝ ፡ ኑ ፡ ልጆቼ ፡ እንሂድ ፡ ሥንቃችንን ፡ አስ ቀድሙ ፡ እንግዴህ ፡ እንደ ፡ ሎጥ ፡ ሚስት ፡ የታሪክ ፡ ዓምድ ፡ እንዳንሆን ፡ ፊታችንን ፡ ወደ ፡ ቤታችን ፡ አዙረን ፡ አንመልከት፡ ብሎ ፡ ልጆቹን ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ አድርጎ ፡ አህያውን ፡ አስቀድሞ ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ ተጓዘ ።

## ምዕራፍ ፡ ፫ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ፡ ረዳና ፡ ተዋበች ፡ አሸብርን ፡ አስከትለው ፡ በሩቁ ፡ እያለቀሱ ፡ በሬሳ ፡ አፋፍ ፡ ላይ ፡ ቆመው ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ተማቹና ፡ ልጆቹ ፡ ወደ ፡ ኋላቸው ፡ ዘወር ፡ ብለው ፡ ሳያዩ ፡ ባንጐለላ ፡ ሜዳ ፡ ሲኄዙ ፡ ጥቂት ፡ በጥቂት ፡ ላይን ፡ እየ ራቁ ተሰወሩ ።



አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከሁለቱ ፡ ልጆቹ ፡ ጋራ ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ሲኄዱ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ካዲስ ፡ አበባ ፡ ከተማ ፡ ገብተው ፡ የዩሉባቦርን ፡ ጦር ፡ ሠራዊት ፡ ወሬ ፡ ቢጠይቅ ፡ ዛሬ ፡ ሆለታ ፡ ላይ ፡ ሰፍሯል ፡ ተነገ ፡ ወዲያ ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ፊት ፡ በሰልፍ ፡ ሊያልፍ ፡ ነው ፡ እየተባለ ፡ ይወራል ፡ አሉት ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ኄዙን ፡ እከተማ ፡ ከዘመድ ፡ ቤት ፡ ትቶ ፡ ልጆ ቹን ፡ አስከትሎ ፡ ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴን ፡ ለመፈለግ ፡ ወደ ፡ ሆለታ ፡ ወረደ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ሰፈሩን ፡ በመጠየቅ ፡ ብዙ ፡ ከደከመ ፡ በኋላ ፡ ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴን ፡ አገኘው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ጌታዬ ፡ ወንድሜ ፡ በዓለም ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ ዘመድ ፡ ነው ፡ ነገር ፡ ግን ፡ እውነተኛው ፡ ዘመድ ፡ በክፉ ፡ ቀን ፡ ነው ፡ የሚታወቅ ፡ ስለዚህ ፡ ካንተ ፡ ከወንድሜ ፡ ጋራ ፡ ስላገሬ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ለመውደቅ ፡ መጣሁ ።

ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴ ፡ ብድግ ፡ ብሎ ፡ ስሞ ፡ ወንድሜ ፡ ተማቹ ፡ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ለመሞት ፡ በመምጣትኽ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ አለኝ ፡ ምግባርኽንና ፡ ጽኑ ፡ ሃይማኖትኽን ፡ ዐውቀዋለሁ ፤ እግ ዚአብሔር ፡ ነው ፡ ያመጣልኝ ።

በምንቅም ፡ ምንም ፡ አታስብ ፡ ከኔው ፡ ጋራ ፡ ተካፍለን ፡ እንበላለን ፡ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ እነዚህ ፡ ሁለቱ ፡ ወጣቶች ፡ ያንተ ፡ ልጆች ፡ ናቸውን ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ አዎን ፡ የኔ ፡ ልጆች ፡ ናቸው ፡ አንድ ፡ ከመሆን ፡ ሁለት ፡ ሦስት ፡ መሆን ፡ ይሻላል ፡ ብዬ ፡ እነሆ ፡ ሁለቱን ፡ ልጆቼን ፡ ግራና ፡ ቀኝ ምርኵዝ ፡ አድርጌ ፡ መጥ ቻለሁ ።

ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴ ፤ ምነው ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡ ሠራኽ ፡ በይሆን ፡ እንኳ ፡ ትንሹን ፡ ልጅኽን ፡ ለዘር ፡ እንዲ ተርፍ ፡ አትተወውም ፡ ኖሯልን ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ጌታዬ ፡ ሆይ ፡ መሬት ፡ ሲገኝ ፡ አልነበ ረምን ፡ ዘርን ፡ ማትረፍ ፡ የሚያስፈልገው ፡ ዘር ፡ የሚመትርና ፡ መሬት ፡ የሚወስድ ፡ ጠላት ፡ ሲመጣ ፡ ዘርን ፡ በጨርቅ ፡ ቋጥሮ ፡ ከጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ መዝራት ፡ የተሻለ ፡ ነው ።

ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴ ፤ ርግጥ ፡ አንተ ፡ እንዳልከው ፡ ነው ። እኔም ፡ ራሴ ፡ እንኳ ፡ ባልሠራውም ፡ ለዘመድ ፡ ለወ ዳጅ ፡ መምከር ፡ ይገባል ፡ በማለት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሁለቱን ፡ ወንዶች ፡ ልጆቼን ፡ ይዤ ፡ መጥቻለሁ ፡ አሁንስ ፡ እንግዴህ ፡ በቶሎ ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ ሄደኽ ፡ አንተም ፡ ልጆችኽም ፡ ካኪ ፡ ገዝታችሁ ፡ ልበሱ ፡ ዋናው ፡ የኛ ፡ የጦር ፡ ጠቅላያችን ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ ነጭ ፡ ልብስ ፡ እንዳይለብስ ፡ ጥብቅ ፡ ትእዛዝ ፡ አሳል ፏል ፡ እንካ ፡ ለካኪ ፡ መግዣ ፡ ሁለት ፡ መቶ ፡ ብር ፡ ብሎ ፡ ሰጠው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ጌታዬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይስጥልኝ ፡ እኔም ፡ በጕልበቴ ፡ ብድርኽን ፡ እከፍላለሁ ፡ እንግዴህ ፡ ልብሴን ፡ አሰ ፍቼ ፡ የት ፡ ድረስ ፡ ልጠብቅ ።

ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴ ፡ ተነገ ፡ ወዲያ ፡ ጉለሌ ፡ ጴጥ ሮስ ፡ ወጳውሎስ ፡ ድረስ ፡ ከልጆችህ ፡ ጋራ ፡ እንድትመጣ ፡ የኔም ፡ ሰልፍ ፡ ከጐንደሬዎች ፡ አለቃ ፡ ከፊታውራሪ ፡ ከበደ ፡ ዘውዴ ፡ ቀጥሎ ፡ ነው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ የጦር ፡ ልብሱን ፡ ለማሰፋት ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ ተመልሰ ።

በሁለተኛው ፡ ቀን ፡ አቶ ፡ ተማቹና ፡ ልጆቹ ፡ ካኪያቸውን ፡ ለብሰው ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ጋሻና ፡ ጦሩን ፡ ይዘ ፤ ክንዴም ፡ ውዥግፉውን ፡ ተሸክሞ ፤ ጋሻው ፡ በዛም ፡ ዱላውን ፡ ተመር ኰዘ ፡ ጉለሌ ፡ ሲጠባበቁ ፡ የይሉባቦር ፡ ጦር ፡ ከወደ ፡ ምዕራብ ፡ ነጋሪቱን ፡ እያልጐሸመ ፡ ደራሽ ፡ ውሃ ፡ መስሎ ፡ ብቅ ፡ አለ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ጥቀርሻ ፡ የመሰለ ፡ ጦር ፡ መንገዱን ፡ ይዘ ፡ ነጋሪቱ ፡ ገብር ፡ ገብር ፡ እያለ ፡ ተጅመል ምሎ ፡ ሲያልፍ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ልቡ ፡ በደስታና ፡ በወኒ ፡ ተመ ልቶ ፡ ይሸልል ፡ ዠመር ። ወደ ፡ ጐን ፡ ቆሞ ፡ ጦሩ ፡ ሲያልፍ ፡ ፊታውራሪ ፡ ኀይለ ፡ ማርያምን ፡ ይመለከትና ፡ ይፈልግ ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ የጐንደሬ ፡ ጦር ፡ ብዙ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ አንድ ፡ ሩብ ፡ ሰዓት ፡ ያኽል ፡ እንደ ፡ ጠበቀ ፡ ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴ ፡ ካኪውን ፡ ለብሶ ፡ ዕጥፍ ፡ ዝናሩን ፡ ታጥቆ ፡ ሴጣ ፡ ያንበሳ ፡ ቈዳ ፡ ለምድ ፡ ደርቦ ፡ ሁለት ፡ ጦሮች ፡ በግራ ፡ እጁ ፡ ይዘ ፡ በቦራ ፡ ፈረስ ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ጦሩን ፡ ሂዱ ፡ ሂዱ ፡ እያለ ፡ ሲመራ ፡ ብቅ ፡ አለ ። በውነትም ፡ የፈረሱን ፡ ንቃት ፡ የኀይለ ፡ ማርያምን ፡ አኳኋን ፡ ያየ ፡ ሰው ፡ አሁኑኑ ፡ ከጠላት ፡ ጋራ ፡ የሚገጥም ፡ ይመስል ፡ ነበር ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ እንዴት ፡ ያለሁ ፡ ዕድለኛ ፡ ሰው ፡ ነኝ ፡ ከዚህ ፡ አንበሳ ፡ ከሚመስል ፡ አርበኛ ፡ ጋራ ፡ ስላገሬ ፡ ከጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ለመውደቅ ፡ የተዘጋጀሁ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴ ፡ ተጠግቶ ፡ እጅ ፡ ነሥቶ ፡ አብሮ ፡ ይጓዝ ፡ ዠመር ። ጦሩ ፡ በጉለሌ ፡ በኩል ፡ ከደጃዝማች ፡ ይገዙ ፡ ቤት ፡ አጠገብ ፡ ሲደርስ ፡ የከተማው ፡ ሕዝብ ፡ ወንዱም ፡ ሴቱም ፡ ሽማግሌውም ፡ ወጥተው ፡ ይመለከቱ ፡ ነበር ። የጦሩን ፡ ንቃትና ፡ የልብሱን ፡ ጥቀርሻ ፡ መምሰል ፡ የነጋሪቱን ፡ ድምፅና ፡ ስልት ፡ የፉከራውንና ፡ የሽለላውን ፡ አኳኋን ፡ በማየትና ፡ በመ ስማት ፡ የሕዝቡ ፡ ልብ ፡ ተነክቶ ፡ ግማሹ ፡ ያለቅስ ፡ ነበር ፤ ግማሹም ፡ እልል ፡ ይል ፡ ነበር ።

አንዳንዱም ፡ ዱሮ ፡ ወታደር ፡ የነበሩት ፡ ሽማግሌዎች ፡ ይፎክሩ ፡ ነበር ። ጦሩም ፡ እንደ ፡ ውሃ ፡ ሙላት ፡ መንገዱን ፡ ይዞ ፡ ከኀይለ ፡ ሥላሴ ፡ አደባባይ ፡ ሲደርስ ፡ ሴቱም ፡ ወንዱም ፡ ሽማግሌውም ፡ ባልቴቱም ፡ በከተማ ፡ የሚኖሩ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎችም ፡ ልጆቻቸውን ፡ እየተሸከሙ ፡ በመንገዱ ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ በየቤቱ ፡ ፎቅም ፡ ላይ ፡ እየተንጠለጠሉ ፡ ያዩ ፡ ነበር ፤ ብዙዎችም ፡ ያለቅሱ ፡ ነበር ።

ሌሎቹም ፡ እግዚአብሔር ፡ ድሉን ፡ ለናንተ ፡ ሰጥቶ ፡ በደኅና ፡ ይመልሳችሁ ፡ እያሉ ፡ ይመርቁ ፡ ነበር ። አንዳንድ ፡ ሴቶችም ፡ እልል ፡ ይሉ ፡ ነበር ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ለሚስቱ ፡ ለጽጌ ፡ ወደ ፡ ጦር ፡ ሜዳ ፡ ልሄድ ፡ ነው ፡ ሲላት ፡ ያለቀሰችው ፡ መራራ ፡ ልቅሶዋ ፡ ትዝ ፡ ብሎት ፡ በውነት ፡ በድል ፡ አድራጊነት ፡ ተመልሰን ፡ ወዳጄ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ በእልልታ ፡ ትቀበለኝ ፡ ይሆን ፤ ወይስ ፡ እኔ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ወድቄ ፡ ስቀር ፡ ልጆቼ ፡ ችጋረኛ ፡ መጻተኛ ፡ ሚስቴ ፡ ጋለሞታ ፡ ይሆኑ ፡ ይሆን ፡ ብሎ ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ የሚያቃጥል ፡ ዕንባ ፡ ሳያስበው ፡ ካይኑ ፡ ፈሰሰ ።

ጀግና ፡ የይሉባቦር ፡ ጦር ፡ በትልቁ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ዋና ፡ በር ፡ ገብቶ ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ፊት ፡ ሲፎክር ፡ ዋናው ፡ የጦር ፡ ጠቅላይ ፡ አራት ፡ ኪሎ ፡ ደርሶ ፡ ነበር ። የጦሩ ፡ ደጀን ፡ ግን ፡ ገና ፡ ካራዳ ፡ ቅዱስ ፡ ጊዮርጊስ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አጠገብ ፡ ደርሶ ፡ ሳያቋርጥ ፡ ይጓዝ ፡ ነበር ።

የጦሩን ፡ ንቃትና ፡ የነጋሪቱን ፡ ድምፅ ፡ የወታደሩን ፡ ሽለላና ፡ ፉከራ ፡ መስማትና ፡ ማየት ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ደስ ፡ ያሰኝ ፡ ነበር ።

ከጥቂት ፡ ጊዜ ፡ በኋላ ፡ ዋናው ፡ የጦር ፡ ጠቅላይ ፡ ከንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ፊት ፡ ቆሞ ፡ የጦር ፡ ዲስኩር ፡ አደረገ ።

ከረዥሙ ፡ ዲስኩር ፡ መጨረሻ ፡ ከሦስት ፡ ሺሕ ፡ ዓመት ፡ ያሚበልጥ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መንግሥቱን ፡ ክብር ፡ ጠብቃ ፡ ከአጥቂ ፡ ጠላቷ ፡ ጋራ ፡ እየተከራከረች ፡ ነጻነቷን ፡ ሃይማኖቷን ፡ ልምዷን ፡ አክብራ ፡ የምትኖረውን ፡ ኢትዮጵያን ፡ ከዚህ ፡ ቀደም ፡ በደም ፡ ቀለም ፡ በዓለም ፡ ታሪክ ፡ ውስጥ ፡ አጽፈን ፡ የመታነው ፡ የዘር ፡ ጠላታችን ፡ ኢትዮጵያን ፡ ቅኝ ፡ አገር ፡ አደርጋለሁ ፡ ማለቱ ፡ በጣም ፡ ይገርማል ።

ትልቁ ፡ እስክንድር ፡ እንኳ ፡ ዓለምን ፡ ሲወር ፡ የኢትዮጵያን ፡ ተራራና ፡ በረሓ ፡ ለመውጣት ፡ አልደፈረም ። እንግዴህ ፡

ይኽንን ፡ የእብሪት ፡ ስድብ ፡ ከደም ፡ በስተቀር ፡ የሚያጥበው ፡ ነገር ፡ ስለሌለ ፡ በቶሎ ፡ ወደ ፡ ጠላት ፡ ግንባር ፡ እንሂድ ፡ ደም፡ ያለደም ፡ አይነጻም ፡ ተብሏል ፡ ብሎ ፡ ሲጨርስ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ሰይፉን ፡ መዞ ፡ እየፎከረ ፡ ወደ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ዙፋኑ ፡ አጠገብ ፡ ቀርቦ ፡ ዐይኑን ፡ አፍጦ ፡ እየተመለከተ ፡ እኔ ፡ ያንተ ፡ አሽከር ፡ ምንም ፡ ብነሳ ፡ የዶሮ ፡ ደም ፡ ያኽል ፡ ለእብሪተኛው ፡ ጠላቴ ፡ ስድብ ፡ ማጠቢያ ፡ ሳላፈስ ፡ አልቀርም ። የደም ፡ አንዲት ፡ ጠብታ ፡ እንኳ ፡ ዋጋ ፡ ያላት ፡ ነች ። እኛ ፡ አሽከሮችህ ፡ መሬት ፡ ሳንሆን ፡ የኢትዮጵያን ፡ መሬት፡ አንድ ፡ ጫማ ፡ እንኳ ፡ ጠላት ፡ አይወስድም ፡ እያለ ፡ ከብዙ ፡ አርበኞች ፡ ጋራ ፡ በጋለ ፡ መንፈስ ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ደረጃ፡ ድረስ ፡ እየወጡ፡ ሲፎክሩ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ አላቸው ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱ፡ ተመለሱ ።

የይሉባቦርም ፡ ጦር ፡ ተመልሶ ፡ ከዚያው ፡ ከሥጋ ፡ ሜዳ ፡ ሰፈረ ። በማግስቱ ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ በተለየ ፡ ለይሉባቦር ፡ ጦር ፡ ከዙፋናቸው ፡ ላይ፡ ተቀምጠው ፡ ትልቅ ፡ግብዣ ፡ አደረጉ ።

የምዕራብ ፡ ኢትዮጵያ ፡ የይሉባቦር ፡ አንበሶች ፡ ከምግቡ ፡ መካከል ፡ እየተነሡ ፡ መታመናቸውን ፡ በፉከራ ፡ ይገልጹ ፡ ዠመር ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ፊታውራሪ ፡ ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴ ፡ ብድግ፡ ብሎ ፡ ባለፈው ፡ ጊዜ ፡ የሠራውን ፡ የጀግንነት ፡ ሥራ ፡ እየቈጠረ፡ አሁንም ፡ እኛ ፡ ባሮችህ ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ጠብታ ፡ ደም፡ድረስ፡ ላገራችንና ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥታችን ፡ ክብር ፡ እናፈሳለን ፡ ብሎ ፡ ከፎከረ ፡ በኋላ ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ አሽከርህ፡ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴ፡አለ ።

ንጉሠ ፡ ነገሥቱም ፡ በደስታ ፡ መልክ ፡ ፍግግ ፡ ብለው ፡ ዐውቅኻለሁ ። አሁንም ፡ወደ ፡ ፊት ፡ እንደምትሠራ ፡ አምናለሁ ፡ አሉት።

በማግስቱ ፡ በንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ሰብሳቢነት ፡ ከፍ ፡ ያሉ፡መኳንንት ፡ መሳፍንት ፡ ሚኒስትሮች ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ ተሰብስበው፡ ስለ ፡ ጦሩ ፡ ፕላን ፡ (ንድፍ) ፡ ከሠሩ ፡ በኋላ ፡ የይሉባቦርን፡የጦር፡ ጠቅላይ፡ ሹምና ፡ የገሙ ፡ ጐፋን ፡ የጦር ፡ ጠቅላይ ፡ ሹም ፡ ግርማዊነታቸው ፡ የጀኔራል ፡ የጦር ፡ ልብስ ፡ ሸልመው ፡ በላይኛው፡ ቤተ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ቅጥር ፡ ውስጥ ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፤ ልዑል ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ፤ ልዑል ፡ መኰንን ፡ መስፍነ ፡ ሐረር ፡ ክቡር ፡ ራስ ፡ ብሩ ፡ ሆነው ፡ ፎቶ ፡ ግራፍ ፡ ተነሡ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ንጉሥ ፡ ነገሥቱ ፡ እኔም ፡ ከጦሩ ፡ መካ ከል ፡ እገኛለሁ ፡ ብለው ፡ ለሕዝባቸው ፡ ስላስታወቁ ፡ ኅዳር ፡ ፲፰ ፡ ቀን ፡ ፲፱፻፳፰ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ በዐዲግራት ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ገፋው ፡ ጦር ፡ ግንባር ፡ የክብር ፡ ዘበኞቻቸውን ፡ አስ ከትለው ፡ በደሴ ፡ በኩል ፡ ተጓዙ ። ከሦስት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡



ግርማዊነታቸው ፡ ሽልማት ፡ ከሰጡ ፡ በኋላ ።

የምዕራብ ፡ ኢትዮጵያ ፡ የይሉባቦር ፡ ጦር ፡ ወደ ፡ ውጋዴን ፡ የጦር ፡ ግንባር ፡ መሳፈር ፡ ጀመረ ። አራት ፡ ቀን ፡ ሙሉ ፡ በባቡር ፡ የጦር ፡ ሠራዊቱ ፡ ከተጓዘ ፡ በኋላ ፡ ባምስተኛው ፡ ቀን ፡ የጦሩ ፡ ጠቅላይ ፡ ሹም ፡ በልዩ ፡ ባቡር ፡ ለመሳፈር ፡ ወደ ፡ ባቡር ፡ መቆሚያ ፡ ወረደ ። ከተዘጋጀው ፡ ቫጎ ፡ ውስጥ ፡ ከመግባቱ ፡ በፊት ፡ የላጋሩ ፡ ሹም ፡ መጥቶ ፡ ከጠቅላዩ ፡ የጦር፤ አለቃ ፡ ጋራ ፡ እጅ ፡ ለጅ ፡ ተያይዘው ፡ ክቡር ፡ ሆይ ፡ በድል ፡ አድራጊነት ፡ እንዲመልስዎ ፡ እመኛለሁ ።

ናፖሊዎን ፡ ድል ፡ የሆነው ፡ ባንድ ፡ ጄኔራል ፡ ስሕተት ፡ ነው ። እንግዴህ ፡ የመድፍ ፡ ድምፅ ፡ በመስማት ፡ ደስ ፡ ይበላችሁ ፡ ብሎ ፡ ተሰናበተ ፤ ወዲያው ፡ የጦሩ ፡ ጠቅላይ ፡ ሹም ፡ ወደ ፡ ተዘጋጀለት ፡ ቫጎ ፡ ወጣ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከዘመዶቹ ፡ ከፊታውራሪ ፡ ኀይለ ፡ ማር
ያም ፡ ጣሴ ፡ ጋራ ፡ ለመሄድ ፡ ከጦሩ ፡ ተለይቶ ፡ ቀርቶ ፡ ነበ
ርና ፡ የላጋሩን ፡ ሹም ፡ ምክር ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ምክር ፡ ይህች፡
ናት ፡ ኑ ፡ ልጆቼ ፡ ከባቡሩ ፡ ላይ ፡ እንውጣ ፡ በመድፉ ፡
ድምፅ ደስ ፡ ይበለን ፡ ብሎ ፡ ሁለቱን ፡ ልጆቹን ፡ ይዞ ፡ ተሳፈረ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ምንም ፡ በቈራጥነት ፡ ስላገሩ ፡ በጦር ፡ ሜዳ፡
ላይ ፡ ለመውደቅ ፡ ቢመጣ ፡ በባቡሩ ፡ መስኮት ፡ ሲመለከት ፡
በየቤቱ ፡ ደጃፍ ፡ ባልና ፡ ሚስት ፡ ልጆቻቸውን ፡ ካጠገባቸው፡
አድርገው ፡ ሲጫወቱ ፡ ከብቶቻቸው ፡ በሜዳ ፡ ሲግጡ ፡ ዶሮዎ
ቻቸው ፡ በውጭ ፡ ፈሰው ፡ ሲለቅሙ ፡ እያየ ፡ ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡
ረዳን ፡ ልጆቹን ፡ ቤቱንና ፡ ንብረቱን ፡ እያሰበ ፡ ዕንባው ፡
ይፈስ ፡ ነበር ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሁለት ፡ ቀን ፡ በባቡር ፡ የጦር ፡ ጠቅላዩ ፡
ከተጓዘ ፡ ወዲያ ፡ ድሬ ፡ ዳዋ ፡ ላይ ፡ ከጦር ፡ ሠራዊቱ ፡ ጋራ ፡
ተገናኘ ። ጦሩ ፡ ብዙ ፡ ስለሆነ ፡ ከተማውን ፡ እንዳያውክ ፡ ወዲ
ያው ፡ ድሬ ፡ ዳዋን ፡ ለቆ ፡ ቀርሳ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ላይ ፡
ሰፈረ ። ሁለት ፡ ሳምንት ፡ ያህል ፡ ከቈየ ፤ በኋላ ፡ ቀርሳን ፡ ለቆ ፡
አቦከር ፡ ከቅዱስ ፡ ጊዮርጊስ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አጠገብ ፡
ሰፈረ ። ደግሞ ፡ ከሦስት ፡ ሳምንት ፡ በኋላ ፡ ጦሩ ፡ ካቦከር ፡
ተነሥቶ ፡ በሐረርጌ ፡ ከተማ ፡ መካከል ፡ ነጋሪቱን ፡ እያስጐሸመ፡
ወደ ፡ ጅጅጋ ፡ ተጓዘ ። ባምስተኛው ፡ ቀን ፡ ከጅጅጋ ፡ አጠገብ፡
ካራ ፡ መራ ፡ ከሚባለው ፡ ተራራ ፡ ሥር ፡ ሰፈረ ።

ከዚያም ፡ ላይ ፡ ከሁለት ፡ ወር ፡ የሚበልጥ ፡ የጦር ፡ ሠራ
ዊቱ ፡ ተቀመጠ ።

ነገር ፡ ግን ፡ የምዕራብ ፡ ኢትዮጵያ ፡ የይሉባቦር ፡ ጦር ፡
ብዙ ፡ ቀን ፡ ከዚያ ፡ በመቀመጡ ፡ በጣም ፡ አዘነ ። ምክንያቱም፡
ከምዕራብ ፡ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ የመጣነው ፡ ጠላትን ፡ ለማጥቃት፡
ነው ፡ እንጂ ፡ ከዚህ ፡ በከንቱ ፡ ለመቀመጥ፡አልነበረም ፡ በማለት፡ነው ።

ስለዚህ ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ ሁሉ ፡ ተሰብስበው ፡ ለዋናው ፡
የጦር ፡ ጠቅላይ ፡ ክቡር ፡ ሆይ ፡ ነገ ፡ በማለዳ ፡ ባ፲፩ ፡ ሰዓት ፡
ጦሩ ፡ ሁሉ ፡ ከቶ ፡ በሰልፍ ፡ ጂጅጋ ፡ ለመሄድ ፡ ቈርጧል ። ምክ
ንያቱም ፡ በከንቱ ፡ ከዚህ ፡ በመቀመጡ ፡ ጕዳት ፡ ስለሆነበት ፡
አዝኖ ፡ ነው ። አሁንም ፡ አንተ ፡ እየመራኸን ፡ ሄደን ፡ ለባለሥ
ጣኖቹ ፡ ወደ ፡ ጦር ፡ ግንባር ፡ በፍጥነት ፡ እንድንሄድ ፡ እን
ለምን ፡ አሉት ።

የጦሩ ፡ ጠቅላይ ፡ ሹም ፡ ደኅና ፡ አስባችኋል ፡ እኔው ፡ ይዤ ችሁ ፡ እኼዳለሁ ፡ በዚሁ ፡ ባ፲፩ ፡ ሰዓት ፡ ታጠቁ ፡ ብሎ ፡ አስታወቃቸው ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በተባለው ፡ ሰዓት ፡ ልክ ፡ ጦሩ ፡ ጥሩምባ ፡ አስነፍቶ ፡ ከሦስት ፡ ሺሕ ፡ የሚበልጥ ፡ ጦር ፡ በሰልፍ ፡ እዋናው ፡ የጦር ፡ ጠቅላይ ፡ ሰፈር ፡ ድረስ ፡ መጣ ።

የጦር ፡ ጠቅላዩም ፡ ታጥቆ ፡ ይጠብቅ ፡ ነበርና አጅበውት ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ተጓዙ ። የግንባሩ ፡ ጦር ከጅጅጋ ፡ ከተማ ፡ ሲደ ርስ ፡ የከተማው ፡ ኗሪና ፡ የጦር ፡ ሠራዊቱ ፡ ምን ፡ ጦር ፡ መጣ ብን ፡ በማለት ፡ ተደናገጡ ።

ጦሩ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ተሰለፈ ፡ ከዋናው ፡ ጦር ፡ አዛዥ ፡ ጽሕፈት ፡ ቤት ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ከሜዳው ፡ ላይ ፡ ተሰልፎ ፡ ቆመ ። ማለዳ ፡ ይህን ፡ ያኸል ፡ ጦር ፡ የተሰበሰበበትን ፡ ምክንያት ፡ ለማ ወቅ ፡ ዋናው ፡ የጦር ፡ አዛዥ ፡ አንድ ፡ የጦር ፡ መኰንን ፡ ቢልክ ፡ እኛ ፡ የምዕራብ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ጦር ፡ ነን ፡ ከዚህ ፡ የተሰ በሰብንበትም ፡ ምክንያት ፡ ለዋናው ፡ የጦር ፡ አዛዥ ፡ የምናመለክ ተው ፡ ጕዳይ ፡ ስላለን ፡ ነው ። አሁን ፡ የምንለምነው ፡ የጦሩ ፡ ዋና ፡ አዛዥ ከሹማምንቱ ፡ ጋራ ፡ ሆኖ ፡ እንዲቀበለን ፡ ነው ፡ ብለው ፡ አስታወቁ ።

መኰንኑም ፡ ተመልሶ ፡ ይህን ፡ ቃል ፡ ባስታወቀ ፡ ጊዜ ፡ ከጧቱ ፡ በ፪ ፡ ሰዓት ፡ ከጅጅጋ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ አስነጥፎ ፡ መኳንንቱን ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ አስቀምጦ ፡ ጄኔራል ፡ ወሂብ ፡ ፓሻ ፡ የሚባለው ፡ የጦር ፡ አማካሪ ፡ የአ ልባኒ ፡ የቱርክ ፡ ተወላጅ ፡ በዋናው ፡ የጦር ፡ አዛዥ ፡ ቀኝ ፡ ተቀምጦ ፡ የይሉባቦር ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ተጠራ ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ባለቃ ፡ ባለቃው ፡ እየተሰለፈ ፡ እየሸለለ እየ ፎከረ ፡ ያልፍ ፡ ዠመር ። ከሰልፉ ፡ መካከል ፡ ዐሥር ፡ የሚሆኑ ፡ የጦር ፡ መኰንኖች ፡ ጕዳዩን ፡ እንዲያመለክቱ የጦሩ ፡ ሠራዊት ፡ የመረጣቸው ፡ ድርብ ፡ ዝናራቸውን ፡ ታጥቀው ፡ ጠመንዣቸውን ፡ በደረታቸው ፡ አቅፈው ፡ እየፎከሩ ፡ ተጠግተው ፡ ክቡራን ፡ ጌቶ ቻችን ፡ ከኢትዮጵያ ፡ ምዕራብ ፡ ተጕዘን ፡ እምሥራቅ ፡ (ፀሐይ ፡ መውጫ) ፡ ውጋዴ ፡ የመጣነው ፡ ጠላትን ፡ ለማጥቃት ፡ ነበር ፡ አሁን ፡ ሕዝባችን ፡ በከንቱ ፡ በተቅማጥ ፡ በሽታ ፡ ርስ ፡ በርሱ ፡ እየተዋጋ ፡ ያልቃል ፤ ከጠላት ፡ ጋራ ፡ ብንጋጠም ፡ ጠላትን ፡

አጥቅተን ፡ ጠላትን ፡ ገድለን ፤ ጠላትም ፡ ገድሎን ፡ በመለዋወጥ ፡ እንጐዳዳ ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ ግን ፡ እኛ ፡ ብቻችንን ፡ ተጐዳን ፡ እባካችሁ ፤ ወደ ፡ ግንባር ፡ ስደዱን ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ መሣሪያ ፡ አታበላሹ ፡ ብሎ ፡ የጐንድሬዎች ፡ አለቃ ፡ ፊታውራሪ ፡ ከበደ ፡ ዘውዴ ፡ ሲናገር ፤ ፊታውራሪ ፡ ኃይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴ ፡ እየሮከረ ፡ ብቅ ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ ምንድነው ፡ ወደ ፡ ጦር ፡ ግንባር ፡ የማትሰዱን ፡ በተቅማጥ ፡ በሽታ ፡ የምታመነምኑን ፡ አሞራውስ ፡ ደኅና ፡ ሥጋ ፡ ቢበላ ፡ ምንቾገራችሁ ፡ ላገራችንና ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥታችን ፡ ክብር ፡ እንድንሞት ፡ ስደዱን ፡ እያለ ፡ ጮኾ ፡ እየሮከረ ፡ ተናገረ ።

ጄኔራል ፡ ወሂብ ፡ ፓሻ ፡ ዐይኑን ፡ ዕንባ ፡ ሞልቶት ፡ አላስችል ፡ ስላለው ፡ ብድግ ፡ ብሎ ፡ ከፊቱ ፡ ካለው ፡ ጠረቤዛ ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡ በአስተርጓሚ ፡ ስሙ ፡ እናንት ፡ የኢትዮጵያ ፡ አርበኞች ፡ ዛሬ ፡ ገና ፡ በታሪክ ፡ ያነበብኩትን ፡ የኢትዮጵያን ፡ ድምፅ ፡ ሰማሁ ። ምነው ፡ እግዚአብሔር ፡ ቢፈቅድልኝ ፡ ሞቴን ፡ ከናንተ ፡ ጋራ ፡ ባደረገው ፡ ብሎ ፡ ከጠረጴዛው ፡ ወርዶ ፡ አርበኞቹን ፡ እየዞረ ፡ ዐይናቸውን ፡ ይመለከት ፡ ነበር ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ዋናው ፡ የጦር ፡ አዛዥ ፡ ስላገራችሁና ፡ ስለ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥታችሁ ፡ ክብር ፡ አስባችሁ ፡ ወደ ፡ ጦሩ ፡ ግንባር ፡ እንሂድ ፡ በማለታችሁ ፡ በጣም ፡ እናመሰግናችኋለን ፡ አሁንም ፡ በቶሎ ፡ ሥንቃችሁን ፡ አደራጅተን ፡ ወደ ፡ ጦር ፡ ግንባር ፡ ትጓዛላችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይርዳችሁ ፡ ብሎ ፡ አሰናበታቸውና ፡ ወደ ፡ ሠፈራቸው ፡ ተመለሱ ።

ምዕራፍ ፡ ፴ ።

አሁንም ፡ ቢሆን ፡ በሥንቅና ፡ በግመል ፡ ማደራጀት ፡ ምክንያት ፡ ሁለት ፡ ወር ፡ ያኽል ፡ ከዚያው ፡ ከካራ ፡ መሬ ፡ የጦር ፡ ሠራዊቱ ፡ ሰፈሮ ፡ ተቀመጠ ።

ነገር ፡ ግን ፡ ለጠቅላይ ፡ ጦሩ ፡ ሹም ፡ የጦር ፡ ሠራዊቱ ፡ ዘወትር ፡ ምነው ፡ ወደ ፡ ጦሩ ፡ ግንባር ፡ አንሄድምን ፡ እያሉ ፡ ስላስቸገሩት ፡ የጦር ፡ ጠቅላዩ ፡ ለዋና ፡ የጦር ፡ አዛዡ ፡ በደብዳቤ ፡ ማስታወስ ፡ ግዴታ ፡ ሆነበት ።

ለክቡር ፡ የጦር ፡ አዛዥ ፡ ደጋ ፡ ሐቡር ፤ ክቡር ፡ ሆይ ፡ ከዛሬ ፡ ሁለት ፡ ወር ፡ በፊት ፡ ለይሉባቦር ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ የተሠጠውን ፡ ተስፋ ፡ በመጠበቅ ፡ ጊዜው ፡ ስለ ፡ ረዘመ ፡ በጣም ፡ አወኩኝ ፤ ምክን ያቱም ፡ የጦር ፡ ሠራዊቱ ፡ ካገሩ ፡ አየር ፡ ባለመስማማት ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ ታሟል ።

ስለዚህ ፡ ከዚህ ፡ ቀደም ፡ ለክቡርነትዎ ፡ ተሰብስበው ፡ እንዳስታ ወቁት ፡ በዚህ ፡ በበሽታ ፡ ከማለቅ ፡ ከጠላት ፡ ግንባር ፡ ሄደን ፡ ተለዋ ውጠን ፡ ብንሞት ፡ ዋጋ ፡ አለው ፡ የክብር ፡ ሞት ፡ እንሞታለን ፡ በማ ለት ፡ ነው ፡ ልመናቸው ፡ እውነትን፡ስለ ፡ ተደገፈ ፡ እኔም ፡ ራሴ ፡ ፈር ጄላቸዋለሁ ።

ስለዚህ ፡ ደጋ ፡ ሐቡር ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ ስብሰባ ፡ ሆኖ ፡ አንድ፡ ነገር ፡ ተቈርጦ ፡ ወደየሥራችን ፡ ብንሰመር ፡ የተሻለ ፡ ይመስለኛል ፡ ብሎ ፡ በጽሕፈት ፡ አስታወቀ ።

የጐሬ ፡ ጦር ፡ ጠቅላይ ፡ ሹም ፡
የገሙ ፡ ጐፋ ፡ ጦር ፡ ጠቅላይ ፡ ሹም ፡
ያሩሲ ፡ ጦር ፡ ጠቅላይ ፡ ሹም ፡
የኰሎ ፡ ጦር ፡ ጠቅላይ ፡ ሹም ፡

በሐረር ፡ ላይ ፡ ዋና ፡ የጦር ፡ አዛዥ ፡ በሆነው ፡ ሹም ፡ ሰብሳቢነት ፡ አራቱ ፡ ሹማምትና ፡ ከጦር ፡ አማካሪው ፡ ጄኔራል ፡ ወሂብ ፡ ፓሻ ፡ ጋራ ፡ ደጋ ፡ ሐቡር ፡ ስብሰባ ፡ ተደረገ ።

በዚህም ፡ ስብሰባ፡የምንመራበትን ፡ መሠረታዊ ፡ የጦር ፡ ፕላን ፡ (ንድፍ) ፡ ለማደራጀት ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ስለ ፡ ሥንቅ ፡ ስለ ፡ ጦር ፡ ታክቲክ፡(ዐቅድ) ፡ ይኸንን ፡ የመሰሉ ፡ የምሥጢር ፡ አሳቦች ፡ ናቸው። ባጭሩ ፡ የምንመራበት ፡ አሳብ ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ የተመለከተው ፡ ነው ። የይሉባቦርና ፡ የገሙ ፡ ጦር ፡ በደጋ ፡ ሐመዶ ፡ በኩል ፡ የሰገ ግን ፡ ሸለቆ ፡ ይዞ ፡ በብርቆት ፡ በኩል ፡ የጀነጋብን ፡ ወንዝ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ጣናን ፡ ተጕዞ ፡ ቈራሔ ፡ የሰፈረውን ፡ የጠላት ፡ ጦር ፡ ማጥቃት ።

የኰሎ ፡ ጦር ፡ ወደ ፡ ጅጅጋ ፡ ተመልሶ ፡ ደጀን ፡ ሆኖ ፡ ወደ ፡ ግንባር ፡ ለቀደመው ፡ ጦር ፡ ሥንቅ ፡ እንዲያቀብል ።

የሐረር ፡ ጦር ፡ በዋናው ፡ የጦር ፡ አዛዥ ፡ መሪነት ፡ በቀብሪ ፡ ደሐር ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ጣናን፡ ለሄደው ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ደጀን ፡ እንዲሆን ።

ያሩሲ ፡ ጦር ፡ ደጋ ፡ ሐቡር ፡ ሦፍሮ ፡ ለሐረር ፡ ጦር ፡ ደጀን ፡ እንዲሆን ፡ ተቈርጦ ፡ ሁሉም ፡ ስለ ፡ ተስማሙበት ፡ የጦር ፡ አለቆቹ ፡ ሁሉ ፡ ፈረሙበት ።

ቀጥሎም ፡ የገሙ ፡ ጐፋ ፡ ጦር ፡ እንደ ፡ ስምምነቱ ፡ መሠረት ፡ ወደ ፡ ጣናን ፡ ጉዞ ፡ ገሠገሠ ።

እንዲዚሁም ፡ የይሉባቦር ፡ ጦር ፡ ከብዙ ፡ ችግርና ፡ ጭቅጭቅ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ጣናን ፡ አመራ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የሁለቱ ፡ አገር ፡ ሠራዊቶች ፡ ቅደም ፡ ተከተል ፡ ሆነው ፡ ወደ ፡ ጦሩ ፡ ግንባር ፡ ጣናን ፡ ከሚባለው ፡ ቦታ ፡ የተከማቸ ውን ፡ የጠላት ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ለመውጋት ፡ ተጓዙ ። በዚያ ፡ በረሐ ፡ በፀሐዩ ፡ ሐሩርና ፡ በውሃ ፡ ጥም ፡ ይልቁንም ፡ እንደ ፡ በረዶ ፡ ቦምብ ፡ ሲዘንምባቸው ፡ በብዙ ፡ ሥቃይና ፡ ችግር ፡ የይሉባቦር ፡ የጦር ፡ ሠራዊትና ፡ የገሙ ፡ ጐፋ ፡ ጦር ፡ ጀነጋብ ፡ ደርሰው ፡ ወንዙንና ፡ ሸለቆውን ፡ ምሽግ ፡ አድርገው ፡ ሠፈሩ ።

የሰው ፡ ልጅ ፡ ምንም ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ጽኑ ፡ መከራ ፡ ቢደቀን ፡ ሞትም ፡ ከበራፉ ፡ እንኳን ፡ መጥቶ ፡ ቢቆም ፡ ራሱን ፡ መውደድና ፡ ኵራቱን ፡ የማይተው ፡ በመሆኑ ፡ የይሉባቦር ፡ ጦርና ፡ የገሙ ፡ ጐፋ ፡ ጦር ፡ ቀኙን ፡ እኔ ፡ ልያዝ ፡ ቀኙን ፡ እኔ ፡ ልያዝ ፡ በመባባል ፡ ጠብ ፡ ለማንሣት ፡ ማሰባቸው ፡ ተሰማ ።

ስለዚህ ፡ በይሉባቦር ፡ ጦር ፡ ጠቅላይ ፡ ሰብሳቢነት ፡ ከራስ ፡ ሰፈር ፡ የሁለቱም ፡ አገር ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ እንዲሰበሰቡ ፡ ተደረገ ።

ትንሽ ፡ ግብዣ ፡ ከሆነ ፡ በኋላ ፡ የይሉባቦር ፡ የጦር ፡ ጠቅላይ ፤ ክቡራን ፡ አባቶቻችን ፡ ዛሬ ፡ ከዚህ ፡ የሰበሰብኳችሁ ፡ እንደምታውቁት ፡ ከጠላት ፡ ግንባር ፡ ተቃረብን ።

እንግዴህ ፡ እናንተ ፡ የሁለት ፡ ወንድማማቾች ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ስለ ፡ ሆናችሁ ፡ ያንድ ፡ የጦር ፡ አለቃ ፡ ያንድ ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ናችሁ ።

ስለዚህ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ አደራ ፡ የምንጥልባችሁ ፡ እኔ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ብወድቅ ፡ ወንድሜን ፡ ተከትላችሁ ፡ ላገራችሁና ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥታችሁ ፡ ክብር ፡ እመጨረሻ ፡ ጠብታ ፡ ድረስ ፡ ደማችሁን ፡ አፍሱ ፡ እንጂ ፡ ባንድ ፡ ሰው ፡ መውደቅ ፡ አትፈቱ ።

እንደዚሁም ፡ ወንድሜ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ቢወድቅ ፡ እኔን ፡ ተከተሉ፡በሚሞት ፡ ሰው ፡ ምክንያት ፡ የማትሞተውን ፡ አገራችሁን ፡ ጥላችሁ ፡ አትሽሹ ።

ደግሞ ፡ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ የምንለምናችሁ ፡ የማን ፡ ጦር ፡ ቀኙን ፡ የማን ፡ ጦር ፡ ግራውን ፡ ይዞ ፡ እንደሚሰመር ፡ አስባችሁ ፡ መክራ ችሁ ፡ አስታውቁን ።

በውነትም ፡ በዚህ ፡ ዘዴ ፡ ሁሉም ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ ልባቸው ፡ ተነካ ። በጣምም ፡ አዝነው ፡ ከቍራን ፡ ጌቶቼ ፡ ሆይ ፡ እንደኛ ፡ እንኳ ፡ ብዙ ፡ ዓለም ፡ ያላያችሁ ፡ ሕፃኖች ፡ ምን ፡ በወጣችሁ ፡ በጭሩ ፡ ትቀ ጫላችሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ በአርበኝነት ፡ መልስ ፡ ከምትወዷቸው ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥትና ፡ ካገራችሁ ፡ ጋራ ፡ ተመልሳችሁ ፡ ለመተያየት ፡ ያብ ቃችሁ ፡ ካሉ ፡ በኋላ ፤ የገሙ ፡ ጐፋ ፡ ጦር ፡ አለቆች ፡ ብድግ ፡ ብለው ፡ ምንም ፡ እኛ ፡ የደጃዝማች ፡ በሻኽ ፡ አሽከሮች ፡ ብንሆን ፡ የራስ ፡ ቢትወደድ ፡ ተሰማን ፡ ጦር ፡ እንቅደም ፡ አንልም ። ስለዚህ ፡ የይሉ ባቦር ፡ ጦር ፡ ቀኙን ፡ ይያዝ ፡ እኛ ፡ ግራውን ፡ እንይዛለን ፡ ብለው ፡ አስታወቁ ።

በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ በማስተዋል ፡ ዘዴ ፡ ሁሉም ፡ ተስማምተው ፡ ከጀነጋብ ፡ ወንዝ ፡ ቀኝና ፡ ግራ ፡ ሸለቆውንና ፡ ዋሻውን ፡ ይዘው ፡ ሰፈሩ።

ጣሊያን ፡ ፋሺስትም ፡ ከቈራሔ ፡ አጠገብ ፡ ጣናን ፡ ከሚባለው ፡ የውሃ ፡ ጕድጓድ ፡ ላይ ፡ የጦ ፡ ሠራዊቱን ፡ አከማቸ ። የጦር ፡ አዝማ ቾቹም ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ የተመለከቱት ፡ ናቸው ።

ጄኔራል ፡ ግራዚያኒ ፤
ጄኔራል ፡ ናዚ ፤
ጄኔራል ፡ ፔርኒ ፤
ጄኔራል ፡ ፍሩሺ ፤
ጄኔራል ፡ አጎስቲኒ ፤

በሚያዝያ ፡ ወር ፡ በ፲፱፻፳፰ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ የፋሲካ ፡ ለት፡ ሌሊት ፡ የይሉባቦርና ፡ የገሙ ፡ ጐፋ ፡ ነጋሪት ፡ ስለ ፡ መድኃኒታችን፡

የትንሣኤ ፡ በዓል ፡ ይጉሸም ፡ ነበር ። ወታደሩም ፡ እየፎከረ ፡ ጠመንዣም ፡ እየተኰሰ ፡ እየሸለለ ፡ እያወካ ፡ ይጫወት ፡ ነበር ።

ጠላትም ፡ ነጋሪቱንና ፡ የጠመንዣውን ፡ ተኵስ ፡ ውካታውን ፡ ስለ ፡ ሰማ ፡ ሌሊት ፡ ጦሩ ፡ ሊገጥም ፡ ነው ፡ በማለት ፡ ፈርቶ ፡ መድ

ፉን ፡ ሲተኰስ ፡ ፋሩን ፡ ሲያበራ ፡ አነጋ ። ሚያዝያ ፡ ፯ ፡ ቀን ፡ ሮብ ፡ ለት ፡ ከጧቱ ፡ ባ፲፩ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ከጠላት ፡ ጋራ ፡ ጀነጋብ ፡ ወንዝ ፡ ውስጥ ፡ ደረት ፡ ለደረት ፡ ተጋጠሙ ። ቀኙን ፡ የይሉባቦር ፡ ጦር ፤ ግራውን ፡ የገሙ ፡ ጐፋ ፡ ጦር ፤ በጀነጋብ ፡ ሸለቆና ፡ ወንዝ ፡ ውስጥ ፡ ከጠላት ፡ ጋራ ፡ ተያይዞ ፡ ይተናነቅ ፡ ገመር ። ምንም ፡ ብዲሱ ፡ መሣሪያና ፡ መድፍ ፡ ታንክ ፡ ባይሮፕላን ፡ ቦምብ ፡ በመጣልና ፡ በጋዝ ፡ ጪስ ፡ እንደ ፡ ውሃ ፡ ፈሶ ፡ አካላት ፡ በሚበጣጥስ ፡ መርዝ ፡ ጠላት ፡ የዓለምን ፡ ሕግ ፡ አፍርሶ ፡ ቢዋጋ ፡ በግፍ ፡ መሬትኽን ፤ ቤትኽን ፤ ወንዝኽን ፤ ተራራኽን ፡ ልቀቅ ፡ የተባለው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ወታደር ፡ አምስት ፡ ጊዜ ፡ ሥፍራውን ፡ አስለቅቆ ፡ አባረረው ። ከሮብ ፡ አንሥቶ ፡ እስከ ፡ እሑድ ፡ ማታ ፡ ድረስ ፡ ከመሬታቸው ፡ ላይ ፡ ተቀብቅበው ፡ አዲስ ፡ መሣሪያ ፡ መከላከያ ፡ የሌላቸው ፡ የኢትዮጵያ ፡ አርበኞች ፡ ከታንኩ ፡ ላይ ፡ እየወጡ ፡ ሲታኰሱ ፡ ማየት ፡ ያኰራ ፡ ነበር ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ሁለቱን ፡ ልጆቹን ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ አድርጎ ፡ ሲከራከር ፡ ጠላት ፡ ቦታ ፡ ለቆለት ፡ ሸሸ ። አቶ ፡ ተማቹ ፡ ጐራዴውን ፡ መዞ ፡ ሲከተል ፡ አንድ ፡ የጦር ፡ አለቃ ፡ ምልክት ፡ ጋሎን ፡ ከትከሻው ፡ ላይ ፡ ያደረገ ፡ ከፊቱ ፡ ስላጋጠመው ፡ በጐራዴው ፡ ትከሻውን ፡ ቢያወራርደው ፡ ጋሎኑና ፡ ትከሻው ፡ ተለያዩ ። ቀደም ብለው ፡ የሸሹት ፡ የጠላት ፡ ወታደሮች ፡ አለቃቸው ፡ ሲወድቅ ፡ ስላዩ ፡ ዞረው ፡ ሮምታ ፡ ተኰሰው ፡ የጅ ፡ ቦምብ ፡ ወረወሩ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ እግሩንና ፡ የቀኝ ፡ ክንዱን ፡ ቈሰለ ፤ ፊቱም ፡ በቦምብ ፡ መርዝ ፡ ተቃጠለ ። ትንሹ ፡ ልጁም ፡ ጋሻው ፡ በዛ ፡ ከደረቱ ላይ ፡ በብርቱ ፡ ቈሰለ ፡ አባቱም ፡ ልጁም ፡ በቈሰሉት ፡ ብርቱ ፡ ቊስል ምክንያት ፡ ደም ፡ አንዝዟቸው ፡ ወደቁ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ጥቂት ፡ ቆይቶ ፡ ነፍሱን ፡ ሲያውቅ ፡ ከግሩ ፡ ላይ ፡ የወደቀው ፡ ምንድነው ፡ ብሎ ፡ አንሥቶ ፡ ቢመለከተው ፡ ልጁ ፡ ጋሻው ፡ በዛ ፡ ሆኖ ፡ አገኘው ። ቀጥሎ ፡ ያለው ፡ የጀነጋብ ፡ የጦር ፡ ሜዳ ፡ ካርታ ፡ ነው ።



Map of Djenegabo

ROME, 19 avril. — Commuinqué numéro 190 :

Le maréchal Badoglio télégraphie :

A l'aube du 14 courant, la division libyenne, sous le commandement du général Nasi a attaqué les forces éthiopiennes concentrées sur le fleuve Gianegobo et commandées par les dedjaz Abbebe Damtou et Maconnel Endelacoiou.

L'ennemi, tirant parti du terrain presque inaccessible et mettant à profit les cavernes et les anfractuosités, opposa une résistance acharnée au cours des journnées du 15 et du 16 et la matinée du 17 courant.

Les troupes nationales libyennes et somalies en liaison étroite et appuyees par lavlation soutinrent pendant o'es deux jóurnees et demie une lutte tres sévére qui s'est terminée par la défite complete de l'adversaire. Le mouvement d'encerclement des ailes qui a suivi a parfaitement réussi.

አንገቱን ፣ አቅፎ ፣ ልጄ ፣ ጋሻው ፣ በዛ ፣ ወግ ፣ ደረስኽ ፣ ስላገ ርኽ ፣ ካባትኽ ፣ ጋራ ፣ በጦር ፣ ሜዳ ፣ ወደቅኽ ፣ እኔም ፣ ወጣት ፣ ሳለሁ ፣ ከነብሮ ፣ ጋራ ፣ ስታገል ፣ ብቻዬን ፣ ከጠላቴ ፣ ጋራ ፣ በመው ደቂ ፣ አዝኜ ፣ እናትኽን ፣ ጽጌ ፣ ረዳን ፣ አገባሁ ። እነሆ ፣ አንተን ፣ በመውለዴ ፣ ካጠገቤ ፣ የምትወድቅ ፣ ልጅ ፣ አገኘሁ ።

ምንም ፣ ያንተን ፣ ሥቃይ ፣ በዚህ ፣ ምድረ ፣ በዳ ፣ በማየቴ ፣ ከልክ ፣ ያለፈ ፣ ኀዘን ፣ እንኳ ፣ ቢደርስብኝ ፣ የተመኘሁትን ፣ በማ ግኘቴ ፣ አልጸጸትም ።

እባክኽ ፣ ወንድምኽ ፣ ክንዴ ፣ ወዴት ፣ ሄደ ።

ጋሻው ፣ በዛ ፤ አባባ ፤ ቀድሞ ፣ ሮምታ ፣ የተተኰሰብን ፣ ጊዜ ፣ ተለያየን ፣ እኔ ፣ ያባባን ፣ ኮት ፣ ይገፎ ፣ ነበርና ፣ ካጠገብኽ ፣ ለመውደቅ ፣ በቃሁ ። አባባ ፤ ውሃ ፣ ጥም ፤ አቃጠለኝ ፣ ምን ፣ ልጠጣ ።

አቶ ፣ ተማቹ ፣ እያለቀሰ ፣ ወይ ፣ ግሩም ፣ ዘፈንና ፣ ተረት ፣ እስ ኪያጋጥም ፣ ድረስ ፣ እውነት ፣ አይመስልም ፣ ልጄ ፣ ሆይ ፣ አትበል ፣ ውሃ ፣ ውሃ ፣ ከደምኽ ፣ ጠጣለት ፤ በጦር ፣ የሞተ ፣ ሰው ፣ ቱነኔም የለ በት ፣ እያለ ፣ በለቅሶ ፣ ዜማ ፣ ዕንባውን ፣ ያፈስ ፣ ገ'መር ።

ጋሻው ፣ በዛ ፣ አባባ ፣ በማን ፣ ዕድሌ ፣ ደሜን ፣ በዋንጫ ፣ ጠጥቼ ፣ ከጥሜ ፣ በረካሁ ። ነገር ፣ ግን ፣ ስንኳን ፣ ደሜ ፣ ምራቄም ፣ ደረቀ ፣ አፌም ፣ ታሰረ ። ከዚህ ፣ ሥቃይ ፣ እንደ ፣ ምን ፣ ዐርፍ ፣ ይሆን ። አባባ ፤ እማማ ፣ ምን ፣ ይመስላት ፤ ያገሬ ፣ ውሃ ፣ በተራራው ፣ ላይና ፣ በሜዳው ፣ ላይ ፣ ሲፈስ ፣ እኔ ፣ አንዲት ፣ ጠብታ ፣ ውሃ ፣ አጥቼ ፣ በውሃ ፣ ጥም ፣ ሥቃይ ፣ ስሞት ።

አቶ ፣ ተማቹ ፣ አይዞኽ ፣ በርታ ፣ ልጄ ፣ ሆይ ፣ እኛ ፣ በበረሓ ፣ በውሃ ፣ ጥምና ፣ በቍስል ፣ በመከራ ፣ ተጨንቀን፤ላገራችን፣ መሥዋዕት ፣ ካልሆን ፣ ያገራችን ፣ ተራራና ፣ ውሃ ፣ በጠቅላላው ፣ ሀብቷ ፣ ሁሉ ፣ ለት ውልዳችን ፣ አይተላለፍም ። የስንዴ ፣ ቅንጣት ፣ በመሬት ፣ ላይ ፣ ተዘ ርታ ፣ ካልበሰበሰች ፣ ብዙ ፣ ፍሬ ፣ አታፈራም ፣ ተብሏል ። የተወደድኽ ፣ ልጄ ፣ ሆይ ፣ ነፃነትን ፣ የሚያፈራ ፣ ይህ ፣ በጦር ፣ ሜዳ ፣ ላይ ፣ የተዘራው ፣ እኽል ፣ አይደለምን ፣ እየተባባሉ ፣ ሲነጋገሩ ፣ መሸ ። በብዙ ፣ሬሳዎች ፣ መካከል ፣ ልጁን ፣ እየዳበሰ ፣ የሚያስፈራ ፣ የሞት ፣ ጥላ ፣ ወድቆበት ፣ ሌሊቱን ፣ ሁሉ ፣ ብቻውን ፣ በሚገርም ፣ እኳኋን ፣ አሳለፈው ፣ ከጧቱ ፣ ፩ ፣ ሰዓት ፣ ሲሆን ፣ የውጋዴን ፣ በረሓ ፣ሙቀት ፣ ገመረ ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ጋሻው ፡ በዛ ፤ አባባ ፡ ውሃ ፡ ውሃ ፡ ሲል ፡ አፉ ፡ ተሳስሮ ፡ በቍስልና ፡ በውሃ ፡ ጥም ፡ ሲጨነቅ ፡ አባቱ፡ጭን፡ ላይ ፡አረፈ።

ባቶ ፡ ተማቹ ፡ የደረሰበት ፡ ጽኑ ፡ ኀዘን ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ ሊነገር ፡ አይቻልም ። ሰው ፡ ምንም ፡ ቢወደው ፡ ሬሳውን ፡ ብቻ ፡ መውደድ ፡ ስለማይችል ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ነፍሱ ፡ ከሥጋው ፡ ስት ለይ ፡ የልጁን ፡ ግንባር ፡ ስሞ ፡ ልጄ ፡ደኅና ፡ ሰንብት ፡ አንተንስ፡ ተሰናበትኩኽ ፡ እንግዴህ ፡ ወንድምህን፡ ክንዴን ፡ ሳልሰናበተው ፡ አላመለስምና፡ ሬሳውን፡ ልፈልግ፡ ብሎ ፡ ልጁን ፡ ከጭኑ ፡ ላይ ፡ አን ሥቶ ፡ ከመሬት ፡ ጥሎ፡ እግሩና ፡ ክንዱ ፡ የቈሰለ ፡ ፊቱ ፡ በቦምብ ፡ መርዝ ፡ የጠቈረ ፡ ልብሱ ፡ በርሳስ ፡ የተበሚጨቀ ፡ ሰውነቱ ፡ በደም፡ የተለወሰ ፡ አንድ ፡ በትር ፡ በጁ ፡ ይዞ ፡ አርበኛው ፡ አቶ ፡ ተማቹ፡ በዚያ ፡ ሁሉ ፡ ሬሳ ፡ መካከል ፡ ቆሞ ፡ ሲታይ ፡ ያሳዝን ፡ነበር ።

ይልቁንም ፡ በሺህ ፡ የሚቈጠሩ ፡ አሞሮች ፡ በሬሳዎቹ ፡ ላይ፡ እያንዣበቡ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ምርኵዙን ፡ ይዞ ፡ ስለ ፡ ቆመ ፡ ምን፡ ይሆን ፡ በማለት ፡ ለመውረድና ፡ ለመብላት ፡ አልደፈሩም ፡ ነበር ። በሩቁም ፡ ዐርፈው ፡ ይጠባበቁ ፡ ነበር ። ካሞሮቹም ፡ በስተቀር ፡ ተናጣቂ ፡ አውሬዎች ፡ እንደ ፡ ዥብና ፡ እንደ ፡ ተኵላ ፡ ያሉ ፡ ሁሉ ፡ በሩቁ ፡ እየተመለከቱ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ የተዘራውን ፡ ሰብላ ቸውን ፡ ለመከፈል ፡ ይጠባበቁ ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ምርኵዙን ፡ ይዞ ፡ አንድ ፡ በጥይት ፡ የተበጣ ጠሰች ፡ የካኪ ፡ ባርኔጣውን ፡ አድርጎ ፡ ልጁን ፡ ክንዴን ፡ ለመፈ ለግ ፡ ሬሳውን ፡ ሁሉ ፡ እያነሣ ፡ እየጣለ ፡ ይበረብር ፡ ዠመር ። ከብ ዙም ፡ ሬሳ ፡ መካከል ፡ ፊታውራሪ ፡ አበበ ፡ መብረቁን ፡ አገኘው ።

አበበ ፡ ፊቴን ፡ አላዞርም ፡ ብለኽ ፡ እንደ ፡ ፎከርኽ ፡ በግንባርኽ፡ ወደቅኽ ፤ አሁንም ፡ አልሞትኽም ፡ ሕያው ፡ ነኽ ፡ ብሎት ፡ አለፈ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ብዙ ፡ ሬሳ ፡ እያየ ፡ ጦርነት ፡ ወደ ፡ ተዠመ ረበት ፡ ራቅ ፡ ብሎ ፡ ከሄደ ፡ በኋላ ፡ ፊታውራሪ ፡ ከበደ ፡ ዘውዴን ፡ ሁለቱ ፡ ልጆቹ ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ ወድቀው ፡ ከብዙ ፡ ሬሳ ፡ መካከል ፡ አገኘውና ፡ ዘውዴ ፡ ጌታዬ ፡ ያስያዘኻን ፡ ቦታ ፡ አለቅም ፡ በማለት፡ ጠላቶችኽን ፡ ፈጅተኽ ፡ ሁለቱን ፡ ልጆችኽን ፡ ለብሰኽ ፡ ተኝተኻ ልን ፡ ዕድለኛው ፡ አርበኛ ፡ በቁምኽ ፡ የልጆችኽን ፡ ሥቃይ ፡ ሳታይ፡ ላገርኽና ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥትኽ፡ ክብር ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ወደ ቅኽ ፤ ዕድለኛ ፡ ነኽ ፡ ብሎ ፡ አለፈ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ እንደዚሁ ፡ ወደ ፡ ፊቱ ፡ እየሄደ ፡ በግንባራቸው ፡ የተደፉትን ፡ ሬሳዎች ፡ እየገለበጠ ፡ ልጁን ፡ ሲፈልግ ፡ ቀኛዝማች ፡ እሸቱ ፡ ተሸበሩን ፡ የጠመንዣውን ፡ ቃታ ፡ በጣቱ ፡ እንደ፡ ያዘ ፡ በግንባሩ ፡ ወድቆ ፡ አየውና ፡ ቀና ፡ አድርጎ ፡ እሸቱ ፡ ስትሞትም ፡ ትተኵሳለኽ ፡ እውነተኛው ፡ እንበሳ ፡ አሁንስ ፡ ጣትኽን ፡



አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ አሞሮችን ሲከላከል ።

ከቃታው ፡ ልቀቅ ፡ ስላገርኽ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ተኛ ፡ አንተ ፡ ብትሞት ፡ ታሪክኽ ፡ አይሞትም ፡ ብሎት ፡ አለፈ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ልጁን ፡ በመፈለግ ፡ እንዳበደ ፡ ሰው ፡ ሬሳውን ፡ ሁሉ ፡ እያነጣ ፡ ሲመለከት ፡ ቀኛዝማች ፡ ጣሾን ፡ በጅ ፡ በምብ ፡ ከወገቡ ፡ ላይ ፡ ከሁለት ፡ ተቈርጦ ፡ ጥይቱ ፡ አልቆ ፡ ዝናሩና ፡ ጠመንዣው ፡ ከፊቱ ፡ ወድቀው ፡ ከመቶ ፡ የሚበልጡ ፡ የፋሺስት ፡ ወታደሮች ፡ ሬሳ ፡ ካጠገቡ ፡ ተጋድመው ፡ አየና ፡ ጣሾ ፡ እውነተኛው ፡ አርበኛ ፡ ለምስክር ፡ ከወገብኽ ፡ በላይ ፡ ተገኘኽ ። ጠላቶችኽ ፡ ከፊትኽ ፡ ስለ ፡ ወደቁ ፡ ልትኰራ ፡ ይገባኻል ። ዝናርኽም ፡ ለምስክር ፡ ባዶውን ወድቋል ። የፈጀኻቸው ፡ ጠላቶች ፡ በዚሁ ፡ ልክ ፡ ይቈጠራሉ ። አሁ

ንም ፡ ቢሆን ፡ ግማሽ ፡ ሰውነትኽ ፡ በጠላቱ ፡ ላይ ፡ ሲፎክር ፡ ይታያል ። ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ አልሞትኽም ፡ ሕያው ፡ ነኽ ፡ ደኅና ፡ ሰንብት ፡ ብሎት ፡ አለፈ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ክንዴን ፡ እየፈለገ ፡ በሬሳ ፡ መካከል ፡ ሲጓዝ፡ ፊታውራሪ ፡ መኰንን ፡ ኃይሌንና ፡ ፊታውራሪ ፡ ደምሴ ፡ ሩፌን ፡ ጐን ፡ ለጐን ፡ ተቃቅፈው ፡ በግንባራቸው ፡ ወድቀው ፡ አየና ፡ በዓለሙ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ተዋደዳችሁ ፡ አሁንም ፡ ስላገራችሁና ፡ ስለ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥታችሁ ፡ ክብር ፡ ስትሉ ። በመ ተባበር ፡ ጠላትን ፡ አጥቅታችሁ ፡ ወድቃችኋልን ፡ ደማችሁ ፡ ነፃነት ፡ እስኪያበቅል ፡ ድረስ፣ ተኙ ፡ ብሎ ፡ አለፈ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሁለተኛ ፡ ጦርነት ፡ ከተደረገበት ፡ ቦታ ፡ ብርቆት ፡ ከሚባለው ፡ ሸለቆ ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ ልጁን ፡ እየፈለገ ፡ ተመልሶ ፡ ይጓዝ ፡ ጀመር ። ብዙ ፡ መንገድ ፡ ከሄደ ፡ በኋላ ፡ አምስት ፡ ሰዎች ፡ ተቃቅፈው ፡ በግንባራቸው ፡ ወድቀው ፡ አሞራ ፡ በላያቸው፣ ላይ ፡ሰፍሮ ፡ ደረሰ ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ አሞሮቹን ፡ ለማባረር ፡ እየጮኸ በትሩን ፡ ይዞ ፡ ወደነሱ ፡ ሲቀርብ ፡ አሞሮቹ ፡ በረሩ ። ቀና ፡ አድርጎ ፡ ቢመለከት ፡ ፊታውራሪ ፡ ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴ ፡ ከነልጆቹና፡ ፊታውራሪ ፡ መኰንን ፡ ዘርጋው ፡ ቀኛዝማች ፡ ገሠሠ፡ መሆናቸውን፡ ከተረዳ ፡ በኋላ ፡ አንበሳው ፡ ኀይለ ፡ ማርያም ፡ ጣሴ ፡ ስላገርኽ ፡ ወደ ፡ ጦሩ ፡ ግንባር ፡ ስደዱን ፡ ምነው ፡ አሞራስ ፡ ደኅና ፡ ሥጋ ፡ ቢበላ ፡ ምን ፡ ቸገራችሁ ፡ ብለኽ ፡ ፎከረኽ ፡ ነበር ። እንሆ ፡ ከነልጆችኽና ፡ ከጦር ፡ ጓደኞችኽ ፡ ጋራ ፡ ያሞራ ፡ ምሳ ፡ ሆንክ ፡ የተመኘኸውን ፡ ስላገኘኽ ፡ ደስ ፡ ይበልኽ ፡ አርበኛው ፡ አንበሳ ፡ ደኅና ፡ ሰንብት ፡ ብሎት ፡

የወታደር ፡ እናት ፡ ታጠቂ ፡ በገመድ ።

ልጅሽን ፡ አሞራ ፡ እንጂ ፡ አይቀብረውም ፡ ዘመድ ፡

ዘመድ ፡ አይቀብረውም ፡ እንደ ፡ ሌላ ፡ ሁሉ ፡

ያርበኛ ፡ መቃብር ፡ አሞራ ፡ ነው ፡ አሉ ።

እያለ ፡ የለቅሶ ፡ ሙሾ ፡ እያዜመ ፡ ብዙ ፡ ከተጓዘ ፡ በኋላ ፡ ቀኛዝማች፡ በለጠን ፡ በታንክ ፡ ተደፍጦ ፡ አንገት ፡ ጉብቱ ፡ ወጥቶ ፡ አገኘውና ፡ በለጠ ፡ በውነትም ፡ በለጥኽ ፡ እንደ ፡ ፎከርኽ ፡ ታንኩን ፡ በጐራዴ ፡ መትኽ ፡ በመሬትኽ ፡ ላይ ፡ ተፈጭተኽ ፡ ትቢያ ፡ ሆንኽ ፡ ቀረኽ ። አይዞኽ ፡ መሬት ፡ ነኽና ፡ ወደ ፡ መሬት ፡ ትመለሳለኽ ፡ የተባለውን ፡

ቃል ፡ አንተ ፡ ፈጸምከው ፡ እንጂ ፡ በዚህ ፡ ሜዳ ፡ የተዘራው ፡ እኽል ሁሉ ፡ መበስበሱና ፡ መፍረሱ ፡ መሬት ፡ መሆኑ ፡ አይቀርም ። አርበ ኛው ፡ በለጠ ፡ አይዞኽ ፡ ከጥቂት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ነፃነትን ፡ ታበቅ ላለኽ ፡ ብሎት ፡ አለፈ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ብዙዎች ፡ ሬሶች ፡ እያየ ፡ ከተራመደ ፡ ወዲያ፡ ፊታውራሪ ፡ ይቀጡን ፡ አገኘና ፤ ይቀጡ ፡ ስላገርኽ ፡ በክብር ፡ ስለ፡ ሞትኽ፡ ደስ ፡ ይበልኽ ፡ በጦር ፡ ሜዳ፡ ላይ ፡ የሚሞት ፡ አይሞ ትም ፡ ሕያው ፡ ነኽ ፡ ደኅና ፡ ሰንብት ፡ ብሎት ፡ እንደዚሁ ፡ ሬሳ ውን ፡ ሁሉ ፡ እያየ ፡ ይጓዝ ፡ ዠመር ። ብዙ ፡ ራቅ ፡ ብሎ ፡ ከኼደ ፡ በኋላ ፡ በሩቁ ፡ አንድ ፡ ሬሳ ፡ በጠላቱ ፡ ሬሳ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ አንድ፡ ጥንበ ፡ በላ ፡ አሞራ ፡ በሱ ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡ ሊበላና ፡ ሊነጭ ፡ ሲጐን በስ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ በሩቁ ፡ አይቶ ፡ አሞራውን ፡ የትአባትኽ ፡ እኔ፡ ሳልኼድ ፡ ይኸንን ፡ ጐበዝ ፡ ትበላዋለኽ ፡ እያለ ፡ በትሩን ፡ አንሥቶ ፡ እያነከሰ ፡ ይሮጥ ፡ ዠመር ። አሞራውም ፡ ያቶ ፡ ተማቹን ፡ ድምፅ፡ በሰማ ፡ ጊዜ ፡ ተነሣና ፡ እልፍ ፡ ብሎ ፡ ዐርፎ ፡ ይጠባበቅ ፡ ዠመር ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ሬሳውን ፡ ከጠላት ፡ ሬሳ ፡ ላይ ፡ አንሥቶ ፡ ቢመ ለከተው ፡ ልጁ ፡ ክንዴ ፡ ሆኖ ፡ አገኘው ። አቶ ፡ ተማቹ ፡ እቅፍ ፡ አድርጎ ፡ እየሳመ ፡ ልጄ ፡ ክንዴ ፡ ከጠላትኽ ፡ ላይ ፡ ሆነኽ ፡ በየሁኸ፡ ጊዜ ፡ እንዴት ፡ ደስ ፡ አለኝ ። አሞራው ፡ ግን ፡ ለጠላት ፡ ረዳት ፡ ሆኖ ፡ ሊበላኽ ፡ ሲል ፡ አዳንኩኽ ። ልጄ ፡ አፍኽን ፡ የከፈትኸው፡ እኔን ፡ ስትጣራ ፡ ነውን። እንግዴህ ፡ አንተን፡ ከተለናበትኩኽ ፡ ሞቴን፡ እስካገኝ ፡ ድረስ ፡ ልጓዝ ፤ አርበኛው ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ደኅና ፡ ሰንብት፡ ብሎ ፡ ሬሳውን ፡ አንገቱን ፡ አቅፎ ፡ እያለቀሰ ፡ ከሳመው ፡ በኋላ ፡ እንግዴህ ፡ አንተ ፡ አሞራ ፡ ያውልኽ ፡ ብላው ፡ ብሎ ፡ ጥሎት ፡ ወደ ፊቱ ፡ ይጓዝ ፡ ዠመር ። መንገዱን ፡ ሁሉ ፡

የኔ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ታጠቂ ፡ በገመድ ፤

ልጅሽን ፡ አሞራ ፡ እንጂ ፡ አይቀብረውም ፡ ዘመድ ።

እያለ ፡ የሰገግን ፡ መንገድ ፡ በለቅሶ ፡ ሲጓዝ ፡ ቀኛዝማች ፡ ሸንኮሩ ፡ መኰንን ፡ የሚባለው ፡ ሁለት ፡ ታፋው ። በቦምብ ፡ ተገንጥሎ ፡ ወድቆ፡ ባጠገቡ ፡ ብዙ ፡ የጠላት ፡ ወታደር ፡ ሬሳ፡ ተረፍርፎ ፤ ቀኛዝማች ሸንኮሩ ፡ አቶ ፡ ተማቹን ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ እባክኽ ፡ አንተ ፡ ሰው፡ ጨርሰኝና ፡ መሣሪያዬን ፡ ለጠላት ፡ እንዳያገለግል ፡ አንተ ፡ ውሰ ደው ፡ እያለ ፡ ጮኸ ፡ ይለምነው ፡ ዠመር ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ በጣም ፡ ስላሳዘነው ፡ ቆሞ ፡ እየተመለከተ ፡ ያስብ ፡ ዠመር ። ተሸክሞት ፡ እንዳይኼድ ፡ ከወገቡ ፡ በታች ፡

ተበጣጥሶ ፡ ለማንሣት ፡ ለመሸከም ፡ የማይቻል ፡ ሆነ ። ገድሎትም ፡ እንዳይሄድ ፡ የወንድሙን ፡ ደም ፡ ማፍሰስና ፡ መግደል ፡ ኃጢአት ፡ ይሆንብኛል ፡ ብሎ ፡ ሠጋ ።

ስለዚህ ፡ እሱን ፡ እሱን ፡ እየተመለከተ ፡ ዕንባውን ፡ እያፈሰሰ ወዳጄ ፡ ሸንኮሩ ፡ አንተን ፡ ለመጨረስ ፡ እጄስ ፡ እንደምን ፡ ይደፍራል ። ወይም ፡ ተሸክሜኽ ፡ እንዳልሄድ ፡ እጄን ፡ እግሬን ፡ የቈሰልኩ ፡ አንተም ፡ ከወገብኽ ፡ በታች ፡ የተበጠስኽ ፡ ነኽ ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ ምን ፡ ላደርግኽ ፡ እችላለሁ ።

ቀኛዝማች ፡ ሸንኮሩ ፡ ስንኳን ፡ እጅኽ ፡ እግርኽ ፡ በዐረር ፡ ተበጣጥሶ ፡ ፊትኽም ፡ በቦምብ ፡ ተቃጥሎና ፡ ደኅናም ፡ ብትሆን ፡ እንኳ ፡ እኔን ፡ ተሸክመኽ ፡ በዚህ ፡ በውጋዴ ፡ በረሐና ፡ ሙቀት ፡ ሐሩርና ፡ ውሃ ፡ ጥም ፡ አገሬ ፡ ታደርሰኛለኽ ፡ ማለት ፡ ሕልም ፡ ነው ።

ነገር ፡ ግን ፡ እነዚህ ፡ የተሰለፉት ፡ አሞሮች ፡ ነፍሴ ፡ ሳት ወጣ ፡ እየበጫጨቁ ፡ ሥቃይ ፡ እንዳያሰዩኝ ፡ በቶሎ ፡ ልታሳርፈኝ ፡ ትችላለኽ ፤ እባክኽ ፡ ወንድሜ ፡ እንደዚህ ፡ ያለው ፡ አገዳደል ፡ ወንድምን ፡ ማዳን ፡ ይባላል ፡ እንጂ ፡ መግደል ፡ አይባልም ። አሁን ፡ ሳትጨርሰኝ ፡ ብትሄድ ፡ ወንድ ፡ አይደለኽም ፡ ስለኔ ፡ ሥቃይ ፡ ማየት ፡ በነፍስኽም ፡ በሥጋኽም ፡ እንደሚፈረድብኽ ፡ ዕወቀው ፡ እያለ ፡ ስቅቅ ፡ ብሎ ፡ አለቀሰ ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ በሰማይ ፡ ላይ ፡ አሞራው ፡ ሬሳውን ፡ ሁሉ ፡ ለመብላት ፡ ሲያንዣብብ ፡ አይቶ ፡ በውነትም ፡ ሥቃይ ፡ ከማየት ፡ ቢያርፍ ፡ ይሻላል ፡ ብሎ ፡ ከቀኛዝማች ፡ ሸንኮሩ ፡ እጅ ፡ ጠመንዣውን ፡ ተቀብሎ ፡ ዝናሩን ፡ ፈቶ ፡ አምስት ፡ ጥይቶች ፡ አጕርሦ ፡ ወንድሜ ፡ ልገድልኽ ፡ ነውና ፡ ዓይንኽን ፡ ጨፍን ፡ አለው ።

ቀኛዝማች ፡ ሸንኮሩም ፡ ሞትን ፡ በጣም ፡ ለማየት ፡ ስለ ፡ናፈቅሁ ፡ ሞቴን ፡ ለማየት ፡ እፈቅዳለሁና ፡ ተኰስ ፡ አለው ።

አቶ ፡ ተማቹም ፡ ተኵሶ ፡ ገደለውና ፡ ጠመንዣውንና ፡ ዝናሩን ፡ ወርውሮ ፡ ጥሎ ፡ እኔ ፡ ሞትን ፡ ለመፈለግ ፡ የምኼዝ ፡ ሰው ፡ የመከላከያ ፡ መሣሪያ ፡ ለምክንያት ፡ መያዝ ፡ አይገባኝም ፡ ብሎ ፡ ወገኑን ፡ ከሚበልጥ ፡ ሥቃይ ፡ ለማዳን ፡ ሲል ፡ ነፍስ ፡ በመግደሉ ፡ እያዘነ ፡ ብቻውን ፡ እንደዚህ ፡ እያለ ፡ ይነጋገር ፡ ነበር ። ወይኔ ፡ ራሴን ፡ ወዳድ ፡ ኀጢአተኛ ፡ ራሴን ፡ በራሴ ፡ መግደል ፡ ፈርቼ ፡ ወንድሜን ፡ ገደልኩ ፡ እያለ ፡ ያሟሟቱ ፡ ነገር ፡ ትዝ ፡ ስለሚለው ፡

እያለቀሰ ፡ በጭቆ ፡ በኩል ፡ የሰገግን ፡ ወንዝ ፡ ይዞ ፡ ወደ ፡ ደጋ ፡ ሐመዶ ፡ ተጓዘ ። ኻያ ፡ ቀን ፡ ያኽል ፡ በዚያ ፡ በረሐ ፡ ቀጭቀጫ ፡ የሚባል ፡ የዛፍ ፡ ፍሬ ፡ እየበላ ፡ በመንገዱ ፡ ላይ ፡ ሁሉ ፡ ሬሳ ፡ ወድቆ ፡ አውሬና ፡ አሞራ ፡ ሲካፈለው ፡ አሁን ፡ አሁን ፡ እኔን ፡ ሊበሉኝ ፡ ነው ፡ እያለ ፡ ሞትን ፡ እየፈለገ ፡ ዕድል ፡ ፈንታውን ፡ ሲጠባበቅ ፡ በኻያ ፡ አንደኛው ፡ ቀን ፡ ከጧቱ ፡ ባንድ ፡ ሰዓት ፡ ደጋ ፡ ሐመዶ ፡ ደረሰ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ፊት ፡ ለፊቱ ፡ የቅዱስ ፡ ገብርኤልን ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ስላየ ፡ ለመሳለም ፡ ሄዶ ፤ በወንዶች ፡ መቋሚያ ፡ በር ፡ አጠገብ ፡ ቆሞ ፡ የደረሰበትን ፡ መከራ ፡ እያሰበ ፡ ይልቁንም ፡ የቀኛዝማች ፡ ሸንኮሩ ፡ አሟሟት ፤ እያንቀጠቀጠው ፡ የመረረ ፡ ልቅሶ ሲያለቅስ ፡ አንድ ፡ የመንዝ ፡ ተወላጅ ፡ አቶ ፡ ፍቅሩ ፡ የሚባል ፡ ሰው ፡ በሩቁ ፡ ሲያለቅስ ፡ ስላየው ፡ አጠገቡ ፡ መጥቶ ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ ከዚህ ፡ ምን ፡ ታደርጋለኽ ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ።

አቶ ፡ ተማቹም ፡ ጌታዬ ፡ ምን ፡ እንደሆንኩ ፡ እኔም ፡ ራሴን ፡ አላውቀውም ፡ ባጭሩ ፡ እንደማስታውቅዎ ፡ እኔ ፡ ሞት ፡ የተፋኝ ፡ ሰው ፡ ነኝ ፡ እንደሚያዩኝ ፡ ሥጋዬ ፡ በጥይት ፡ ተበጣጥሶ ፡ ፊቴም፡ በቦምብ ፡ መርዝ ፡ ተበላሽቶ ፡ በእሳትም ፡ ተቃጥሎ ፡ ከዚህ ፡ ሁሉ መከራ ፡ አምልጬ ፡ እንሆ ፡ ለጉድ ፡ ከዚህ ፡ ቆሜያለሁ ፡ እኔም ፡ ራሴን ፡ በራሴ ፡ ለመግደል ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ አስቤ ፡ ነበር ።

ነገር ፡ ግን ፡ የራሴ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ ከመሆን ፡ አውሬ ፡ ቢበላኝ ፡ ወይም ፡ ሱማሌ ፡ ቢገድለኝ ፡ ይሻላል ፡ በማለት ፡ ብቻዬን ፡ መከላከያ ፡ መሣሪያዬን ፡ ጥዬ ፡ ስጓዝ ፡ ምንም ፡ አደጋ ፡ ሳያገኘኝ ፡ ከዚህ ፡ ደረስኩ ።

ሰውዬው ፤ አገርኽ ፡ ወዴት ፡ ነው ፤

አቶ ፡ ተማቹ ፤ አገሬ ፡ ተጉለት ፡ ነው ።

ሰውዬው ፤ ካገርኽ ፡ በምን ፡ ምክንያት ፡ ወደዚህ ፡ መጣኽ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ አገሬ ፡ በጠላት ፡ ስለ ፡ ተወረረች ፡ ሁለቱን ፡ ትልልቅ ፡ ልጆቼን ፡ ይዤ ፡ ለመርዳት ፡ መጣሁ ።

ሰውዬው ፤ ልጆችኽ ፡ ወዴት ፡ ሄዱ ፤

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ሁለቱም ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ወድቀው ፡ ቀሩ። እንሆ ፡ እኔም ፡ ዘሬን ፡ በጨርቅ ፡ ቋጥሬ ፡ ከጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ዘርቼ ፡ መጣሁ ።

ሰውዬው ፤ ዕንባው ፡ ካይኑ ፡ እየፈሰሰ ፡ ሚስትና ፡ ሌሎች ፡ ልጆች ፡ የሉኽምን ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከራሴ ፡ አብልጬ ፡ የምወዳት ፡ ሚስት ፡ አለችኝ ፤ ከሷም ፡ ጋራ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ልጅና ፡ አንድ ፡ ሕፃን ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ አለኝ ።

አሁንም ፡ ቢሆን ፡ ሞት ፡ ከጠላኝ ፡ ሚስቴን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ አይቻት ፡ ብሞት ፡ እወድ ፡ ነበር ፡ ብሎ ፡ ዕንባው ፡ ካይኑ ፡ ይረግፍ ፡ ዠመር ።

ሰውዬው ፤ አይዞኽ ፡ አታልቅስ ፡ እኔ ፡ አስታምምኽና ፡ ስትድን ፡ ወደሚስትኽ ፡ ትኼዳለኽ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ወስዶ ፡ ደኅና ፡ አድርጎ ፡ ያስታምመው ፡ ዠመር ።

ከስድስት ፡ ወር ፡ በኋላ ፡ በጣም ፡ ተሻለው ፤ እግሩም ፡ ከማንከሱ ፡ በቀር ፡ ቍስሉ ፡ ፈጽሞ ፡ ሻረ ። ፊቱም ፡ በመርዝ ፡ ስለ ፡ ተቃጠለ ፡ በፍጹም ፡ የማይታወቅ ፡ ጥቍር ፡ ሰው ፡ ደዌ ፡ ሥጋ ፡ የያዘው ፡ ይመስል ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በቍስሉ ፡ ምክንያት ፡ የሚያመው ፡ ነገር ፡ የለም ። በጣም ፡ የሚያሳዝነው ፡ በመርዙ ፡ ምክንያት ፡ አንድ ፡ ዓይኑ ፡ ጠፍቶ ፤ አንድ ፡ ዓይኑ ፡ ብቻ ፡ ያያል ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ በጣም ፡ ከተሻለው ፡ በኋላ ፡ ለሰውዬው ፡ ወንድሜ ፡ እንግዴህ ፡ ወዳገሬ ፡ ልሂድ ፡ አንተም ፡ ስላደረግኽልኝ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ የርኅራኄ ፡ ሥራ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዋጋህን ፡ ይክፈልህ ፤ እንግዴህ ፡ ኑሮ ፡ ኑሮ ፡ ከመሬት ፤ ዞሮ ፡ ዞሮ ፡ ከቤት ፡ የሚቀር ፡ የለምና ፡ ለጕድ ፡ ካስቀመጠኝ ፡ ይኸንን ፡ ኀዘኔን ፡ የምጸናናበት ፡ ሚስቴንና ፡ የተረፉትን ፡ ልጆቼን ፡ ማየት ፡ ብቻ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ እንድታሰናብተኝ ፡ እለምንኻለሁ ።

ሰውዬውም ፡ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ እኔ ፡ ከዚህ ፡ የበለጠ ፡ ደስታ ፡ የለኝም ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ስላገርኽ ፡ ቈስለኽ ፡ ፊትኽ ፡ ተበላሽቶ ስትመጣ ፡ ማስታመም ፡ ኢትዮጵያ ፡ ቈስላ ፡ እንደማስታመም ፡ ያለ ፡ ነው ።

ስለኛ ፡ መልካም ፡ ኑሮ ፡ ስትል ፡ ሁለቱን ፡ ልጆችኽን ፡ መሥዋዕት ፡ ያደረግክ ፡ ጀግና ፡ አንተን ፡ ማስታመም ፡ ትልቅ ፡ ዕድል ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ አንገቱን ፡ አቅፎ ፡ ስሞ ፡ ሂድ ፡ እግዚአብሔር ፡ በደኅና ፡ ያግባኽ ። ነገር ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ የምመክርኽ ፡ አገር ፡ ስትጠፋ ፡ የቤተ ፡ ዘመድ ፡ ኑሮና ፡ የሰውነት ፡ መብት ፡ አብረው ፡ ተያይዘው ፡ እንደሚጠፉ ፡ የታወቀ ፡ ነውና ፡ ተጠንቀቅ ፤ ላንተ ፡ መልካም ፡ ዕድል ፡ ያጋጥምኽ ፡ አደራኽን ፡ ከሚስትኽና ፡ ከልጆችህ ፡ ደኅና ፡ መገናኘትህን ፡ ጻፍልኝ ፡ ብሎ ፡ ለሥንቁ ፡ ጥቂት ፡ ገንዘብ ፡ ሰጥቶ ፡ ጕንጩንና ፡ ጕንጩን ፡ ስሞ ፡ አሰናበተው ፡ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ጕዞውን ፡ ቀጠለ ።

ምዕራፍ ፡ ፫ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ምርኵዙን ፡ ይዞ ፡ አሮጌ ፡ ካስኩን ፡ አድርጎ፡ የተበጫጨቀ ፡ ልብሱን ፡ ለብሶ ፡ በባዒሌ ፡ በኩል ፡ የሐረርን ፡ መን ገድ ፡ ይዞ ፡ ይጓዝ ፡ ዠመር ።

በ፲፫ኛው ፡ ቀን ፡ ሐረርጌ ፡ ከተማ ፡ ደረሰ ፤ በከተማው ፡ ውስጥ፡ እያለቀሰ ፡ ምርኵዙን ፡ ይዞ ፡ በቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ አጠገብ ፡ ሲያ ልፍ ፡ ቀና ፡ ብሎ ፡ ሰንደቅ ፡ ዓላማው ፡ የሚሰቀልበትን ፡ ቢመለከት ፡ የጠላት፡ባንዲራ፡ሲውለበለብበት፡በማየቱ፡ጥልቅ፡የሆነ፡ አዘን፡ አዘነ።

ይልቁንም ፡ ከከተማው ፡ ውስጥ ፡ ያገሩ ፡ ተወላጅ ፡ ሸሽቶ ፡ ነጭ ፡ ብቻ፡ ስለ፡ ሰፈረበት ፡ ፈጽሞ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ከተማ አልመስል ፡ አለው ። በጣም ፡ ያሳዘነው ፡ አንድ ፡ ያገር ፡ ተወላጅ፡ ቢኖር ፡ እንኳ ፡ እንደ ፡ ሰረቀ ፡ ሰው ፡ ሲፈራና ፡ ሲጨነቅ ፡ ሲንቀጠ ቀጥ ፡ አይቶ ፡ በዚች ፡ በጠላት ፡ የሞት ፡ ጥላ ፡ ባረፈባትና ፡ በተ ረገመች ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ ማደር ፡ አይገባኝም ፡ ብሎ ፡ ከእኩለ ፡ ቀን ፡ በኋላ፡ከሐረርጌ፡እልፍ ፡ ብሎ ፡ አማሬሳ ፡ ከሚባለው ፡እገር ፡ ሲደርስ ፡ካንድ ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፤ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ተሰብስቦ ፡ ሲመለከት ፡ አየ ።

አቶ ፡ ተማቹም ፤ ይህ ፡ ነገር ፡ ምን ፡ ይሆን ፡ ብሎ ፡ ሸለቆ ውን ፡ ወርዶ ፡ ቢያይ ፡ አንድ ፡ የፋሺስት ፡ ሹም ፡ የኢትዮጵያ ፡ ተወላጅ ፡ የሆነውን ፡ አንድ ፡ ድኻ ፡ እጁን ፡ አጣምሮ ፡ አስሮ ፡ አንገቱን ፡ እንደ ፡ ሙቀጫ ፡ ባለ ፡ ዕንጨት ፡ ላይ ፡ አጋድሞ ፡ በፋስ ፡ ሲያስጐርጥ ፡ አየ ።

ስላገሩ ፡ እንደ ፡ በግ ፡ የታረደው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ድኻ ፡ ደሙ፡ እንደ ፡ ጐርፍ ፡ ሲፈስ ፡ አንድ ፡ የፋሺስት ፡ ወታደር ፡ በቆርቆሮ፡ ሲቀዳ ፡ አይቶ ፡ ያለፈውን ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ መከራ ፡ ሁሉ ፡ የሚያስ ረሳና ፡ የሚያሳዝን ፡ ነገር ፡ ስላጋጠመው ፡ የመረረ ፡ ልቅሶ ፡ እያለ ቀሰ ፡ ወደ ፡ ድሬ ፡ ዳዋ ፡ ይሮጥ ፡ ዠመር ። በኅሊናው ፡ ውስጥ ፡ ስለምንድነው ፡ ሰው ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ይህን ፡ ያኽል ፡ የጭካኔ ፡ ሥራ ፡ የሚሠራው ፡ ይገርማል ፤ ይልቁንም ፡ የወንድሙን ፡ ደም ፡ በቊና ፡ የሚሠፍረው ፡ በጣም ፡ ያሳዝናል ፡ ካለ ፡ በኋላ ፤ ከመንገዱ ፡ ወጣ ፡ ብሎ ፡ ካንዲት ፡ ቊጥቋጦ ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፡ በጕልበቱ ፡ ተንበር ክኮ ፤ «አቤቱ ፡ የዓለም ፡ መድኅኒት ፡ በሰፈራችሁት ፡ ቊና ፡ ትሰ ፈራላችሁ» ፡ ብለኸ ፡ ተናግረኻልና ፡ የበቀል ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ጠላ ቶቻችን ፡ በሰፈሩት ፡ ቊና ፡ እንዲሰፈሩ ፡ አድርጋቸው ፡ ብሎ ፡ ጸሎ ቱን ፡ ከጨረሰ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ይሮጥ ፡ ዠመር ።

ወዲያው ፡ ድሬ ፡ ዳዋ ፡ እንደ ፡ ደረሰ ፡ ያስታመመው ፡ ወዳጁ ፡ ከሰጠው ፡ ገንዘብ ፡ የመሣፈሪያ ፡ ወረቀት ፡ ገዝቶ ፡ በሦስተኛው ፡ ማዕርግ ፡ ባቡር ፡ ተጓዘ ።



የጣልያን ፡ ፋሽስት ፡ የግፍ ፡ አገዳደል ።

ነገር ፡ ግን ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ ለመሄድ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ የተሳፈሩት ፡ መንገደኞች ፡ በጣም ፡ አስጨነቁት ። ምክንያቱም ፡ እግሩና ፡ እጁ ፡ ሽባ ፡ በመሆኑ ፡ ፊቱ ፡ በቦምብ ፡ ተቃጥሎ ፡ የሚያስጠይፍ ፡ በመሆኑ ፡ ብዙዎች ፡ ሰዎች ፡ ምንስ ፡ ገንዘብ ፡ ቢኖረው ፡ ከዚህ ፡ ከቆማጣው ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ እንደምን ፡ ያስቀ ምጡናል ፡ በማለት ፡ ነው ። ሌሎቹም ፡ እጁና ፡ እግሩ ፡ ሽባ ፡ የሆነው ፡ የኢትዮጵያን ፡ ብርሃን ፡ ሙሶሊኒን ፡ ወግቶ ፡ ይሆናል ፡

ይኽንንስ ፡ ከዚህ ፡ አውርዶ ፡ በረሓ ፡ ውስጥ ፡ መጣል ፡ ነበር ፡ የሚሉም ፡ አሉ ። ከዚህም ፡ በቀር ፡ አንዳንዶቹ ፡ በሽታም ፡ ቢሆን ፡ እግዚአብሔር ፡ ያመጣበት ፡ ነው ፤ በቦምብም ፡ ተቃጥሎ ፡ እንደሆን ፡ ስላገሩ ፡ ነው ፡ ስለምንድነው ፡ እነዚህ ፡ ሰዎች ፡ ይኽ ንን ፡ ድኻ ፡ የሚያስጨንቁት ፡ እያሉ ፡ ያዝኑ ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ግን ፡ ላገሬና ፡ ለሕዝቤ ፡ መብት ፡ ስል ፡ ሽባና ፡ አንካሳ ፡ መልኬም ፡ የሚያጸይፍ ፡ ቢሆን ፡ ያገሬ፡ ሰዎች እንደ ፡ ጠላት ፡ መጠየፍና ፡ መጥላት ፡ አይገባቸውም ፡ ነበር ። መቼስ ፡ ምን ፡ ይደረጋል ፤ ጊዜ ፡ ያመጣው ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ከነሱ ፡ ለመለየት ፡ ሞጆ ፡ ሲደርስ ፡ ወረደና ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ በእግሩ ፡ ይጓዝ ፡ ዠመር ።

ቢሾፍቱ ፡ እንደ ፡ ደረሰ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ከወደ ፡ ፊቱ ፡ ሰው ፡ እንደሚያሳድደው ፡ እየተገላመጠ ፡ እንደ ፡ ነፋስ ፡ እየ ሮጠ ፡ ሲመጣ ፡ አየውና ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፤ ወንድሜ ፡ ምን ፡ ሆነኽ ፡ ነው ፡ ጠላት ፡ እንደሚያሳድደው ፡ ሰው ፡ የምትሮጥ ፡ እባክኽ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም ፡ ጠርቼ ፡ እለምንኻለሁና ፡ ንገረኝ ።

ሰውዬውም ፤ ርግጥ ፡ ነው ፡ ከወደ ፡ ኋላዬ ፡ ሞት ፡ ስለ ሚከተለኝ ፡ ነው ፡ እንደዚህ ፡ የምሮጠው ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጠርተኽ ፡ ስለ ፡ ለመንከኝ ፡ ጥቂት ፡ ደቂቃዎች ፡ ላጫውትኽ ፡ እፈቅዳለሁ ። ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ እንሆ ፡ አሁን ፡ ካዲስ ፡ አበባ ፡ መምጣቴ ፡ ነው ፤ አዲስ ፡ አበባ ፡ ተቃጠለች ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ምክንያቱ ፡ ምንድነው ፤

ሰውዬው ፤ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ ግራዚያኒ ፡ የሚባለውን ፡ የፋ ሽስት ፡ ጠቅላይ ፡ ሹም ፡ ትላንት ፡ የኢትዮጵያ ፡ ልጆች ፡ በቦ ምብ ፡ መቱት ። በዚህ ፡ ምክንያት ፡ ወንድም ፡ ሴትም ፡ ሕፃንም ቄስም ፡ መነኵሴም ፡ ቢሆን ፡ ግደሉት ፡ አቃጥሉት ፡ ጥረጉት ፡ የሚል ፡ የጭካኔና ፡ ያረመኔ ፡ ትእዛዝ ፡ ስለ ፡ ወጣ ፡ በየመን ገዱ ፡ የተገኘውን ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ ቢሆን ፡ ባካፋ ፡ በፋስ ፡ በዱላ ፡ እየደበደቡ ፡ እንደ ፡ ውሻ ፡ ሬሳ ፡ በመንገድ ፡ ሲጥሉት ፡ ብታይ ሰው ፡ መሆንኽን ፡ ትጠላለህ ፤ ከሁሉም ፡ የሚያሳዝን ፡ ነገር ፡ ያየሁት ፡ ፋሺስቶች ፡ ያንድ ፡ ሰው ፡ ቤት ፡ ሲያቃጥሉ ፡ ከው ስጡ ፡ አንዲት ፡ ሕፃን ፡ ልጅ ፡ ደንግጣ ፡ አባባ ፡ አባባ ፡ እያ

ለች ፡ ወደ ፡ ፋሺስት ፡ የጦር ፡ አለቃ ፡ ስትመጣ ፡ አንዱ ፡ የጦር ፡ አለቃ ፡ ሆዷን ፡ በጠመንዣ ፡ ሳንጃ ፡ ወግቶ ፡ አንጠልጥሎ ፡ ከእሳቱ ፡ ውስጥ ፡ ጣላት ፤ ይኸንን ፡ ባየሁ ፡ ጊዜ ፡ በኀዘን ፡ ራሴ ፡ ዞሮ ፡ ደሜ ፡ ስለ ፡ ፈላ ፡ በግርግር ፡ ውስጥ ፡ ያን ፡ ጨካኝ ፡ አረመኔ ፡ ፋሺስት ፡ በጩቤ ፡ ከደረቱ ፡ ላይ ፡ ወግቼ ፡ ሲወድቅ ፡ ጨለማው ፡ ስላገዘኝ ፡ ለማምለጥ ፡ በቃሁ ፡፡

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ዕሠይ ፡ ያገሬ ፡ ልጅ ፡ ደፋሩ ፡ አርበኛ ፡ እባክኽ ፡ ግራዚያኒ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ የቈሰለው ፡ ወይስ ፡ ሌሎችም ፡ የቈሰሉ ፡ ሹማምንት ፡ አሉ ፡፡

ሰውዬው ፤ ከሱ ፡ በቀር ፡ ሌሎች ፡ ብዙዎች ፡ መኳንንትና የጦር ፡ አለቆች ፡ ቈስለዋል ፡፡ ያሮፕላኑ ፡ ዋና ፡ ሹምማ ፡ ከዚያው ፡ ከደጋው ፡ ላይ ፡ ሞተ ፡ ይባላል ፤ ሌሎችም ፡ ብዙ ፡ የቈሰሉና ፡ የሞቱ ፡ አሉ ፡፡

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ስለምንድነው ፡ የከተማው ፡ ሕዝብ ፡ ባካፋ ሲቀጠቀጥ ፡ ዝም ፡ ብሎ ፡ ከመሞት ፡ የጠላቱን ፡ ጕረሮ ፡ አንቆ ፡ አይሞትም ፡ ኖሯልን ፡፡ ለምሳሌ ፤ ይኸው ፡ አንዱን ፡ ጨካኝ ፡ ጠላትኽን ፡ ገድለኸው ፡ ለማምለጥ ፡ በቃኽ ፡፡

ሰውዬው ፤ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝብ ፡ ነፃነቱን ፡ ከተገፈፈና ፡ ሞራሉ ፡ ከወደቀ ፡ በኋላ ፡ ከመግደል ፡ መሞትን ፡ እንደሚመርጥ ፡ አታውቅምን ፡፡

አቶ ፡ ተማቹ ፤ እባክኽ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ምን ፡ መስሎ ፡ ይታያል ፡፡

ሰውዬው ፤ አዲስ ፡ አበባ ፡ ገብተኽ ፡ ብታይ ፡ በውነት ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ መናገሻ ፡ ከተማ ፡ ነች ፡ ለማለት ፡ አትችልም ፡፡ ምክንያቱም ፡ የውስጡ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ተገልብጦ ፡ ትንሹ ፡ ትልቅ ፡ ሆኖ ፡ ሌባው ፡ የታመነ ፤ ታማኙ ፡ ከሓዲ ፡ ሆኖ ይታያል ፡፡ ይልቁንም ፡ በከተማው ፡ ሁሉ ፡ ነጭ ፡ ሰፍሮበት ፡ ያገሩ ፡ ተወላጅ ፡ የሰው ፡ ገንዘብ ፡ እንደ ፡ ሰረቀ ፡ ሰው ፡ በዋናው ፡ መንገድ ፡ ለመሄድ ፡ እየፈራ ፡ በየዛፉ ፡ ውስጥ ፡ ሲሹለከለክ ፡ ብታይ ፡ ታዝናለኽ ፡፡ አዲስ ፡ አበባን ፡ የቤት ፡ ቃጠሎና ፡ የተኰሱ ፡ ጢስ ፡ የወታደር ፡ ውካታ ፡ የሕዝቡ ፡ ለቅሶና ፡ የጭንቅ ፡ ጩኸት ፡ የሞት ፡ ጥላ ፡ ስላጨለማት ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የሚመጣበትን ፡ መከራ ፡ ከቤቱ ፡ ውስጥ ፡ እስረኛ ፡ ሆኖ ፡ ይጠባበቃል ፡፡

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ወይ ፡ ግሩም ፡ ሞት ፡ ላይቀር ፡ በገዛ ፡ ቤቱ እስረኛ ፡ ሆኖ ፡ የሚገድለውን ፡ ጠላት ፡ ከመጠበቅ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ተነሥቶ ፡ በጠላቱ ፡ ላይ ፡ አይወድቅበትምን ፤ ድር ፡ ቢያብር ፡ አንበሳ ፡ ያስር ፡ ይባላል ።

እንደ ፡ ርቢ ፡ በጎች ፡ ዝም ፡ ብሎ ፡ ለጠላት ፡ ከመመቸት ፡ ይልቅ ፡ የክብር ፡ ሞት ፡ መሞት ፡ አይሻልም ፡ ነበር ።

ሰውዬው ፤ በዚህ ፡ መፍረድ ፡ አይቻልም ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ በድል ፡ ሞራሉ ፡ ከተመታና ፡ ምግባሩ ፡ ከወደቀ ሃይማኖቱ ፡ ከጐደለ ፡ ወዲህ ፡ ስንኳን ፡ ሰው ፡ የገዛ ፡ ጥላውን ፡ ይፈራል ። ጠላቱን ፡ የሚያጠቃበት ፡ ምቹ ፡ ምክንያት ፡ እንኳ ፡ ቢያጋጥመው ፡ ምንም ፡ አይጠቀምበትም ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ እንግዴህ ፡ አትፍረዱ ፡ ይፈረድባችኋል ፡ የተባለው ፡ እንዳይደርስብኝ ፡ እግዚአብሔርን ፡ እየለመንኹ ፡ በከተማው ፡ ውስጥ ፡ አልፌ ፡ ሚስቴንና ፡ ልጆቼን ፡ ለማየት ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ብርሃን ፡ ልጓዝ ፡ አንተም ፡ እኔን ፡ ለማጫወት ፡ ስትል ፡ ጊዜኽን ፡ በማጥፋትኽ ፡ በጣም ፡ አመሰግንኻለሁ ፤ እግዚአብሔር ፡ መንገድኽን ፡ ያቅናልኽ ፡ ደኅና ፡ ሰንብት ፡ ብሎ ፡ ሰላምታ ፡ ሰጠው ።

ሰውዬውም ፤ እግዚአብሔር ፡ አንተንም ፡ ከቤተ ፡ ሰቦችህ ፡ በደኅና ፡ እንዲያገናኝኽ ፡ እመኛለሁ ። ደኅና ፡ ሰንብት ፤ ነገር ፡ ግን ፡ አንድ ፡ የማሳስብኽ ፡ ዋና ፡ ነገር ፡ በከተማው ፡ ውስጥ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ አትበል ፡ ቶሎ ፡ ብለኽ ፡ ውጣ ፡ ምክንያቱም ፡ ይኽንን ፡ ሰውነትኽን ፡ ሲያዩ ፡ ደዌ ፡ ሥጋ ፡ የያዘኽ ፡ መስሏቸው ፡ ከድኾች ፡ ጋራ ፡ ካንድ ፡ ቤት ፡ ውስጥ ፡ ዘግተው ፡ በችጋርና ፡ በሥቃይ ፡ ይገድሉኻል ፤ እንግዴህ ፡ እኔም ፡ ወደ ፡ ፊቴ ፡ ልሩጥ ፡ አንተም ፡ እግዚአብሔር ፡ ይጠብቅኽ ፡ ብሎት ፡ ይበር ፡ ዠመር ።

አቶ ፡ ተማቹም ፡ ምርኵዙን ፡ ይዞ ፡ አሮጌ ፡ ካስኩን ፡ እራሱ ላይ ፡ አድርጎ ፡ እያነከሰ ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ ተጓዘ ። ካዳማ ፡ አቃቂ ፡ በሦስት ፡ ቀን ፡ ደረሰ ፡ ካቃቂ ፡ ማለዳ ፡ ተነሥቶ ፡ ከእኵለ ፡ ቀን በኋላ ፡ ባሥር ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ገባ ። አቶ ፡ ተማቹ ፡ አዲስ አበባ ፡ በውነት ፡ ተገልብጣ ፡ ሌላ ፡ መልክ ፡ አውጥታ ፡ በማየቱ ፡ ቆሞ ፡ እየተመለከተ ፡ ዕንባው ፡ ከፈሰሰ ፡

በኋላ ፡ በፍል ፡ ውሃ ፡ ሜዳ ፡ በኩል ፡ አለፈ ። ከክቡር ፡ ራስ፡ ቢትወደድ ፡ ተሰማ ፡ ቤት ፡ አንሥቶ ፡ እስከ ፡ ክቡር ፡ ራስ ፡ ብሩ፡ ቤት ድረስ ፡ ሜዳው ፡ በሙሉ ፡ ታንክና ፡ የጦር ፡ ካሚዎን ፡ ሞልቶት በማየቱ ፡ ሰውነቱ ፡ ተሸበረ ። በኀሊናው ፡ ያገሬ ፡ ልጆች ፡ ምን ያኽል ፡ አልቃችሁ ፡ ይሆን ፡ እያለ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ተጓዘ ።

ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ቅጥር ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፡ የቤተ ፡ መንግሥቱን ፡ ግንብ ፡ ሲመለከት ፡ የመንግሥቱ ፡ ሰንደቅ ፡ ዐላማ ፡ ተነሥቶ ፡ የጠላት ፡ ባንዲራ ፡ ሲውለበለብበት ፡ አየ ።

በዚየ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ አእምሮው ፡ በኀዘን ፡ ጠፍቶ ፡ እየጮኸ ፡ የመረረ ፡ ለቅሶ ፡ እያለቀሰ ፡ ያገሬ ፡ ክብር ፡ የነፃነቴ ፡ ምልክት ፡ ወዴት ፡ አውርደው ፡ ጣሉሽ ፡ በፋሺስት ፡ እግር ፡ ተረገጥሽን ፡ ይኸን ፡ ውርደት ፡ ሳያይ ፡ የሞተ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ዕድለኛ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ዘወር ፡ አለና ፡ ቢመለከት ፡ ምንም ፡ ሰው ፡ ባጠገቡ ፡ ስለሌለ ፡ ዕንባውን ፡ ጠራርጎ ፡ እንግዴህ ፡ መሸ ፡ በየካ ፡ ቅዱስ፡ ሚካኤል ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መቃብር ፡ ቤት ፡ አድሬ ፡ ወደ ፤ ደብረ ፡ ብርሃን ፡ ማለዳ ፡ ልሂድ ፡ ብሎ ፡ ምርኰዙን ፡ ይዞ ፡ ባውራው ፡ ጐዳና ፡ ሲጓዝ ፡ የፋሺስቶችን ፡ እብሪትና ፡ ደስታ ፡ ዘፈን ፡ የኢትዮጵያን ፡ ልጆች ፡ ፍራትና ፡ ጭንቀት ፡ እያየ ፡ በካስኩ ፡ ፊቱን ፡ አልብሶ ፡ የመረረ ፡ ለቅሶ ፡ እያለቀሰ ፡ ከቅዱስ ፡ ሚከኤል ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ደረሰ ።

ከዚያም ፡ ቆሞ ፡ ትንሽ ፡ ጸሎት ፡ ካደረገ ፡ በኋላ ፡ ከደጀ ፡ ሰላሙ ፡ አጠገብ ፡ ተኰራምቶ ፡ መኰራውን ፡ ሲያስብ ፡ እንቅልፍ ፡ ይዞት ፡ ወገግ ፡ አለ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ተነሥቶ ፡ በሾላ ፡ በር ፡ በኩል ፡ ወደ ፡ ደብረ፡ ብርሃን ፡ ተጓዘ ።

የአቶሞቢል ፡ መንገድ ፡ የወታደር ፡ መመላለሻ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አደጋ ፡ እንዳይደርስበት ፡ በቀድሞው ፤ የእግር ፡ መንገድ ፡ በኩል ፡ ምርኰዙን ፡ ይዞ ፡ እየተጓዘ ፡ ሰንዳፋ ፡ አጠገብ ፡ ሲደርስ ፡ መሸበትና ፡ ሌሊቱን ፡ የሚያሳልፍበት ፡ አንዲት ፡ ጥግ ፡ ሲፈልግ ፡ በድንገት ፡ አንድ ፡ ጐፈሬያም ፡ ድርብ ፡ ዝናር ፡ የታጠቀና ፡ ዲሞትፎር ፡ ጠመንዣ ፡ የያዘ ፡ ወታደር ፡ አጋጠመው ፤ ያም ፡ ወታደር ፡ አቶ ፡ ተማቹን ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ ከዚህ ፡ ምን ፡ ታደርጋለኽ ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ እኔ ፡ አንድ ፡ ድኻ ፡ ለመለመን ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ ሂጄ ፡ ምንም ፡ ሳላገኝ ፡ ስለቀረሁ ፡ አሁን ፡ መሽቶብኝ ፡ ሌሊቱን ፡ የማሳልፍበት ፡ ጥጋት ፡ እፈልጋለሁ ።

ወታደሩ ፤ አገርኽ ፡ ወዴት ፡ ነው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ አገሬ ፡ ተጕለት ፡ ነው ፡ የምኖርበት ፡ ግን ፡ ደብረ ፡ ብርሃን ፡ አጠገብ ፡ ከከተማው ፡ ወጣ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ቡሎ ፡ ወርቄ ፡ ከሚወስደው ፡ መንገድ ፡ አንድ ፡ ትልቅ ፡ ዛፍ ፡ በላይ ፡ ነው ።

ወታደሩ ፤ ዐወቅሁት ፡ ካቶ ፡ ተማቹ ፡ ቤት ፡ አጠገብ ፡ ሳይሆን ፡ አይቀርም ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ አዎን ፡ ዐውቅኸው ፡ ከሱ ፡ ቤት ፡ አጠገብ ፡ ነው ።

ወታደሩ ፡ ስምኽ ፡ ማን ፡ ይባላል ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ስሜ ፡ ጕድ ፡ አለ ፡ ሸዋ ፡ ይባላል ።

ወታደሩ ፤ ያቶ ፡ ተማቹ ፡ ጭሰኛ ፡ ነህን ፡ ወይስ ፡ ጎረቤት ፡ ነኽ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ አንድ ፡ ችጋረኛ ፡ ድኻ ፡ ስለ ፡ ሆንኩ ፡ ባቅራቢያው ፡ ጐጆ ፡ ቀልሼ ፡ በምጽዋት ፡ እኖራለሁ ። ይልቁንም ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ስለሚዘከረኝ ፡ የዕለት ፡ እራት ፡ ሳላጣ ፡ ጊዜዬን ፡ በዚሁ ፡ አሳልፋለሁ ፤ እባክህ ፡ ወንድሜ ፡ ደፈረኝ ፡ አትበለኝና ፡ ካቶ ፡ ተማቹ ፡ ከተለያየሁ ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ ሆነኝ ፤ እሱም ፡ ባለቤቱም ፡ ልጆቹም ፡ ደኅና ፡ መሆናቸውን ፡ አልሰማኽምን ፡ ብትነግረኝ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኝ ፡ ነበር ።

ወታደሩ ፡ ስለ ፡ ጠየቅኸኝ ፡ መልስ ፡ የሚያሳዝን ፡ በመሆኑ ፡

ይቅርታህን ፡ እየለመንኩ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ በውጋዴ ፡ በኩል ፡ ከምዕራብ ፡ ጦር ፡ ጋራ ፡ ዘምቶ ፡ በአርበኝነት ፡ ከጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ከሁለቱ ፡ ትልልቆች ፡ ወንዶች ፡ ልጆቱ ፡ ጋራ ፡ ሞቷል ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ የመረረ ፡ ለቅሶ ፡ እያለቀሰ ፡ እባክህ ፡ ወንድሜ ፡ ሚስቱና ፡ የቀሩት ፡ ልጆቹ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ሆነው ፡ ይሆን ።

ወታደሩ ፤ ወሬያቸውን ፡ ከሰማሁ ፡ ብዙ ፡ ቀኔ ፡ ነው ። ነገር ፡ ግን ፡ ሚስቱ ፡ የባሏን ፡ ሞት ፡ እንደ ፡ ተረዳች ፡ በቤቷ ፡ በኩል ፡ ሳልፍ ፡ ጥቍር ፡ ልብስ ፡ ለብሳ ፡ በጣም ፡ ተጐሳቍላ ፡ ከስታ ፡ ጠቍራ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ልጅና ፡ አንድ ፡ ትንሽ ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ አስከትላ ፡ ስትሄድ ፡ አይቻት ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ባሏስ ፡ ስላገሩ ፡ ከነልጆቹ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፡ እንግዴህ ፡ እሷ ፡ ከነልጆቿ ፡ የዚህን ፡ ዓለም ፡ ኑሮ ፡ በጠላት ፡ መከከል ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ትዘልቀው ፡ ይሆን ፡ እያለ ፡ ዕንባው ፡ ይፈስ ፡ ዠመር ።

አርበኛው ፡ እባክህ ፡ አቶ ፡ ጉድ ፡ አለ ፡ ሸዋ ፡ አቶ ፤ ተማቹን ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ትወደው ፡ ኖሯል እንደዚህ ፡ የምታለቅሰው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ እንደ ፡ ራሴ ፡ አድርጌ ፡ እወደው ፡ ነበር ። ምክንያቱም ፡ በጣም ፡ ቸር ፡ ሰው ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ በችግሬ ፡ ጊዜ ፡ ከሱ ፡ ለምኜ ፡ አንድ ፡ ቀንም ፡ አፍሬ ፡ አላውቅም ፤ ስለዚህ ፡ እሱ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ቤቱ ፡ መፈታቱንና ፡ ልጆቹ ፡ መቸገራቸውን ፡ ሳስብ ፡ የመረረ ፡ ኀዘን ፡ ይሰማኛል ።

ወታደሩ ፡ ድመት ፡ ያው ፡ በገሌ ፡ ነው ፡ አለች ፡ ይባላል ። አንተም ፡ መቼም ፡ መች ፡ ኑሮህ ፡ ያው ፡ መለመን ፡ ነው አሁንም ፡ ቢሆን ፡ ቸር ፡ ሰው ፡ አይታጣም ። አቶ ፡ ተማቹም ፡ በሚገባ ፡ ስላገሩ ፡ በክብር ፡ ሞት ፡ ሞተ ፤ ሚስቱም ፡ መብልና ፡ መጠጥ ፡ ካለ ፡ ሴቷቱ ፡ የተዋበች ፡ ቈንገር ፡ ናት ፡ ባል ፡ አታጣም ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ ሁለተኛ ፡ ባል ፡ ታገባ ፡ አይመስለኝም ፡ ጌታዬ ፡ እኔ ፡ እንደማውቀው ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያሉ ፡ ባልና ፡ ሚስት ፡ ይመስሉዎታል ። እሱ ፡ ከሷ ፡ በቀር ፤ እሷም ፡ ከሱ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ ያለ ፡ አይመስላቸውም ፤ ስለዚህ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ታገባለች ፡ ብዬ ፡ አልጠረጥርም ።

አርበኛው ፤ አይምሰልኽ ፡ አቶ ፡ ጉድ ፡ አለ ፡ ሸዋ ፡ ለራሷ ፡ ሕይወት ፡ ለማሰብ ፡ እንኳ ፡ ባይሆን ፡ ጕሽ ፡ ለልጅዋ ፡ ተዋጋች ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ እነዚያን ፡ ሕፃናት ፡ በችጋር ፡ ሲሞቱ ፡ ከማየት ፡ ማንኛውንም ፡ ውርደት ፡ መጣስ ፡ ግዴታ ፡ ይሆንባታል ። አሁንስ ፡ ያቶ ፡ ተማቹን ፡ ቤተ ፡ ሰቦች ፡ ወሬ ፡ እንተውና ፡ እንግዴህ ፡ አንተ ፡ ቤትኽ ፡ ከዚያው ፡ ካቶ ፡ ተማቹ ፡ ቤት ፡ አጠገብ ፡ ከሆነ ፡ ማንኛውንም ፡ ነገር ፡ እየሰለልክ ፡ ቡሎ ፡ ወርቄ ፡ ድረስ ፡ እየመጣህ ፡ እንድትነግረኝ ፤ በውነት ፡ ላገርህ ፡ መርዳት ፡ ካሰብሕ ፡ እንዳንተ ፡ ያለ ፡ ድኻ ፡ በሽተኛ ፡ በማንኛውም ፡ ሥፍራ ፡ ለመለመን ፡ ስትሄድ ፡ ልታውቀው ፡ ትችላለህ ፡ የሚጠረጥርህ ፡ ሰው ፡ የለም ፤ እኛም ፡ በገንዘብ ፡ እንረዳኻለን ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ሰልዬ ፡ ለማነው ፡ የምነግረው ፡ መሬታችን ፡ ለጠላት ፡ ሆኖ ፡ የለምን ።

አርበኛው ፤ አይዞህ ፡ አትፍራ ፡ ተስፋም ፡ አትቍረጥ ፤ ጠላት ፡ የነገሠው ፡ በመንገድና ፡ በከተማ ፡ ላይ ፡ ነው ። የኢትዮጵያ ፡ መሬትና ፡ ሰንደቅ ፡ ዐላማችን ፡ ባርበኞች ፡ እጅ ፡ ነው ፤ ፍርዳችንም በንጉሠ ፡ ነገሥታችን ፡ እጅ ፡ በዓለም ፡ መንግሥታት ፡ ፊት ፡ ቀርቧል ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ንጉሠ ፡ ነገሥታችን ፡ አሉ ፡ አልሞቱምን ። አርበኛው ፤ አልሞቱም ፡ ስላገራቸው ፡ በዓለም ፡ መንግሥታት ፤ ፊት ፡ በፖለቲካ ፡ ጦርነት ፡ ይዋጋሉ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ወንድሜ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱን ፡ ወሬ ፡ ስላል ሰማኸኝ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸር ፡ ወሬ ፡ ያሰማህ ። እንግዲያስ ፡ የኢት ዮጵያ ፡ ነፃነት ፡ ጠፍቶ ፡ አይቀርም ፤ እኔም ፡ በተቻለኝ ፡ አኳኋን ፡ አገሬን ፡ ለመርዳት ፡ የተዘጋጀሁ ፡ ነኝ ። እንግዴህ ፡ ከዚያው ፡ ከተ ባባልነው ፡ ቦታ ፡ ድረስ ፡ እንፈላለጋለን ፤ እግዚአብሔር ፡ በደኅና ፡ ለመገናኘት ፡ ያብቃን ። አርበኛው ፡ አንተም ፡ እግዚአብሔር ፡ በደ ኅና ፡ ያግባህ ፡ እንደ ፡ ችሎታህ ፡ መጠን ፡ አገርህን ፡ አትርሳ ፡ ተባብለው ፡ ሁለቱም ፡ መንገዳቸውን ፡ ቀጠሉ ።

ምዕራፍ ፡ ፮ ።

በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ዐርብ ፡ ጧት ፡ ባ፰ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ደብረ ፡ ብርሃን ፡ ከተማ ፡ ደረሰ ። አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከተማውን ፡ በማየቱ ፡ የኀዘንና ፡ የደስታ ፡ ዕንባ ፡ ካይኑ ፡ ይፈነዳ ፡ ነበር ።

ምክንያቱም ፡ ስለ ፡ ሁለት ፡ ነገሮች ፡ ነው ፤ አንደ ኛው ፡ ጽጌ ፡ ረዳን ፡ ለማየት ፡ በመቃረቡ ፡ የደስታና ፡ የሰቀቀን ፤ ዕንባ ፡ አነቀው ። ሁለተኛው ፡ እሱ ፡ እንደዚህ ፡ ተበላሽቶ ፡ ጨርሶ ፡ ተለውጦ ፡ ሽባ ፡ አንካሳ ፡ ሆኖ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ስታየው ፡ ምን ፡ ስሜት ፡ ይሰማት ፡ ይሆን ፡ በማለት ፡ ነው ። ይልቁንም ፡ የደብረ ፡ ብርሃን ፡ ከተማ ፡ በፋሺስት ፡ ወታደሮች ፡ ተጨንቃ ፡ ያገሩ ፡ ተወላጆች ፡ ቤታ ቸውን ፡ ለቀው ፡ አዲስ ፡ ቤቶች ፡ ተሠርተውበት ፡ ካዲስ ፡ አበባ ፡ አሥ መራ ፡ የሚመላለሰው ፡ የጦር ፡ ካሚዎን ፡ ታንክ ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ እንደ ፡ ጐርፍ ፡ ሲያልፍ ፡ የፋሺስትን ፡ መኳንንት ፡ እብሪትና ፡ ጥጋብ ፡ ኩራት ፡ በማየት ፡ የወታደሮቹን ፡ የጦር ፡ ሙዚቃና ፡ ዘፈን ፡ በመ ስማት ራሱ ፡ ዞሮ ተጨነቀ ። በትሩን ፡ ተደግፎ ፡ አገጩን ፡ በእጁ ይዞ ፡ አገሩ ፡ ስትሞት ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ያልሞተ ፡ የተረገመ ፡ ነው ። በጀነጋብ ፡ ወንዝ ፡ ውስጥ ፡ ወድቃችሁ ፡ የቀራችሁ ፡ ወንድሞ ቹና ፡ ልጆቹ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያላችሁ ፡ ዕድለኞች ፡ ናችሁ ፤ ወይኔ ፡ የኔ ፡ መጨረሻ ፡ ምን ፡ ይሆን ፡ ብሎ ፡ ምርኩዙን ፡ ይዞ ፡ የተበጫ ጨቀ ፡ ልብሱን ፡ ለብሶ ፡ አሮጌ ፡ ከስኩን ፡ ከራሱ ፡ ላይ ፡ ደፍቶ ፡ ወደ ፡ ቤቱ በሚወስደው ፡ መንገድ ፡ አቀና ።

ከዚያም ፡ እንደ ፡ ደረሰ ፡ ከቅጥሩ ፡ ውጭ ፡ ከዋናው ፡ በር ፡ አጠገብ ፡ ቆሞ ፡ ሲመለከት ፡ ቤቱ ፡ ታድሶ ፡ ቀለም ፡ ተቀብቶ ፡ ሌሎቹም ፡ ክፍሎት ፡ ተጨምረውበት ፡ አምሮ ፡ አየው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ወይ ፡ ግሩም ፡ እኔ ፡ ብቻ ፡ ተበላሽቻለሁ ፡ እንጂ ፡ ቤቴስ ፡ አምራለች ፡ እያለ ፡ ቤቱን ፡ በሩቅ ፡ ከተመለከተ ፡ በኋላ ፡ ዘወር ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ጐን ፡ ቢመለከት ፡ አንድ ፡ ማለፊያ ፡ ፈረስ ፡ በፈረንጅ ፡ ዕቃ ፡ ተጭኖ ፡ ታስሮ ፡ አየ ።



አቶ ፡ ተማቹ ፡ በቤት ፡ በራፍ ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡ ሲለምን ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ምን ፡ ይሆን ፡ ብሎ ፡ ደነገጠ ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ይኸንን ፡ ታምር ፡ ለማወቅና ፡ ለማየት ፡ ቢያስብ ፡ በሩ ፡ ስለ ፡ ተዘጋ ፡ ምንም ፡ ለማየት ፡ አልቻለም ። ስለዚህ ፡ ከውስጥ ፡ ሰው ፡ ለመጠየቅ ፡ እንዲችል ፡ ስለ ፡ ወላዲተ ፡ አምላክ ፡ የራበኝ ፡ በሽተኛ ፡ ድኻ ፡ ከዚህ ፡ ቆሚያለሁና ፡ ተዘከሩኝ ፡ እያለ ፡ ጮኾ ፡ ይለምን ፡ ዠመር ፤

ልጁ ፡ ተዋበች ፡ ሰምታ ፡ በር ፡ ከፍታ ፡ ብትወጣ ፡ አንድ ፡ በሽተኛ ፡ ድኻ ፡ ሰው ፡ ከቅጥሩ ፡ በራፍ ፡ ቆሞ ፡ ሲለምን ፡ አይታ ፡ ወደ

ናቷ ፡ ተመልሳ ፡ እማማ ፡ አንድ ፡ በጣም ፡ የሚያሳዝን ፡ በሽተኛ ፡ ድኻ ፡ ከውጭ ፡ ቆሞ ፡ ይለምናልና ፡ ምጽዋት ፡ ስጪው ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ አንድ ፡ ሶልዲ ፡ ስጠቻትና ፡ ይዛ ፡ ሄዳ ፡ ሰጠችው ።

አቶ ፡ ተማቹም ፡ ሶልዲውን ፡ ተቀብሎ ፡ ቢመለከተው ፡ የጣልያንን ፡ ንጉሥ ፡ መልክ ፡ አየና ፡ ወረወረው ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ተዋበች ፡ ስለ ፡ ምንድነው ፡ ምጽዋት ፡ ብሰጥኽ ፡ የደጉ ፡ የገናናው ፡ ቢክቶር ፡ ዐማኑኤል ፡ መልክ ፡ ያለበትን ፡ ገንዘብ ፡ የምትወረውረው ፡ ብላ ፡ ተቈጣችው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ አትቆጪ ፡ ልጄ ፡ እኔ ፡ ቤት ፡ ንብረት ፡ ሚስት ፡ ልጅ ፡ የሌለኝ ፡ ድኻ ፡ የበሰለ ፡ ነገር ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ የምወስድ ፡ እንጂ ፡ ገንዘብ ፡ ተቀብዬ ፡ አላውቅም ፤ ስለዚህ ፡ አንቺ ፡ አዛኝ ፡ እርኅርኅት ፡ ልጅ ፡ ከሆንሽ ፡ በገንዘቡ ፡ ፋንታ ፡ አንዲት ፡ ቍራሽ ፡ እንጀራና ፡ የምለምንበትንም ፡ ከረጢት ፡ የማስርበት ፡ ገመድ ፡ ብትሰጪኝ ፡ አመሰግንሻለሁ ።

ተዋበች ፡ ወደ ፡ ቤቷ ፡ እየሮጠች ፡ ተመልሳ ፡ እማማ ፡ ይህ ፡ ድኻ ፡ በጣም ፡ ያሳዝናል ። ፊቱ ፡ በበሽታ ፡ ተበላሽቶ ፡ ጠቍሯል ፡ እጁም ፤ እግሩም ፡ ሽባ ፡ ነው ። ከችግሩ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ዕንባው ፡ እንደ ፡ ውሃ ፡ ይፈሳል ፤ ይህችን ፡ ገንዘብ ፡ ብሰጠው ፡ ወርውሮ ፡ ጣላት ። እኔም ፡ የለማኝ ፡ ኵሩ ፡ መስሎኝ ፡ ብቈጣው ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ እኔ ፡ አንድ ፡ ድኻ ፡ ቤት ፡ ንብረት ፡ ሚስት ፡ ልጅ ፡ የሌለኝ ፡ ገንዘብ ፡ ምን ፡ ያደርግልኛል ፡ ብትፈቅጂ ፡ የበሰለ ፡ ነገርና ፡ ለመለመኛዬ ፡ ስልቻ ፡ ማሰሪያ ፡ የሚሆን ፡ ገመድ ፡ አምጪልኝ ፡ አለኝ ፡ እማማ ፡ ይኽ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያሳዝናል ። እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ልቤን ፡ የነካው ፡ ድኻ ፡ ከዚህ ፡ ቀደም ፡ አላጋጠመኝም ፤ ይልቁንም ፡ በጣም ፡ ያሳዘነኝ ፡ እኔን ፡ ቀና ፡ ብሎ ፡ ባየኝ ፡ ቍጥር ፡ ዕንባው ፡ ይፈሳል ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ መልካም ፡ ልብ ፡ ስላለሽ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመሰግነዋለሁ ። ለሰው ፡ ልጅ ፡ ለድኻ ፡ ወንድሙ ፡ ከመራራት ፡ በቀር ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ምግባር ፡ የለም ፡ አንቺማ ፡ ያቶ ፡ ተማቹ ፡ ልጅ ፡ ሆንሽ ፡ ምን ፡ ታደርጊ ፡ አባትሽ ፡ በበረሓ ፡ በምድረ ፡ በዳ ፡ ከነልጆቹ ፡ ውሃ ፡ ውሃ ፡ ሲል ፡ ወድቆ ፡ የለምን ። እንደዚህ ፡ ያለ ፡ መከራ ፡ ዘወትር ፡ ከፊትሽ ፡ ሲታይሽ ፡ ለችግረኛ ፡ ስታዝኚ ፡ እንደምትኖሪ ፡ የታወቀ ፡ ነው ።

ተዋበች ፡ አዎን ፡ እማማ ፡ እኔም ፡ ይህ ፡ ድኻ ፡ ቤት ፡ ንብረት ፡ ሚስት ፡ ልጅ ፡ ስለሌለኝ ፡ ገንዘብ ፡ አልፈልግም ፡ ሲለኝ ፡ አባባ ፡ ቤቱን ፡ ንብረቱን ፡ ልጆቹን ፡ አንቺን ፡ የሚወድሽ ፡ ሚስቱን ፡ ጥሎ ፡ በበረሓ ፡ የወደቀው ፡ ትዝ ፡ ብሎኝ ፡ አዘንኩ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ተዪው ፡ እርሽው ። ይኸንን ፡ የመረረ ፡ ኑሮ ፤ ይህ ፡ ዓለም ፡ በማር ፡ የተሸፈነ ፡ መርዝ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ዝም ፡ ብሎ ፡ ልብ ፡ እያወቀ ፡ መዋጥ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ መመራመር ፡ አያስ ፈልግም ፤ አሁንስ ፡ እንቺ ፡ ይኸንን ፡ ዳቦ ፡ ስጪው ።

ተዋበች ፡ ደግሞ ፡ ለመለመኛው ፡ ከረጢት ፡ ማሰሪያ ፡ ገመድ ፡ ለምኖኛል ፡ ብርገደሌ ፡ ማሪዮ ፡ ቅድም ፡ ካመጡት ፡ ገመድ ፡ ትንሽ ፡ ስጪኝ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ይሁን ፡ አምስት ፡ ክንድ ፡ የሚሆን ፡ ቍረ ጪና ፡ ውሰጂለት ።

ተዋበች ፡ ገመዱን ፡ ቈርጣ ፡ ዳቦውን ፡ ይዛ ፡ ሄደችና ፡ ለድኻው ፡ ሰጠችው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይስጥሽ ፡ በጸሎቴ ፡ እንዳስ ማሽ ፡ ስምሽ ፡ ማነው ።

ተዋበች ፤ እኔ ፡ ተዋበች ፡ ተማቹ ፡ እባላለሁ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ የክርስትና ፡ ስምሽ ፡ ማነው ።

ተዋበች ፤ ወለተ ፡ ማርያም ፡ ነው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ እናት ፡ አለችሽን ።

ተዋበች ፤ አዎን ፡ እናት ፡ አለችኝ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ የናትሽ ፡ ስም ፡ ማነው ።

ተዋበች ፤ የናቴ ፡ ስም ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ነው ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ አባት ፡ አለሽን ፤

ተዋበች ፤ አባቴ ፡ ሞቷል ፡ እንጂ ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ አባት ፡ ነበረኝ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ማን ፡ ይባላል ፤

ተዋበች ፤ አባቴ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ይባላል ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ አባትሽ ፡ የሞተው ፡ ታሞ ፡ ነውን ።

ተዋበች ፤ በሕመም ፡ አይደለም ፡ ስላገሩ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ከሁለት ፡ ልጆቹ ፡ ጋራ ፡ ወድቆ ፡ ቀረ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ እናትሽ ፡ ከባሏ ፡ ሞት ፡ ወዲህ ፡ ሳታገባ ፡ ተቀም ጣለች ፡ ወይስ ፡ ባል ፡ አግብታለች ።

ተዋበች ፤ የዚህን ፡ ነገር ፡ ማነው ፡ ያስለቀሰኝል ፤ ቢሆንም ፡ አንተ ፡ ስለ ፡ ጠየቅኸኝ ፡ አጫውትኻለሁ ። እናቴ ፡ የባሏን ፡ ሞት ፡ ከተረዳች ፡ ወዲህ ፡ እስከ ፡ ስምንት ፡ ወር ፡ ያህል ፡ በጣም ፡ በሚያሳዝን ፡ ችግርና ፡ ኀዘን ፡ ላይ ፡ ነበረች ፤ ዘወትር ፡ ጧት ፡ በማለዳ ፡ ተነሥታ ፡ እኔንና ፡ አሸብርን ፡ ይዛ ፡ ከበሬሳ ፡ አፋፍ ፡ ድረስ ፡ ሄደን ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ጋሻና ፡ ጦሩን ፡ ይዞ ፡ ሁለቱን ፡ ልጆቹን ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ አድርጎ ፡ ላይናችን ፡ እስኪርቅ ፡ ድረስ ፡ በአንጐለላ ፡ ሜዳ ፡ ወደ ፡ ኋላው ፤ ሳይመለከት ፡ የሚ ወዳት ፡ ሚስቱንና ፡ ልጆቹን ፡ ጥሎ ፡ የሄደባቸውን ፡ ተራሮችና ፡ ሜዳ ምች ፡ እያየች ፡ ወዳጄ ፡ በዕንባዬ ፡ ጭጋግ ፡ ውስጥ ፡ ትታየኛለኽ ፡ እኔን ፡ ደካማ ፡ ወዳጅኽን ፡ ቤትኽን ፡ ንብረትኽን ፡ ልጆችኽን ፡ ዘወር ፡ ብለኽ ሳታይ ፡ ወደ ፡ ሞት ፡ ጕዳና ፡ ካይኔ ፡ እስክትሰወር ፡ ድረስ ፡ ስትጓዝ ፡ ያየ ኹኽ ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፡ ሕይወቴ ፡ አይረሳኝም ፡ እያለች ፡ ከመሬት ፡ ወድቃ ፡ ታለቅስ ፡ ነበር ፤ እቤቷም ፡ ገብታ ፡ እንደዚሁ ፡ ማልቀስ ፡ መተ ከዝ ፡ መሬት ፡ መቈርቈር ፡ ብቻ ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ከዚያ ፡ በኋላስ ፡ እንደ ምን ፡ ሆነ ፡ ተዋበች ፤ ከዚያ ፤ በኋላማ ፡ አንድ ፡ የፋሺስት ፡ ሹም ፡ ብርገደሌ ፡ ማሪዮ ፡ የሚባል ፡ የኛን ፡ ቤት ፡ ከሁሉም ፡ ቤት ፤ የተሻለ ፡ ነው ፡ በማለት ፡ እናቴንና ፡ እኔን ፡ አሸብርን ፡ አስወጥቶ ፡ ገባበት ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ እናንተ ፡ ወዲት ፡ ወደቃችሁ ።

ተዋበች ፤ እኛማ ፡ ወደ ፡ ጕረቤት ፡ ተዳብለን ፡ ተቀመጥን ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ በጣም ፡ የሚገርም ፡ ነገር ፡ ነው ፡ ታዲያ ፡ እንደ ምን ፡ ተመልሳችሁ ፡ ወደ ፡ ቤታችሁ ፡ ገባችሁ ።

ተዋበች ፤ እናቴ ፡ ከጎረቤት ፡ ተቀምጣ ፡ ጧትና ፡ ማታ ፡ ለኛ ፡ ምግብ ፡ ለመፈለግ ፡ ስትወጣና ፡ ስትገባ ፡ ይኸው ፡ ብርገደሌ ፡ ማሪዮ ፡ አይቷት ፡ ኖሮ ፡ ወደዳትና ፡ ጎረቤቶቹን ፡ ሁሉ ፡ እየላከ ፡ ላግባሽ ፡ ብሎ ፡ ያስቸግራት ፡ ዠመር ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ እባክሽ ፡ መጨረሻው ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ሆነ ፡ ዕንቢ ፡ ብላ ፡ ቀረች ፡ ወይስ ፡ አገባችው ።

ተዋበች ፤ ምንም ፡ ቢሆን ፡ አላደርገውም ፡ በማለት ፡ ጨክና ፡ ነበር ። እንዲያውም ፡ ልጆቼ ፡ እንደ ፡ ሞቱ ፡ ይሙቱ ፡ እንጂ ፡ እኔ ፡ ጥያቸው ፡ እጠፋለሁ ፡ ብላ ፡ አስባ ፡ ነበር ። ነገር ፡ ግን ፡ በሷ ፡ ምክንያት ፡ ጎረቤቷን ፡ ሁሉ ፡ ለማስፈጀትና ፡ እኛንም ፡ አባ

ታችን ፡ ስላገሩ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ሞተ ፡ እነዚህ ፡ ልጆች ፡ ለፋሺስት ፡ መንግሥት ፡ ተቃራኒ ፡ ዘሮች ፡ ናቸውና ፡ ሳያድጉ ፤ መፍጀት ፡ ነው ፡ እያለ ፡ ስላስወራ ፡ ከሁለት ፡ መጥፎ ፡ ነገር ፡ አን ዱን ፡ መምረጥ ፡ ግዴታ ፡ ቢሆንባት ፡ ጐሽ ፡ ለልጅዋ ፡ ተወጋች ፡ እንደሚባለው ፡ እኛን ፡ ከማስገደል ፡ ጎረቤቶቿን ፡ ከማስፈጀት ፡ ያለውድ ፡ በግድ ፡ እሱን ፡ ማግባት ፡ መረጠች ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ የሚገርም ፡ ነገር ፡ ነው ፤ የባሏን ፡ ሞት ፡ በሰ ማች ፡ በስንት ፡ ቀን ፡ ተጋቡ ።

ተዋበች ፤ ምናልባት ፡ ባልሳሳት ፡ ዘጠኝ ፡ ወር ፡ ያኽል ፡ ይመ ስለኛል ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ እናታችሁ ፡ ፈረንጁን ፡ ካገባች ፡ በኋላ ፡ በጣም ፡ ተመቻችሁን ።

እኔና ፡ እማማ ፡ ደኅና ፡ ነን ፡ አሽብር ፡ ግን ፡ አባባ ፡ ወደ ፡ ዘመቻ ፡ በሄደ ፡ ጊዜ ፡ የፎከረውን ፡ አልረሳ ፡ ብሎ ፡ ፋሺስት ፡ ገዳይ ፡ እያለ ፡ ስለሚፎክር ፡ እናቴ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ትመታዋለች ፡ ብርገደሌ ፡ ማሪዮም ፡ እማማን ፡ ስለ ፡ ወደደ ፡ ታግሦታል ፡ እንጂ ፡ ለመግደል ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ አስቦ ፡ ነበር ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ እባክሽ ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ሕፃን ፡ ለማ የት ፡ እወድ ፡ ነበር ፡ ብቅ ፡ ለማድረግ ፡ አትችይምን ።

ተዋበች ፤ በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኝ ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ በቅርብ ፡ ጊዜ ፡ አገሩን ፡ ፈጽሞ ፡ እንዲረሳና ፡ የፋሺስትን ፡ ገናናነት ፡ ብቻ ፡ እንዲያጠና ፡ እተማሪ ፡ ቤት ፡ ገብቷል ፡ እኛ ፡ እንኳን ፡ እንዳናሜ ውተው ፡ ተከልክለናል ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ካስኩን ፡ ወደ ፡ ፊቱ ፡ ጣል ፡ አድርጎ ፡ ዕንባ ውን ፡ እያፈሰሰ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ታሪክ ፡ በጠላት ፡ እንኳ ፡ አያ ድርስ ። አንቺ ፡ ልጅ ፡ አሁን ፡ ስታጫውቺኝ ፡ ሕልም ፡ ይመስለ ኛል ፡ እንጂ ፡ በውኔ ፡ አይመስለኝም ፤ እባክሽ ፡ አባትሽ ፡ ይህን ፡ ታምር ፡ ቢያይ ፡ እንዴት ፡ በገረመው ።

ተዋበች ፤ አባቴማ ፡ ሞቷል ፡ ነፍሱ ፡ መጥታ ፡ ለማየት ፡ አት ችል ፤ ስለ ፡ ምን ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ትናገራለኽ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፤ ምን ፡ ይታወቃል ፡ ነፍሱ ፡ መጥታ ፡ ካጥር ፡ ውጭ ፡ ቆማ ፡ ትመለከት ፡ ይሆናል ።

ተዋበች ፤ ይኸንንስ ፣ አያድርስባት ፣ አበባና ፣ እነጋሼ ፣ ቤታ ቸው ፣ በጠላት ፣ ተይዞ ፣ እማማ ፣ ያለውድ ፣ በግድ ፣ ጠላቷን ፣ አግ ብታ ፣ እኔ ፣ ላባቴ ፣ ገዳይ ፣ አገልጋይ ፣ ሆኜ ፣ አሽብር ፣ አገሩንና ፣ ወገኑን ፣ እንዲረሳ ፣ እፋሺስት ፣ ተማሪ ፣ ቤት ፣ ገብቶ ፣ ኀጢአት ፣ ሲማር ፣ነፍሱ ፣ ለመጐብኘት ፣ ብትመጣ ፣ እንደ ፣ ምን ፣ ታዝን ፤ ከዚህስ ፣ እዚያው ፣ በጦር ፣ ሜዳ ፣ ላይ ፣ ወድቀው ፣ መቅረታቸው ፣ ይሻላል ።

አቶ ፣ ተማቹ ፤ በውነት ፣ ተናገርሽ ፣ ይልቁንም ፣ ቤትን ፣ እንደ ፣ እንግዳ ፣ በበረሩፍ ፣ ላይ ፣ ቆሞ ፣ ማየት ፣ የሞት ፣ ሞትነቱን ፣ በማ ወቅሽ ፣ በጣም ፣ አመሰግንሻለሁ ፣ እየተባባሉ ፣ ሲጫወቱ ፣

ወይዘሮ ፣ ጽጌ ፣ ረዳ ፤ ተዋበች ፣ ተዋበች ፣ ብላ ፣ እየጮኸች ፣ ተጣርታ ፣ ከበሽተኛ ፣ ጋራ ፣ ይኸንን ፣ ያኽል ፣ ጨዋታ ፣ ምን ፣ ያደ ርግልሻል ፣ አትመጪምን ፣ ብላ ፣ ተቈጣቻት ።

ተዋበች ፣ እሺ ፣ እማማ ፣ መጣሁ ፣ ካለች ፣ በኋላ ፣ አንተ ፣ ሰውዬ ፣ ስለ ፣ መልካም ፣ ጨዋታኽ ፣ በጣም ፣ አመሰግንኻለሁ ፣ አለችው ።

አቶ ፣ ተማቹ ፤ እኔም ፣ ምጽዋት ፣ ስለ ፣ ሰጠሽኝ ፣ አመሰግን ሻለሁ ፣ እንጂ ፣ አንቺ ፣ ምን ፣ ታመሰግኚኛለሽ ።

ተዋበች ፤ ከኔ ፣ ቊራሽ ፣ ዳቦ ፣ ምጽዋት ፣ ይልቅ ፣ አንተ ፣ የሚ ጠቅም ፣ ጨዋታ ፣ ምጽዋት ፣ የሰጠኸኝ ፣ ይበልጣል ፣ እባክኽ ፣ ስምኽ ፣ ማነው ።

አቶ ፣ ተማቹ ፤ ስሜ ፣ ጕድ ፣ አለ ፣ ሸዋ ፣ ይባላል ።

ተዋበች ፤ እንግዴህ ፣ ደኅና ፣ ያገናኘን ፣ ብላ ፣ ወደ ፣ እናቷ ፣ ተመለሰች ።

ወይዘሮ ፣ ጽጌ ፣ ረዳ ፤ ልጄ ፣ ሆይ ፣ እጅግ ፣ ከልክ ፣ ያለፈ ፣ ነገር ፣ ትሠሪያለሽ ፣ ለድኻ ፣ ሰው ፣ ምጽዋቱን ፣ ሰጥቶ ፣ መመለስ ፣ ነው ፣ እንጂ ፣ ይኸንን ፣ ያኽል ፣ ጨዋታ ፣ ምን ፣ ያደርግለታል ፣ ከሱስ ፣ ምን ፣ ነገር ፣ ይገኛል ፣ ብለሽ ፣ ነው ፣ ይኸንን ፣ ያኽል ፣ ጊዜ ሽን ፣ ያጠፋሽ ፣ በጣም ፣ ይገርማል ።

ተዋበች ፤ ይህ ፣ ድኻ ፣ በጣም ፣ የሚጠቅም ፣ ሰው ፣ ነው ፤ ንግ ግሩም ፣ ዕጥንት ፣ ሰብሮ ፣ ይገባል ። ይልቁንም ፣ እኔን ፣ ቤታች ንን ፣ እየተመለከተ ፣ ዕንባው ፣ እንደ ፣ ጐርፍ ፣ ሲፈስ ፣ በውነት ፣

መከራችንን ፡ ሁሉ ፡ የተረዳው ፡ ይመስላል ። እማማ ፡ ብርገደሌ ፡ ማሪዮ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ በሽተኛ ፡ ሰው ፡ አይወድም ፡ እንጂ ፡ ከቤታችን ፡ አስቀምጠን ፡ ብንጦረው ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ደስ ፡ ባለኝ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ የብርገደሌን ፡ ዐመል ፡ ስታውቂው ፡ ይኸንን ፡ መናገርሽ ፡ ያሳዝናል ፡ ይልቁንስ ፡ ይህ ፡ ድኻ ፡ ምንድነው ፡ ያጫወተሽ ።

ተዋበች ፤ ያጫወተኝ ፡ ብዙ ፡ ነገሮች ፡ ናቸው ። ከነሱም ፡ ውስጥ ፡ እጅግ ፡ ያሳዘነኝና ፡ ልቤን ፡ የነካኝ ፡ የሞተ ፡ ሰው ፡ መጥቶ ፡ ቤቱን ፡ ይጐበኛል ፡ ያለኝ ፡ ነገር ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ በጣም ፡ አሳዘ ነኝና ፡ አለቀስሁ ።

ጽጌ ፡ ረዳ ፤ ስለ ፡ ምንድነው ፡ ያለቀሽው ።

ተዋበች ፤ እማማ ፡ ያባባ ፡ ነፍስ ፡ በውነት ፡ መጥታ ፡ ቤቷን ፡ ከበር ፡ ውጭ ፡ ቆማ ፡ ብትመለከት ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይገርማት ፡ በማለት ፡ ነው ። ምክንያቱም ፡ እማማ ፡ ያለውድ ፡ በግድ ፡ ጠላት ሽን ፡ አግብተሽ ፡ እኛ ፡ የሙት ፡ ልጆች ፡ በጠላት ፡ የእንጀራ ፡ አባት ፡ ስንጐላላ ፡ ሥቃይ ፡ ስናይ ፡ ያባባ ፡ ነፍስ ፡ መጥታ ፡ በበ ራፍ ፡ ቆማ ፡ የምትመለከት ፡ ብትሆን ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ኀዘን ፡ ይወድቅባት ፡ ይሆን ፡ ብዬ ፡ ነው ፡ ያለቀስኩት ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፤ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ይኸንን ፡ ያኽል ፡ አርቀሽ ፡ መመልከት ፡ አይገባሽም ። የባሌ ፡ ያቶ ፡ ተማቹ ፡ ኀዘን ፡ ካንች ፡ ይልቅ ፡ ለኔ ፡ ይሰማኛል ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እናንተን ፡ ለማሳደግ ፡ የኀ ዘኔን ፡ ፍሕም ፡ አመድ ፡ አልብሼ ፡ ማዳፈን ፡ የሚያስፈልግ ፡ ሆነ። እሳት ፡ ቢዳፈን የጠፋ ፡ ይመስላል ፡ የተባለውን ፡ አታውቂምን ፡ በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ጊዜ ፡ እንዳላዋቂ ፡ መሆን ፡ ይገባል ፡ ብላ ፡ ተቈጥታ ፡ ሁለቱም ፡ ወደ ፡ ሥራቸው ፡ ተመለሱ ።

## ምዕራፍ ፡ ፯ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ቤቱን ፡ በሩቁ ፡ እየተመለከተ ፡ ቤቴ ፡ እንደ ፡ እንግዳ ፡ በቅጥር ፡ ውጭ ፡ ሆኜ ፡ አየሁሽ ። ሚስቴም ፡ የሙት ፡ ሚስት ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ ባል ፡ አገባች ፡ ልጆቼም ፡ የሙት ፡ ልጆች ፡ ናቸው ፡ እኔም ፡ በገዛ ፡ ቤቴ ፡ በር ፡ ውጭ ፡ መጻተኛ ፡ ለማኝ ፡ ሆኜ ፡ ከልጄ ፡ እጅ ፡ ምጽዋት ፡ ተቀበልኩ ። እንግዴህ ፡ አል ሞትኹም ፡ ብል ፡ አሰተኛ ፡ ነኝ ፤ በውነትም ፡ ሞቻለሁ ፡ እያለ ፡

የመረረ ፤ ልቅሶ ፡ ካለቀሰ ፡ በኋላ ፡ ምርኵዙን ፡ ይዞ ፡ እያነከሰ ፡ ከቤቱ ፡ በታች ፡ ካንድ ፡ ትልቅ ፡ ዛፍ ፡ ሥር ፡ ሄዶ ፡ ተከናንቦ ፡ ተኛ ።

በሌሊቱ ፡ ጉዞና ፡ በደረሰበት ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ መከራ ፡ ምክን ያት ፡ በጣም ፡ ስለ ፡ ደከመ ፡ በኀዘን ፡ ሰመመን ፡ በጠለቀ ፡ እንቅ ልፍ ፡ ተውጦ ፡ ሳለ ፡ በዚያኑ ፡ ቀን ፡ ብርገደሌ ፡ ማሪዮ ፡ ብዙ ፡ የጦር ፡ መኰንኖችንና ፡ ወይዛዝሮችን ፡ ወዳጆቹን ፡ ጠርቶ ፡ ትልቅ ፡ በዓል ፡ ስላደረገ ፡ ከሌሊቱ ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ በሙዚቃ ፡ ዳንስ ፡ ሲደ ረግ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ በውካታውና ፡ በሙዚቃ ፡ ድምፅ ፡ ምክንያት ፡ ብንን ፡ ብሎ ፡ ተቀምጦ ፡ ሲመለከት ፡ ያ ፡ የድኻ ፡ ጐጆው ፡ በኤሌ ክትሪክ ፡ መብራት ፡ ቀን ፡ መስሎ ፡ አየውና ፡ እስኪ ፡ ቤቴን ፡ ደግሞ ፡ በሌሊት ፡ ልየው ፡ ከጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ከወደቁት ፡ ቅዱ ሳን ፡ ወንድሞቼ ፡ ተለይቼ ፡ ጉድ ፡ ለማየት ፡ የመጣሁ ፡ መከረኛ ፡ እያለ ፡ የመረረ ፡ ልቅሶ ፡ እያለቀሰ ፡ ከቅጥሩ ፡ በራፍ ፡ ቆሞ ፡ ይመ ለከት ፡ ጀመር ።

በቤቱ ፡ ሙሉ ፡ የጦር ፡ መኰንኖችና ፡ ወይዛዝሮች ፡ ተያይዘው ፡ ዳንስ ፡ ሲያደርጉ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ሚስቱን ፡ ለማየት ፡ በመብራቱ ፡ ውጋገን ፡ ሲፈልግ ፡ በሰው ፡ ብዛት ፡ ምክንያት ፡ ለማየት ፡ አልቻ ለም ። ከጥቂት ፡ ጊዜ ፡ በኋላ ፡ ደስ ፡ ያላት ፡ አዘነተኛ ፡ LA VEUVE JOYEUSE የሚባለው ፡ ሙዚቃ ፡ ሲመታ ፡ ብርገደሌ ፡ ማሪዮና ፡ ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ተያይዘው ፡ ብቻቸውን ፡ ዳንስ ፡ ሲያደርጉ ፡ አየና ፡ ራሱን ፡ ይዞ ፡ እያለቀሰ ፡ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ የመከራ ፡ ታምር ፡ ከማየት ፡ ምነው ፡ ከወንድሞቼና ፡ ከልጆቼ ፡ ጋራ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ወድቄ ፡ አሞራ ፡ በበላኝ ፡ እያለ ፡ እጁን ፡ ከግንባሩ ፡ ላይ ፡ አድርጎ ፡ ሲመለከት ፡ ብርገደሌ ፡ ማሪዮ ፡ በሩቅ ፡ አይቶት ፡ ምድነው ፡ ከቅጥሩ ፡ ውጭ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ቆሞ ፡ ይመለከታል ፡ አለ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ተዋበችን ፡ ጠርታ ፡ ከበራፍ ፡ የቆመው ፡ ሰው ፡ ምንድነው ፡ ጠይቂና ፡ ነይ ።

ተዋበችም ፡ ሄዳ ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ ከዚህ ፡ ምን ፡ ታደርጋለኽ ።

አቶ ፡ ተማቹም ፤ እኔ ፡ ዛሬ ፡ ጧት ፡ ምጽዋት ፡ የሰጠሽኝ ፡ ጉድ ፡ አለ ፡ ሸዋ ፡ የምባለው ፡ ድኻ ፡ ነኝ ፡ መሽቶብኝ ፡ ከዚህ ፡ ስላደርኩ ፡ ይኸንን ፡ ዓለምና ፡ ደስታ ፡ ለማየት ፡ ቆሜያለሁ ።

ተዋበችም ፡ ይኸንን ፡ በሰማች ፡ ጊዜ ፡ ሮጣ ፡ ለናቷና ፡ ለብርገደሌ ፡ ማሪዮ ፡ ያ ፡ ጧት ፡ ምጽዋት ፡ የሰጠነው ፡ በሽተኛ ፡ ድኻ፡ ነው ። ለምን ፡ መጣኽ ፡ ብዬ ፡ ብጠይቀው ፡ መሽቶብኝ ፡ ከዚህ ፡ አድሬ ፡ ነበር ። አሁን ፡ ግን ፡ ይኸንን ፡ ዓለምና ፡ ደስታ ፡ ለማየት ፡ ቆሚያለሁ ፡ አለኝ ።

ብርገደሌ ፡ ማሪዮ ፡ ችግረኛው ፡ ድኻ ፡ ይኸንን ፡ ዓለምና ፡ ደስታ ፡ ለመካፈል ፡ ጓጒቶ ፡ ነውና ፡ እንቺ ፡ ይኸንን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ በዚች ፡ ብርጭቆ ፡ ውሰጅለትና ፡ ከጠጣ ፡ በኋላ ፡ በሽታው ፡ እንዳይጋባብን ፡ ብርጭቆውን ፡ ስበሪው ።

ተዋበችም ፡ ቶሎ ፡ ብላ ፤ ሄዳ ፡ እንሆ ፡ የተከበረው ፡ ብርገደሌ ፡ የላከልኽ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ።

አቶ ፡ ተማቹም ፡ ከልጁ ፡ እጅ ፡ ተቀብሎ ፡ የሞቱን ፡ ጽዋ ፡ ልጠጣ ፡ ብሎ ፡ በሲቃ ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ ጭልጥ ፡ አድርጎ ፡ ብርጭቆውን ፡ መለሰላት ።

ተዋበችም ፡ ብርጭቆውን ፡ ከፊቱ ፡ አንድ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ ከስክሳው ፡ ወደ ፡ ቤቷ ፡ ገባች ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ የተሰባበረውን ፡ ብርጭቆ ፡ በኀዘን ፡ ከተመለከተ ፡ በኋላ ፤ እኔም ፡ እኮ ፡ እንደዚህ ፡ ብርጭቆ ፡ የተሰባበርኹ ፡ የማረባ ፡ ዕቃ ፡ ነኝ ፡ ብርሌ ፡ ከነቃ ፡ አይሆንም ፡ ዕቃ ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ እኔ ፡ እንግዴህ ፡ ሞቻለሁ ። ይህ ፡ ብርጭቆ ፡ እንኳ ፡ የኔን የዕድል ፡ ቢሱን ፡ ከንፈር ፤ በመንካቱ ፡ ተሰባበረ ፡ እንግዴህ ፡ ይኸንን ቲያትር ፡ ከቤቱ ፡ በራፍ ፡ ሆኜ ፡ ከተመለከትኹ ፡ በኋላ ፡ መቆም ፡ አይገባኝምና ፡ ሚስቴ ፡ ቤቴ ፡ ልጆቼ ፡ ደኅና ፡ ሰንብቱ ፡ ብሎ ፡ ወደ፡ ዛፉ ፡ ሥር ፡ ተመልሶ ፡ ተቀመጠና ፡ ከኅሊናው ፡ ጋራ ፡ እንደዚህ ፡ እያለ ፡ ይጫወት ፡ ዠመር ።

ያጡትን ፡ ነገር ፡ በሩቁ ፡ ሲያዩት ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያምራል ፤ የቤቴንና ፡ የሚስቴን ፡ ውበት ፡ ዛሬ ፡ ገና ፡ ከቤቴ ፡ በራፍ ፡ ሆኜ ፡ አየሁት ፡ የቤቴ ፡ ለማኝ ፡ ሆኜ ፡ በሩቁ ፡ ቆሜ ፡ ነበር ። ሚስቴ ፡ ከነጭ ፡ ልብሷ ፡ ጋራ ፡ በውበት ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ መስላ ፡ ከጠላቴ ፡ ጋራ ስትዘፍን ፡ የሙዚቃው ፡ ስልት ፡ ልቤን ፡ እንደ ፡ ጦር ፡ ወጋኝ ፡ በዕንባዬ ፡ ሰሌዳ ፡ ላይ ፡ ተጽፎ ፡ የሚታየኝ ፡ ይህ ፡ ቤትኽ ፡ አይደለም ፡ ሚስትኽም ፡ ያንተ ፡ አይደለች ፡ የረገጥኸውም ፡ መሬት ፡ እንኳ ፡ የጠላት ፡ ነው ፡ የሚል ፡ ነው ።

እንግዴህ ፡ ማነኝ ፡ ሟቹ ፡ ተማቹ ፡ አይደለሁምን ፡ እያለ ፡ ሲያስብ ፡ እንቅልፍ ፡ ያዘውና ፡ ወደቀ ። ጥቂት ፡ እንዳሸለበው ፡ በሕልሙ ፡ ልጁ ፡ ተዋበች ፡ በብርጭቆ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ አምጥታ ፡ ይኸንን ፡ የሞት ፡ ጽዋ ፡ ጠጣ ፡ ብላ ፡ ስትሰጠው ፡ እሱም ፡ ተቀብሎ ፡ በብርጭቆ ፡ ውስጥ ፡ ያለውን ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ጭልጥ ፡ አድርጎ ፡ ብርጭቆውን ፡ ሲሰጣት ፡ ተዋበች ፡ ተቀብላ ፡ ከድንጋይ ፡ ላይ ፡ ስትሰባብረው ፡ እንደ ፡ ጠመንዣ ፡ ተኵስ ፡ ስለ ፡ ጮኸበት ፡ ደንግጦ ፡ ብንን ፡ አለ ።

አቶ ፡ ተማቹ ፡ ብድግ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ቢመለከት ፡ ብርገደሌ ፡ ማሪዮ ፡ ከተጠሩት ፡ መኰንኖችና ፡ ወይዛዝሮች ፡ ጋራ ፡ የጽጌ ፡ ረዳን ፡ እጅ ይዞ ፡ ከውጭ ፡ ወጥተው ፡ የእሳት ፡ ነበልባል ፡ (ፊ ፡ አርቲፊሲዩል) ። እየተኰሱ ፡ ሲያወኩ ፡ ሲሥቁ ፡ አይቶ ፡ ተመልሶ ፡ ከዛፉ ፡ ሥር ፡ ተቀምጦ ፡ የሞቴ ፡ አስታዋሾቼ ፡ በዙ ። እንግዴህ ፡ የሕይወቴ ፡ ብርጭቆ ፡ መሰበሪያዋ ፡ ደረሰ ፡ ብሎ ፡ በጠለቀ አሳብ ፡ ተውጦ ፡ መሬት ፡ መሬቱን ፡ ሲመለከት ፡ ጎሕ ፡ ቀደደ ፡ ሰማዩም ፡ ደም ፡ መሰለ ። ስለዚህ ፡ ጽሕፈት ፡ ለመጻፍ ፡ ጥቂት ፡ ብርሃን ፡ ስላገኘ ፡ ከኪሱ ፡ አንዲት ፡ ወረቀት ፡ አውጥቶ ፡ በርሳስ ፡ የተወደድሽ ፡ ፍቅሬ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ እኔ ፡ ወዳጅሽ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ የወደቁትን ፡ አርበኞች ፡ ጥዬ ፡ ሞት ፡ ተፍቶኝ ፡ መጣሁ ፡ ልጅሽ ፡ ክንዴ ፡ በጠላቱ ፡ ሬሳ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ እኔን ፡ ሲጠራ ፡ አፉን ፡ እንደ ፡ ከፈተ ፡ አግኝቼው ፡ ተሰናበትሁት ። ጋሻው ፡ በዛ ፡ የምትወጂው ፡ ልጅሽ ፡ በጭኔ ፡ ላይ ፡ ውሃ ፡ ውሃ ፡ ሲል ፡ ዐረፈ ። የቀሩትም ፡ አርበኞች ፡ ከጠላት ፡ ጋራ ፡ ተቃቅፈው ፡ ተኝተዋል ። እኔም ፡ በርሻ ፡ መካከል ፡ ወፍ ፡ እንደሚጠብቅ ፡ እረኛ ፡ አ፡በኞችን ፡ ለመመገብ ፡ የተዘጋጁትን ፡ አሞሮች ፡ ስከላከል ፡ ነበር ።

ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ የነሱን ፡ ዕድል ፡ ለማግኘት ፡ ብፈልግ ፡ ሳይሆንልኝ ፡ ቀረ ። ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ራሴን ፡ ለመግደል ፡ አስቤ ፡ የራሴን ነፍስ ፡ ገዳይ ፡ አልሆንም ፡ በማለት ፡ ተውኹት ፤ ስለዚህ ፡ ተመልሼ ወዳገሬ ፡ መጣሁ ።

ከመናገሻው ፡ ከተማ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ገብቼ ፡ በቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ላይ ፡ የጠላት ባንዲራ ፡ ሲውለበለብበት ፡ አየሁ ።

እንግዴህ ፡ አንዲት ፡ ተስፋ ፡ ያደረግኋት ፡ አንቺን ፡ ማየትና ልጆቼን ፡ መሳም ፡ ነበር ፤ ሳይሆንልኝ ፡ ቀረ ።

ቤቴን ፡ በሩቅ ፡ አየሁት ፤ በልጄ ፡ እጅ ፡ ምጽዋት ፡ ተቀበ ልኹ ። ከጠላቴ ፡ ጋራ ፡ ስትዘፍኝ ፡ በመብራቱ ፡ ውጋጋን ፡ አየ ሁሽ ፤ የደስታሽ ፡ ተካፋይ ፡ እንድሆን ፡ ጠላቴ ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ ልኮልኝ ፡ ጠጣሁ ። ዕድለ ፡ ቢሷ ፡ ብርጭቆ ፡ የኔን ፡ አፍ ፡ በመን ካቷ ፡ ሞት ፡ ተፈርዶባት ፡ በድንጋይ ፡ ላይ ፡ ተሰበረች ።

እኝግዴህ ፡ አልሞትኹም ፡ ብል ፡ አሰተኛ ፡ ነኝ ፡ በውነትም ሞቻለሁ ። አንቺም ፡ የሙት ፡ ሚስት ፡ ነሽ ፡ ልጆቼም ፡ የሙት ፡ ልጆች ፡ ናቸው ።

ወዳጄ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ የሚገድለኝ ፡ ሰው ፡ ስላጣሁ ፡ የዕድ ሚዬን ፡ ገመድ ፡ እኔው ፡ ራሴ ፡ መቍረጥ ፡ ግዴታ ፡ ሆነብኝ ፡ ተዋበችንና ፡ አሸብርን ፡ ሳሚልኝ ፡ ደኅና ፡ ሰንብች ። እኔ ፡ ባልሽ ፡ ተማቹ ፡ ነኝ ፡ የሚል ፡ ጽፎ ፡ ከግሩ ፡ ላይ ፡ በገመድ ፡ አስሮ ፡ ለከ ረጢት ፡ ማሰሪያ ፡ ብሎ ፡ ከልጁ ፡ ለምኖ ፡ የወሰደውን ፡ ገመድ ፡ ካንገቱ ፡ አግብቶ ፡ እዛፉ ፡ ላይ ፡ ለመውጣት ፡ ይጣጣር ፡ ዠመር ።

ካሥር ፡ ደቂቃ ፡ በኋላ ፡ በግድ ፡ በብዙ ፡ ችግር ፡ ወጥቶ ፡ ካንድ ወፍራም ፡ ቅርንጫፍ ፡ ላይ ፡ ገመዱን ፡ አጥብቆ ፡ ካሰረ ፡ በኋላ፡ ከዛፉ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ መጨረሻ ፡ ጸሎቱን ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ጸለየ ።

አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ እኔን ፡ የራሴን ፡ ነፍስ ፡ ገዳይ ፡ ይቅር ፡ በለኝ ከዚህ ፡ ቀደም ፡ የጦር ፡ ጓደኛዬን ፡ ሸንኰሩን ፡ ከብዙ ፡ ሥቃይ ፡ ለማዳን ፡ ስል ፤ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ በመሆኔ ፡ ሳዝን ፡ የራሴ ፡ ዕጣ ፡ ደረሰ። እኔ ፡ ስላገሬ ፡ ሽባና ፡ ስንኩል ፡ የሆንኩ ፡ ፊቴም ፡ ዐይኔም ፡ በመ ርዝ ፡ ተቃጥሎ ፡ የተበላሸና ፡ የጠቈረ ፡ ሚስቴም ፡ ባል ፡ አግብታ ፡ ልጆቼም ፡ የሙት ፡ ልጆች ፡ ከሆኑ ፡ አልሞትኹም ፡ ብዬ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ብኖር ፡ በቁማቸው ፡ አሞራ ፡ እንደ ፡ በላቸው ፡ የጦር ፡ ጓደ ኞቼ ፡ በሥቃይ ፡ ከመሞት ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ ትርፍ ፡ እንደሌለኝ ፡ አምናለሁ ። ስለዚህ ፡ እኔ ፡ መሆኔን ፡ አስታውቄ ፡ በዚህ ፡ ዛፍ ፡ ላይ ብሰቀል ፡ ያገሬን ፡ ሕዝብ ፡ እንዲያነቃቃና ፡ የተዳፈነውን ፡ እሳት ፡ እንዲቈሰቍስ ፡ ስላመንኹ ፡ ራሴን ፡ በራሴ ፡ መግደል ፡ መረጥኹ ። አቤቱ ፡ የዓለም ፡ መድኃኒት ፡ ነፍሴን ፡ ተቀበላት ፡ ብሎ ፡ ዘሎ ፡ ሲወ ድቅ ፡ በቅርንጫፉ ፡ ላይ ፡ ተንጠልጥሎ ፡ ታንቆ ፡ ሞተ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ከባሏና ፡ ከልጆቿ ፡ ሞት ፡ ወዲህ ፡ ማለዳ ከደብረ ፡ ብርሃን ፡ ሥላሴ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እየሄደች ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ለወደቀው ፡ ባሏና ፡ ልጆቿ ፡ የሙታን ፡ ጸሎት ፡ ማድ

ረግ ፡ ስላስለመደች ፡ በሯን ፡ ከፍታ ፡ ሦስት ፡ አራት ፡ ጊዜ ፡ ያህል ፡ እንደተራመደች ፡ ከቤቷ ፡ አጠገብ ፡ ካለው ፡ ዛፍ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ድኻ ፡ ልብሱ ፡ የተበጫጨቀ ፡ ሰው ፡ ተሰቅሎ ፡ አየች ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ከራሷ ፡ እስከግሯ ፡ ድረስ ፡ በድንጋጤ ፡ ተንዘፈዘፈች ፡ ዕንባዋም ፡ ይንጠባጠብ ፡ ዠመር ።

ወዲያው ፡ ይህ ፡ ችጋረኛ፡ሰው ፡ አገሩን፡ በመውደድ፡ ምክንያት ፡ ፋሺስቶች ፡ ሰቅለውት ፡ ይሆናል ፡ ብላ፡ ስትፈራ ፡ ስታመነታ ፡ ጕዱን ፡ ለማየት ፡ ካጠገቡ ፡ ሄዳ ፡ ትመለከት ፡ ዠመር ።

በድንገት ፡ ከእግሩ ፡ ላይ ፡ የታሰረውን ፡ ወረቀት ፡ አየች ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ የሠራውን ፡ ኃጢአት ፡ ለሕዝቡ ፡ ለማሳወቅ ፡ ፋሽስቶች ፡ ጽፈው ፡ ያሰሩት ፡ ስለ ፡ መሰላት ፡ ጠጋ ፡ ብላ ፡ ብታነበው ፡ የምትወደው ፡ ባሏ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ መሆኑን ፡ የሚገልጥና ፡ የልጆቿን ፡ አማሖት ፡ የሚያስረዳ ፡ የሚያሳዝን ፡ ጽሑፍ ፡ ሆኖ፡ አገኘችው ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ለወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ የተሰማትን ፡ ኀዘን ፡ በጽሑፍ ፡ ለመግለጽ ፡ ያስቸግራል ።

በጠቅላላው ፡ ዐይኗ ፡ ነጭ ፡ ሆኖ ፤ ፊቷ ፡ እንደ ፡ ዕብነ ፡ በረድ ፡ ሐውልት ፡ በኀዘን ፡ ገርጥቶ ፡ ዕንባዋ ፡ ካይኗ ፡ ደርቆ ፡ የሞተ ፡ ሰው ፡ ትመስል ፡ ነበር ።

እውነተኛው ፡ ደረቅ ፡ ኀዘን ፡ ስለ ፡ ያዛት ፡ የምታስበው ፡ ጠፍቷት ፡ እንደ ፡ አበደች ፡ ሴት ፡ ስትሥቅ ፤ ስትንቀጠቀጥ ፤ ራሷን ፡ ስትነጭ ፤ ለማልቀስም ፡ ስትሞክር ፡ ከቈየች ፡ በኋላ ።

ከላዩ ፡ ላይ ፡ ተጠምጥማ ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ በገዛ ፡ ቤትኽ ፡ ከልጅኽ ፡ ምጽዋት ፡ ተቀበልኽን ።

እኔም ፡ በደከምኽበት ፡ ቤት ፡ ከጠላት ፡ ጋራ ፡ ስዘፍን ፡ አየኸኝን ።

ያገርኽና ፡ የሚስትኽም ፡ ጣውንት ፡ ወይን ፡ ጠጅ ፡ ልክልኽ ፡ ስትጠጣ ፡ በሩቅ ፡ አየንኽ ።

የምወድኽ ፡ ወዳጄ ፡ አፍህ ፡ የነካውን ፡ ብርጭቆ ፡ ከቤታችን ፡ እንዳይገባ ፡ ተጠይፈን ፡ አሰበርነው ።

ለካ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ጭልጥ ፡ ያደረግኸው ፡ የሞትህን ፡ ጽዋ ፡ ኖሯልን ።

እንደዚህ ፡ ያለ ፡ መከራ ፡ ከዚህ ፡ ቀደም ፡ በማንም ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ አልደረሰም ።

ወይ ፡ እኔ ፡ ከሐዲዋ ፡ እንደዚህ ፡ ሆኜ ፡ ቈየሁህ ፡ ብላ ፡ እንደ አበደ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ቤቷ ፡ ተመልሳ ፡ ገባች ።

ብርገደሌ ፡ ማሪዮም ፡ አርበኞችን ፡ ለማሳደድ ፡ ለምክር ፡ በጧት ወደ ፡ ጎቨርነሩ ፡ ለመሄድ ፡ ቀጠሮ ፡ ስላለበት ፡ ልብሱን ፡ ለብሶ ፡ ቡና ፡ ለመጠጣት ፡ ከመብል ፡ ጠረጴዛ ፡ ላይ ፡ ተደግፎ ፡ ጋዜጣ ፡ እየ ተመለከተ ፡ ሚስቱን ፡ ሲጠብቅ ፡ ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ እንደ ፡ አበደ ፡ ሰው ፡ እየሮጠች ፡ በሩን ፡ ከፍታ ፡ ገባችና ፡ ወደ ፡ ወጥ ፡ ቤት ፡ ለመግባት ፡ ቸኰለች ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ብርገደሌ ፡ ማሪዮ ፡ ቀና ፡ ብሎ ፡ በጣሊያን ፡ ቋንቋ ፡ ወዳጄ ፡ ምን ፡ ሆንሽ ፡ አለና ፡ ጠየቃት ።

እሷም ፡ በጣሊያን ፡ ቋንቋ ፡ ወዳጅኽ ፡ አይደለሁም ፡ አለ ችውና ፡ ወደ ፡ ወጥ ፡ ቤት ፡ ገባች ።

ብርገደሌም ፡ እሷ ፡ ከወጥ ፡ ቤት ፡ እስክትመለስ ፡ ድረስ ፡ ያንኑ ፡ ጋዜጣውን ፡ እያነበበ ፡ ምን ፡ ነገር ፡ አገኛት ፡ ይሆን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ መጥታ ፡ ምክንያቱን ፡ በጠየቅኋት ፡ እያለ ፡ ሲያ ስብ ፡ ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ የወጥ ፡ ቤት ፡ ዕንጨት ፡ መፍለጫ ዋን ፡ የተሳለ ፡ ፋስ ፡ ይዛ ፡ መጥታ ፡ ሳያያት ፡ አንተ ፡ ያገሬና ፡ የባሌ ፡ ጠላት ፡ ሕይወቴ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ታልፋለች ፡ ብላ ፡ አን ገቱን ፡ በፋሱ ፡ ብትመታው ፡ ተቈርጦ ፡ ከጠረጴዛው ፡ በታች ፡ ወደቀ ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ፋሱ ፡ በደም ፡ እንደ ፡ ተነከረ ፡ በጅዋ ፡ ይዛ ፡ ከከተማው ፡ መካከል ፡ ሄዳ ፡ ካንድ ፡ ትልቅ ፡ ቋጥኝ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ ቆማ ፤ ስሙ ፡ ስሙ ፡ እናንት ፡ የኢትዮጵያ ፡ ልጆች ፤ እናታችሁ ፡ ኢትዮጵያ ፡ በባርነት ፡ ሰንሰለት ፡ ታስራ ፡ ስትጮኽ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ዝም ፡ ብላችሁ ፡ በጥቅም ፡ ገሯችሁን ፡ ደፍናችሁ ፡ ውርደትን ፡ ተሸክማችሁ ፡ ትሮጣላችሁ ።

በውነት ፡ አታፍሩምን ።

ወንድሞቼ ፡ ሆይ ፡ እኔ ፡ በቋጥኝ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ ቆሚ ፡ የማመለክታችሁ ፡ አንዲት ፡ ደካማ ፡ ድኻ ፡ ሴት ፡ የዛሬ ፡ ዓመት ፡ ባሌና ፡ ሁለቱ ፡ ልጆቼ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ስላገራቸው ፡ ሞቱ ፡

ብለው ፡ ካረዱኝ ፡ በኋላ ፡ እንሆ ፡ ከትላንት ፡ ወዲያ ፡ ባሌ ፡ በብ ርቱ ፡ ቍስል ፡ ቈስሎ ፤ ፊቱም ፡ በመርዝ ፡ ተቃጥሎ ፡ ከውጋዴን ፡ በረሓ ፡ ልጆቹን ፡ ላሞራ ፡ ምግብ ፡ ትቶ ፡ እኔንና ፡ የተረፉት ፡ ልጆቹን ፡ ለማየት ፡ ቢመጣ ፡ የጠላት ፡ ሚስት ፡ ሆኜ ፡ ቈየሁት ።

ቤቱም ፡ የጠላት ፡ ቤት ፡ ሆኖ ፡ አገኘው ፤ በቤቱ ፡ በራፍ፡ቆሞ ፡ ሲለምን ፡ ከልጁ ፡ ምጽዋት ፡ ተቀበለ ።

እኔንም ፡ በሩቁ ፡ ከጠላት ፡ ጋራ ፡ ስዘፍን ፡ አየ ።

ስለዚህ ፡ ቤቴ ፡ በውጭ ፡ አየሁሽ ፡ በውነትም ፡ ሞቻለሁ ፡ አልሞትኹም ፡ ብዬ ፡ አልዋሽም ፡ ብሎ ፡ በረዥሙ ፡ ጽፎ ፤ እነሆ፡ ከቤቱ ፡ በታች ፡ ካለው ፡ ዛፍ ፡ ላይ ፡ ተሰቅሎ ፡ ይታያል ።

እኔ ፡ ሴቲቷ ፡ እንኳ ፡ ያለውድ ፡ በግድ ፡ ከጠላቴ ፡ ጋራ ፡ ተጋብቼ ፡ የነበርኩት ፡ ግፍ ፡ ጕበዝ ፡ አድርጎኝ ፡ ዛሬ ፡ ጧት ፡ በደም ፡ ተፋታን ።

ያገሬ ፡ ልጆች ፡ ሆይ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ የግፍ ፡ ባሪያ፡ ሆናችሁ ፡ ትኖራላችሁ ።

እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ሕግ ፡ አልባ ፡ እንደ ፡ ከብት ፡ ያለ መብትና ፡ ያለነፃነት ፡ ትገዛላችሁ ።

ያገሬ ፡ ሴት ፡ ስንፍ ፡ የዶብ ፤ ላም ፡ የጋለሞታ ፡ ብላ ፡ ጮኸች፡ ይባላል ።

አሁንም ፡ ጥቃቱ ፡ የሴቶችና ፡ የሰላማዊ ፡ ሕዝብ ፡ ቢሆን ፡ ስንፉ ፡ የወታደሮችና ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ ነውና ፤ ያገሬ ፡ ልጅ ፡ እጅኽን ፡ በጠላትኽ ፡ ላይ ፡ አንሣ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ የወንድ ፡ ያለኽ፡ የጕበዝ ፡ ያለኽ ፡ እያለች ፡ ትጮኽ ፡ ዡመር ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ከቋጥኝ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ በደም ፡ የተነ ከረ ፡ ፋስ ፡ ይዛ ፡ በፊቷ ፡ ላይ ፡ ለሞት ፡ የተደራጀ ፡ የቈራጥ ፡ አር በኛ ፡ መንፈስ ፡ ይታይባት ፡ ነበር ።

ስለዚህ ፡ የደብረ ፡ ብርሃን ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ተገርሞ ፡ ዙሪ ያውን ፡ ተሰብስቦ ፡ ሲመለከት ፡ አገረ ፡ ገዢው ፡ ሰምቶ ፡ አንድ ፡ ያልታሰበ ፡ አደጋ ፡ የመጣ ፡ ስለ ፡ መሰለው ፡ ባቅራቢያው ፡ አገር፡ በሸዋና ፡ በደብረ ፡ ሲና ፡ ያለውን ፡ ጦር ፡ በቶሎ ፡ ወደ ፡ ደብረ፡ ብርሃን ፡ እንዲመጣ ፡ አዘዘ ።

የደብረ ፡ ብርሃን ፡ ከተማም ፡ በዚያው ፡ ባለው ፡ ፖሊስና ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ተከበበ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ግን ፡ ሳታቋርጥ ፡ ያገሬ ፡ ጕበዝ ፡ እጅኽን ፡ በጠላትኽ ፡ ላይ ፡ አንሣ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ ትል ፡ ነበር ።

አንድ ፡ ሰዓት ፡ ያኽል ፡ የከተማው ፡ ሕዝብ ፡ እሷን ፡ እየ ተመለከተ ፡ ሲገረም ፡ ከቈየ ፡ በኋላ ፡ የደብረ ፡ ብርሃኑ ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ አለቃ ፡ መጥቶ ፡ ሕዝቡን ፡ አባሮ ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ እስከ ፡ ነገ ፡ ድረስ ፡ ከቤቱ ፡ ወጥቶ ፡ በውጭ ፡ የተገኘ ፡ ይገደላል ፡ የሚል ፡ ዐዋጅ ፡ በራዲዮ ፡ ስለ ፡ ተነገረ ፡ በደብረ ፡ ብርሃን ፡ ከተማ ፡ ከጦር ፡ ሠራዊት ፡ በቀር ፡ ምንም ፡ የሰላም ፡ ሕዝብ ፡ የማይታይ ፡ ሆነ ።

ወዲያው ፡ የከተማው ፡ ፖሊስ ፡ አለቃ ፡ ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳን ፡ ከቋጥኝ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ አውርዶ ፡ ወደ ፡ ዋናው ፡ አገረ ፡ ገዥ ፡ ወሰዳት ።

ምርመራ ።

ዋናው ፡ አገር ፡ ገዢ ፤ ስምሽ ፡ ማነው ፡

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፤ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ እባላለሁ ።

ዋናው ፡ አገረ ፡ ገዢ ፤ ባል ፡ አግብተሻልን ፤

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፤ አዎን ፡ ሁለት ፡ ባሎች ፡ ነበሩኝ ።

አገረ ፡ ገዢው ፤ ሁለቱንም ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ አግብተሽ ፡ ተቀምጠሻልን ፡

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፤ አንዱ ፡ ስለ ሞተብኝ ሌላውን ፡ አግብቼ ፡ ነበር ።

የሞተው ፡ ተነሥቶ ፡ ስለ ፡ መጣና ፡ በቤቱ ፡ አጠገብ ፡ ስለ ፡ ተሰቀለ ፡ ሁለተኛውን ፡ ባሌን ፡ በፋስ ፡ አንገቱን ፡ ቈርጬ ፡ ጥዬው ፡ በመብል ፡ ቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ይገኛል ።

አገረ ፡ ገዢው ፤ ምን ፡ የሚገርም ፡ ነገር ፡ ነው ፤ የተሰቀለው ፡ ባልሽ ፡ ማን ፡ ይባላል ።

ጽጌ ፡ ረዳ ፤ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ይባላል ።

አገረ ፡ ገዢው ፤ ሁለተኛው ፡ አንቺ ፡ የገደልሺው ፡ ባልሽ ፡ ማን ፡ ይባላል ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፤ ብርገደሌ ፡ ማሪዮ ፡ ይባላል ።

አገረ ፡ ገዢው ፤ ደንግጦ ፡ ማሪዮ ፤ ጽጌ ፡ ረዳም ፡ ማሪዮ ፡ ብላ ፡ መለሰችለት ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ በድንጋጤ ፡ እሱው ፡ ራሱ ፡ ሹማምቱን ፡ ይዞ ፡ ከብርገደሌ ፡ ማሪዮ ፡ ቤት ፡ ቢሄድ ፡ አንገቱን ፡ ተቈርጦ ፡ ከመብሉ ፡ ጠረጴዛ ፡ ውስጥ ፡ ወድቆ ፡ የቀረው ፡ አካላቱ ፡ ከወንበሩ ፡ ላይ ፡ ተፈንግሎ ፡ በገርባው ፡ ተዘርሮ ፡ አገኙት ።

ሹማምቱ ፡ ሁሉ ፡ ተገርመው ፡ ቆመው ፡ ሲመለከቱ ፡ አንድ ፡ የፖሊስ ፡ ሹም ፡ ሲሮጥ ፡ መጥቶ ፡ ከዚህ ፡ ከበታቻችን ፡ ካለው ፡ ዛፍ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ልብሱ ፡ የተበጫጨቀ ፡ ሰው ፡ ተሰቅሏል ፡ ብሎ ፡ አስታወቀ ።

አገረ ፡ ገዢው ፡ ቶሎ ፡ ብሎ ፡ ወጥቶ ፡ ቢያየው ፡ የሕይወቱን ፡ ታሪክ ፡ በእግሩ ፡ ላይ ፡ አስሮ ፡ ተሰቅሎ ፡ አየና ፡ ወረቀቱን ፡ ፈቶ ፡ በኪሱ ፡ አድርጎ ፡ ከሁለቱም ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ ፖሊስ ፡ አቁሞ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ተመለሰ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ ሁለተኛ ፡ ቀርባ ፡ ትመረመር ፡ ገመር ።

አገረ ፡ ገዢው ፡ እባክሽ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ የጭካኔና ፡ የብርታት ፡ የዕውቀት ፡ ሥራ ፡ ደፍረሽ ፡ እንድትሠሪ ፡ ማን ፡ መከረሽ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፤ በባሌ ፡ ባቶ ፡ ተማቺና ፡ በኔ ፡ የደረሰው ፡ ግፍና ፡ መከራ ፡ ነው ፡ የመከረኝ ።

አገረ ፡ ገዢው ፤ ይህ ፡ እውነት ፡ አይደለም ፡ አንቺን ፡ ሴቲቱን ፡ እንደዚህ ፡ ያበረታታሽ ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ አለ ።
ይልቅስ ፡ በብርቱ ፡ ሥቃይ ፡ እየተመረመርሽ ፡ ከማውጣት ፤ እንደዚሁ ፡ ክብርሽ ፡ ሳይደፈር ፡ ብትናገሪ ፡ ይሻላል ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፤ ማንም ፡ አልመከረኝም ፤ ማንም ፡ ሰው ፡ በዚህ ፡ ጉዳይ ፡ የረዳኝ ፡ የለም ።

አገረ ፡ ገዢው ፤ እየማቀ ፡ በተፈጥሮሽ ፡ ደካማ ፡ የሆንሽ ፡ ሴት ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ብርታትና ፡ ጥልቅ ፡ የሆነ ፡ የክፋት ፡ ፕሮፓጋንዳ ፡ ካንች ፡ አንጎል ፤ ውስጥ ፡ እንዳይወጣ ፡ የታወቀ ፡ ነው ።

መከራ ፡ ባሕርይን ፡ ይለውጣልን ፡ ሴትን ፡ ወንድ ፡ ያደርጋልን ፡ ይኸንን ፡ የሚያምንም ፡ እንዳቺ ፡ ዕብድ ፡ የሆነ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ይልቁንስ ፡ ብትናገሪ ፡ ይሻላል ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ በስድቡ ፡ ምክንያት ፡ ደሟ ፡ ፈልቶ ፡ ክቡር ፡ ሆይ ፡ ጊዜና ፡ ግፍ ፡ ሰውን ፡ ጉበዝ ፡ እንደሚያደርገውና ፡ ሴትንም ፡ እንደ ፡ ወንድ ፡ እንደሚያበረታ ፡ ርስዎም ፡ አይስቱትም ።

ለምሳሌ ፡ እንሆ ፡ ጊዜ ፡ እናንተን ፡ ጕበዝ ፡ አድርጓችሁ ፡ የዠግኖችን ፡ አገር ፡ ኢትዮጵያን ፡ ትገዙ ፡ የለምን ።

አገረ ፡ ገዢው ፡ ብድግ ፡ ብሎ ፡ አንቺ ፡ ሽርሙጣ ፡ ታላቁ ፡ ዓለም ፡ ሁሉ ፡ የሚንቀጠቀጥለትን ፡ የፋሺስት ፡ መንግሥት ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ትሳደቢያለሽ ፡ ብሎ ፡ በቡጢ ፡ መትቶ ፡ ጥሎ ፡ በጫማው ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ራሷን ፡ ከረገጠ ፡ በኋላ ፡ የካራቢኔሩን ፡ ሹም ፡ ጠርቶ ፡ ይህቺን ፡ ሴት ፡ ከዚያ ፡ ከድፋም ፡ ባሏ ፡ ጋራ ፡ ከዛፍ ፡ ላይ ፡ ስቀሏት ፡ ብሎ ፡ አዘዘ ።

ወይዘሮ ፡ ጽጌ ፡ ረዳም ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ከምወደው ፡ ባሌ ፡ ጋር ፡ ስሰቀል ። ነገር ፡ ግን ፡ አንተ ፡ በስፈርከው ፡ ቍና ፡ ሳትሰፈር ፡ አትቀርም ፡ ብላው ፡ ዘበኞቹን ፡ ቀድሞ ፡ ደሟ ፡ በፍንጫዋ ፡ እየፈሰሰ ፡ በሕዝቡ ፡ መካከል ፡ ያገሬ ፡ ልጅ ፡ በጠላትኽ ፡ ላይ ፡ እጅኽን ፡ አንሣ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ እያለች ፡ ወስደው ፡ ሰቀሏት ።

ብርገደሌ ፡ ማሪዮንም ፡ በማግሥቱ ፡ ትልቅ ፡ ሰልፍና ፡ የክብር ፡ በዓል ፡ ተደርጎለት ፡ በጣሊያን ፡ ባንዲራ ፡ ማጥኑ ፡ ተሸፍኖ ፡ በከተማው ፡ መካከል ፡ ተጕዞ ፡ ከፍ ፡ ባለው ፡ ክብር ፡ ተቀበረ ።

ነገር ፡ ግን ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከሚሰቀልበት ፡ ዛፍ ፡ ላይ ፡ የመጨረሻ ፡ ጸሎቱን ፡ ሲያደርግ ፡ ያገሬን ፡ ሕዝብ ፡ እንዲያነቃቃና ፡ የተዳፈነውን ፡ እሳት ፡ እንዲቈሰቍስ ፡ ስላመንሁ ፡ ራሴን ፡ በራሴ ፡ መግደል ፡ መረጥሁ ፡ ብሎ ፡ እንደተናዘዘው ፤ በውነትም ፡ የሱ ፡ ግፍና ፡ የመከራ ፡ አሟሟት ፡ ሚስቱን ፡ አርበኛ ፡ እንድትሆን ፡ አበረታትቶ ፡ በቋጥኝ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ ሆና ፡ በተናገረችው ፡ ቃልና ፡ እሷም ፡ ራሷ ፡ ከባሏ ፡ ጋራ ፡ በተሰቀለችበት ፡ ምክንያት ፡ የብዙ ፡ ሕዝቡን ፡ ልብ ፡ ቀሰቀሰ ።

ተዳፍኖ ፡ የነበረውን ፡ እሳትም ፡ ቈሰቈሰው ።

በዚያኑ ፡ ሌሊት ፡ ከደብረ ፡ ብርሃን ፡ ከተማ ፡ ውስጥ ፡ በሺሕ ፡ የሚቈጠሩ ፡ ወጣቶች ፡ አርበኞች ፡ ሆኑ ።

ይልቁንም ፡ ይህ ፡ ወሬ ፡ በጐጃም ፡ በበጌምድር ፡ በሸዋ ፡ በትግሬ ፡ በጋላም ፡ አገር ፡ ስለ ተሰማ ፡ የብዙ ፡ አርበኞችን ፡ ምግባር ፡ አበረታታ ።

ብዙዎችም ፡ ሰዎች ፡ ከከተማው ፡ ውስጥ ፡ እየወጡ ፡ አርበኞች ፡ ሆኑ ።

ከብዙ ፡ ሰው ፡ ድምፅና ፡ ከብዙ ፡ ፕሮፓጋንዳ ፡ (ስብከት) ይልቅ ፡ የግፍና ፡ የጭንቅ ፡ የመከራ ፡ ያንድ ፡ ሰው ድምፅ ፡ አየርን ፡ ሠንጥቆ ፡ ይወጣል ።

እንሆ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ በደም ፡ የተነከረውን ፡ ፋስ ፡ በእጇዋ ፡ ይዛ ፡ ያገሬ ፡ ሰው ፡ እጅህን ፡ በጠላትኽ ፡ ላይ ፡ አንሣ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ የጕበዝ ፡ ያለኽ ፡ ብላ ፡ ስለ ፡ ጮኸች ፡ ከምሥራቅ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፤ ከሰሜን ፡ እስከ ፡ ደቡብ ፡ የተዳፈነው ፡ እሳት ፡ ተቈሰቈሰ ።

——==——

የማይ ፡ ጨው ፡ ጦርነትና ፡

ባጭሩ ፡ የዓለም ፡ ፖለቲካ ።

የማይ ፡ ጨው ፡ ጦርነትና ፡ ባጭሩ ፡ የዓለም ፡ ፖለቲካ ።

ባ፲፱፻፳፰ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡ መጋቢት ፡ ፳፱ ፡ ቀን ፡ ግር ማዊነታቸው ፡ በማይጨው ፡ ጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ የሚገባቸ ውን ፡ የአርበኝነት ፡ ምግባር ፡ ከፈጸሙ ፡ በኋላ ፡ ብጠላት ፡ ቦም ባርደማና ፡ በጋዝ ፡ አስፌክሲ ፡ በሌላም ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ መርዝ ፡ ምክንያት ፡ የጦር ፡ ሠራዊቱ ፡ ምግባር ፡ ወደቀ ። ኀይሉም ፡ ተሰ በረ ፤ ተበታተነም ፤

ስለዚህ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ሰይፋቸውን ፡ መዘው ፡ እናንት ፡ አርበኞች ፡ ወታደሮች ፡ ሆይ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥታችሁን ፡ በጦር ፡ ሜዳ ላይ ፡ ጥላችሁ ፡ ወዴት ፡ ትመለሳላችሁ ፡ በውነት ፡ በታሪክ ፡ ፊት ፡ የሚያስጠይፍ ፡ የሚያሳፍር ፡ ኀጢአት ፡ አይደለምን ፡ እያሉ ፡ ቢጮኹም ፡ የኢትዮጵያ ፡ ወታደር ፡ ካቅሙ ፡ በላይ ፡ በሆነው ፡ መሣሪያ ፡ ምክንያት ፡ ምግባሩን ፡ ለማበርታት ፡ አልተቻለውም ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ የድል ፡ ድንጋጤ ፡ በጦሩ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ፈሰሰና ፡ የጦር ፡ ሜዳውን ፡ የሞት ፡ ጥላ ፡ ስላጨለመው ፡ መሬት ፡ ስለ ፡ ከዳች ፡ ክፍ ፡ ያለው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ልጆች ፡ የጦር ፡ ምግ ባር ፡ እንደ ፡ ባቢሎን ፡ ግንብ ፡ ስለ ፡ ፈረሰ ፡ መታዘዝ ፡ መስማማት ፡ መተባበር ፡ ስለ ፡ ጠፋ ፡ ወንድም ፡ የወንድሙን ፡ ሬሳ ፡ እየረገጠ ፡ ወደ ፡ ኋላው ፡ ተመለሰ ።

ስለዚህ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ከእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ሽብር ፡ መካከል ፡ በመከራና ፡ በሥቃይ ፡ መንግሥታቸውን ፡ ለማቋቋም ፡ ወደ ፡ መና ገሻ ፡ ከተማቸው ፡ ተመለሱ ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ አገር ፡ በድል ፡ ከተመታ ፡ ወዲህ ፡ መልሶ ፡ ማቋቋም ፡ ችግር ፡ ሆነ ።

ምክንያቱም ፡ የጠላታችን ፡ መሣሪያ ፡ ካቅማችን ፡ በላይ ፡ ከመ ሆኑም ፡ በቀር ፡ በዓለም ፡ መንግሥታት ፡ ማኅበር ፡ የተከለከለውን ፡ መርዝ ፡ የፋሺስት ፡ መንግሥት ፡ ያለልክ ፡ በጦሩ ፡ ላይ ፡ ስላፈሰሰው ፡ ፊቱ ፡ በመርዝ ፡ የተቃጠለው ፡ ዐይኑ ፡ የፈሰሰው ፡ እጅና ፡ እግሩ ፡ የተቈረጠው ፡ ከጦሩ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ እየተመለሰ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ስለ ፡ ገባ ፡ የከተማው ፡ ነዋሪ ፡ ሕዝብ ፡ ተሸበረ ፤ መንግሥቱንም ፡ መልሶ ፡ ለማቋቋም ፡ የማይቻል ፡ የማይያያዝ ፡ ነገር ፡ ሆነ ።

ስለዚህ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ በእንደዚህ ፡ ያለ ፡ ሽብር ፡ ውስጥ ፡ ከመሞት ፡ በኢትዮጵያ ፡ ላይ ፡ የተሠራውን ፡ ግፍና ፡ በደል ፡ ለዓለም ፡ መንግሥታት ፡ ማኅበር ፡ ለማመልከት ፡ ወደ ፡ ሮፓ ፡ መሄድ ፡ የበለጠ ፡ አገልግሎት ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ በምክር ፡ ስለ ፡ ተቈረጠ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ በምድር ፡ ባቡር ፡ ጒዞ ፡ ዠመሩ ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ እኛ ፡ የይሉባቦርና ፡ የገሙ ፡ ጐፋ ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ በውጋዴ ፡ ውስጥ ፡ በሚገኘው ፡ ጀነጋብ ፡ በሚባለው ፡ ሸለቆ ፡ ውስጥ ፡ የሚገባንን ፡ ተግባር ፡ ከፈጸምን ፡ በኋላ ፡ የጅ ጅጋ ፡ ከተማ ፡ ዋናው ፡ የሥንቅና ፡ የመሣሪያ ፡ መከማቻው ፡ በቦምብ ፡ ስለ ፡ ተቃጠለ ፡ የጦሩ ፡ ሠራዊት ፡ ሥንቅ ፡ በማጣቱ ፡ ከቦምባርደማና ፡ ከጋዝ ፡ አስፊክሲው ፡ ከሌላውም ፡ መርዝ ፡ ይልቅ ፡ በችጋሩ ፡ ምክንያት ፡ ያቅም ፡ ድካምና ፡ የምግባር ፡ መውደቅ ፡ በኛም ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ላይ ፡ ደረሰበት ።

ስለዚህ ፡ ወደ ፡ ኋላችን ፡ እያፈገፈግን ፡ ሐረርጌ ፡ ከደረስን ፡ በኋላ ፡ ሁለተኛ ፡ ጦር ፡ ሰብስበን ፡ ከጅጅጋ ፡ ላይ ፡ ጠላትን ፡ ለመግ ጠም ፡ ቈረጥን ።

ነገር ፡ ግን ፡ በጀነጋብና ፡ በብርቆት ፡ የጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ በብ ርቱ ፡ የቈሰሉና ፡ በመርዝ ፡ ሰውነታቸው ፡ የተበላሸ ፡ ወታደሮች ፡ እየሸሹ ፡ ደጋ ፡ ሐቡር ፡ ከተማ ፡ ስለ ፡ ገቡና ፡ በከተማው ፡ ያለ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ በድንጋጤ ፡ ስለ ፡ ፈረሰ ፡ ደጋ ፡ ሐቡርና ፡ ጅጅጋ ፡ ያለው ፡ ጦር ፡ ጠቅሎ ፡ ወደ ፡ ሐረርጌ ፡ ከተማ ፡ ወጣ ።

የይሉባቦርና ፡ የገሙ ፡ ጐፋ ፡ ጦር ፡ ጠቅላዮች ፡ የተረፉትን ፡ አርበኞቻችንን ፡ ይዘን ፡ በወንድሞቻችን ፡ ሬሳ ፡ ላይ ፡ በጭቆ ፡ በኩል ፡ የሰገንን ፡ ወንዝ ፡ ይዘን ፡ በፊቅ ፡ በኩል ፡ በብዙ ፡ ድካምና ፡ ጦርነት ፡ ሚደጋ ፡ አሉላ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ደረስን ።

ከዚያች ፡ ትንሽ ፡ ከተማ ፡ ውስጥ ፡ ስልክ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ጅጅ ጋና ፡ ደጋ ፡ ሐቡር ፡ ደውለን ፡ የጦሩን ፡ አኳኋን ፡ ለመጠየቅ ፡ ሄድን። ለስልከኛው ፡ ጅጅጋና ፡ ደጋ ፡ ሐቡር ፡ ደውሎ ፡ ሰው ፡ እንዲያቀርብ ልን ፡ ነገርነው ።

ስልከኛውም ፡ በማሽሚጠጥና ፡ በንቀት ፡ በድፍረት ፡ አኳኋን ፡ ደጋ ፡ ሐቡር ፡ ምንም ፡ ሰው ፡ የለም ፡ የጅጅጋም ፡ የጦር ፡ አለቆች ፡ ወደ ፡ ሐረር ፡ ከወጡ ፡ ካንድ ፡ ወር ፡ ይበልጣል ፤ እናንተም ፡ ሞታ ችኋል ፡ ተብሎ ፡ ለሐረር ፡ ባለሥልጣኖች ፡ ተላልፏል ፤ ግርማዊ ነታቸውም ፡ ትላትና ፡ ወደ ፡ ድሬ ፡ ዳዋ ፡ መጥተዋል ፡ ይባላል ፡ አለን።

እኔም ፡ ለስልከኛው ፡ ምንድነው ፡ የመጡበት ፤ ምክንያት ፡ ብዬ ጠየቅኹት ።

ስልከኛውም ፡ ዲስፒሊን ፡ በሌለው ፡ አመላለስ ፡ እኔ ፡ አላውቅም ፡ ብትፈልጉ ፡ ከፊታውራሪ ፡ ተሰማ ፡ ባንቴ ፡ ላገናኛችሁና ፡ ተነጋገሩ ፡ አለኝ ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ የደረሰብን ፡ ኀዘን ፡ ምን ፡ ብሎ፡ ይወራል ፡ እኔና ፡ የጦር ፡ ጓደኛዬ ፡ በድንጋጤ ፡ ዐይን ፡ ላይን ፡ እንተያይ ፡ ዠመር ።

ዐሥር ፡ ደቂቃ ፡ ያኽል ፡ በድንጋጤ ፡ ደርቀን ፡ ከቈየን ፡ በኋላ፡ የገሙ ፡ ጐፋ ፡ ጦር ፡ ጠቅላይ ፡ በቊጣ ፡ ስለ ፡ ምንድነው ፡ የመንግሥት ፡ ሠራተኛ ፡ ሆነኽ ፡ የምንጠይቅኽን ፡ ነገር ፡ በሥራት ፡ የማትመልስልን ፡ ብሎ ፡ ጠየቀው ።

ስልከኛውም ፡ ከዚህ ፡ የበለጠ ፡ ምን ፡ ልንገራችሁ ፡ ብሎ ፡ ተቈጣ ። በዚያ ፡ ጊዜ ፡ እኔም ፡ የጦር ፡ ጓደኛዬም ፡ ኢትዮጵያ ፡ እንደ፡ ፈረሰችና ፡ ድል ፡ እንደ ፡ ተመታን ፡ በስልከኛው ፡ ሰው ፡ ግንባር ፡ ተጽፎ ፡ አየነው ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በኀዘንና ፡ በትካዜ ፡ የቴሌፎኑን ፡ መስሚያ ፡ አንሥቼ ፡ ሐረር ፡ የቀረበውን ፡ ደጃዝማች ፡ ተሰማ ፡ ባንቴን ፡ አነጋግረው ፡ ዠመር ።

ደጃዝማች ፡ ተሰማ ፡ ባንቴም ፡ የኛን ፡ ደኅንነት ፡ መላልሶ ፡ ከጠየቀ፡በኋላ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ግርማዊት ፡ እቴጌን ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም፡ሸኝተው ፡ ለመመለስ ፡ ትላንት ፤ ድሬ፡ ዳዋ ፡ ገብተዋል ። እናንተም ፡ መጥታችሁ ፡ ብታዩዋቸውና ፡ ስለ ፡ ጦሩም ፡ ነገር ፡ ብትመካከሩ ፡ መልካም ፡ ነው ፡ አለኝ።

እኔም ፡ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ የግርማዊነታቸውን ፡ መምጣት ፡ ስለ ፡ ነገርኸኝ ፡ በጣም ፡ እናመሰግንኻለን ፤ ነገር ፡ ግን ፡ እኛም ፡ የጦር ፡ ሠራዊቱም ፡ በጣም ፡ ስለ ፡ ደከመን ፡ በፍጥነት ፡ ሐረር፡ ድረስ ፡ ለመምጣት ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይቻላል ።

ደጃዝማች ፡ ተሰማ ፡ ምንም ፡ መንገዱ ፡ መጥፎ ፡ ቢሆን ፡ እንደ ፡ ምንም ፡ ብዬ ፡ አንድ ፡ ካሚዎን ፡ እልክላችኋለሁና ፡ ጦሩን፡ ትታችሁ ፡ አንዳንድ ፡ አሽከር ፡ አስከትላችሁ ፡ ኑና ፡ ከግርማዊነታቸው ፡ ከተነጋገራችሁ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ሥራችሁ ፡ ትመለሳላችሁ ፡ አለኝ ።

እኔም ፡ በጦር ፡ ጓደኛዬና ፡ በኔም ፡ ስም ፡ አመስግኘው ፡ ወደ ፡ ሰፈራችን ፡ ተመለስን ።

የጦር ፡ ጓደኛዬ ፡ ወንድሜ ፡ የወንድሞቻችንና ፡ ያሽከሮቻችን ፡ በመንገድ ፡ የፈሰሰው ፡ ደም ፡ አሰቅቆናል ፡ እንጂ ፡ ይህ ፡ ስልከኛ ፡ የሚገደል ፡ ሰው ፡ ነበር ፡ አለኝ ።

እኔም ፡ ርግጥ ፡ ነው ፡ መልኩ ፡ በገሩ ፡ ጥፋት ፡ ደስ ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ ይመስላል ። ነገር ፡ ግን ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ መሪ ፡ እንደሌለው ፡ መርከብ ፡ የሚደርስበትን ፡ አላወቀውምና ፡ እንተወው ። ይልቁንስ ፡ ሌላ ፡ የቁም ፡ ነገር ፡ ጨዋታ ፡ እንጨዋት ፡ አልኩትና ፡ ብዙ ፡ የቁም ፡ ነገሮች ፡ ጨዋታ ፡ ስንጫወት ፡ የምሳ ፡ ጊዜ ፡ ደረሰ ።

ምሳችንን ፡ ከበላን ፡ በኋላ ፡ በ፱ ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ ካሚዎኑ ፡ መጣልን ። የጦር ፡ ጓደኛዬና ፡ እኔ ፡ አንዳንድ ፡ አሽከር ፡ ይዘን ፡ ተሳፍረን ። በመንገዱ ፡ መጥፎነት ፡ ምክንያት ፡ ከሌሊቱ ፡ ባ፫ ፡ ሰዓት ፡ ሐረርጌ ፡ ከተማ ፡ ገባን ።

ጊዜው ፡ ስለ ፡ ተላለፈ ፡ ይልቁንም ፡ የኢትዮጵያን ፡ ሞት ፡ ለማርዳት ፡ ሲሉ ፡ አንድም ፡ ሰው ፡ መጥቶ ፡ ሳያየን ፡ የፈረስ ፡ ኩቴ ፡ ከሚባለው ፡ ቤት ፡ ገብተን ፡ ተኛን ። ከሌሊቱ ፡ በ፲፩ ፡ ሰዓት ፡ ደጃዝማች ፡ ነሲቡ ፤ ደጃዝማች ፡ ዐምዴ ፤ ደጃዝማች ፡ ሀብተ ፡ ሚካኤል ፤ ደጃማች ፡ ተሰማ ፡ ባንቴ ፤ ጄኔራል ፡ ወሂብ ፡ ፓሻ ፡ ሌሎችም ፡ መኳንንት ፡ ሆነው ፡ ወደኛ ፡ መጡ ።

እኛም ፡ ልብሳችንን ፡ እንደ ፡ ለበስን ፡ ነበርና ፡ የተጋደም ነው ፡ ከውጭ ፡ ለቅሶ ፡ ሲዠመር ፡ ደንግጠን ፡ ተነሣን ። እነሱም ፡ ገብተው ፡ ምክንያቱን ፡ ሳይነግሩን ፡ ያለቅሱ ፡ ዠመር ። እኛም ፡ ምክንያቱን ፡ ሳናውቅ ፡ አብረን ፡ እናለቅስ ፡ ነበር ። እንደዚሁ ፡ እያለቀስን ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ከቈየን ፡ በኋላ ፡ ደጃዝማች ፡ ነሲቡ ፡ ብድግ ፡ ብሎ ፡ ከግርማዊነታቸው ፡ የመጣውን ፡ ቴሌግራም ፡ አነበበልን ። ሁላችንም ፡ በጠለቀ ፡ ኀዘን ፡ ጥቂት ፡ ጊዜ ፡ ዝም ፡ ብለን ፡ እናስብ ፡ ዠመር ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጄኔራል ፡ ወሂብ ፡ ፓሻ ፡ እኔን ፡ ለብቻዬ ፡ ጠርተው ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ ወጥተን ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ ይህች ፡ ሰዓት ፡ እንደዚህ ፡ በዝምታ ፡ የምናሳልፋት አይደለችም ፡ ጊዜዋ ፡ አጭር ፡ ስለ ፡ ሆነች ፡ በቶሎ ፡ ከሁለት ፡ ነገሮች ፡ አንዱን ፡ መምረጥ ፡ ያስፈልጋል ፡ አሉኝ ።

እኔም ፡ የምንመርጣቸው ፡ ነገሮች ፡ ምን ፡ ምን ፡ ናቸው ፡ ብዬ፡ ጠየቅኋቸው ።

ጀኔራል ፡ ወሂብ ፡ ፓሻም ፡ አንደኛው ፡ መሞት ፡ ሁለተኛውም፡ ስደት ፡ ነው ፡ አሉኝ ።

እኔም ፡ ሁለቱም ፡ ያው ፡ ሞት ፡ ማለት ፡ ነው ፡ እርስዎ ፡ የትኛ ውን ፡ ይመርጣሉ ፡ አልኋቸው ።

ጀኔራል ፡ ወሂብ ፡ ፓሻም ፡ እኔ ፡ መዠመሪያ ፡ የማደርገው ፡ በኢትዮጵያ ፡ ላይ ፡ ትልቅ ፡ ታሪክ ፡ ለመተው ፡ ሽጉጥ ፡ ጠጥቶ ፡ የክብር ፡ ሞት ፡ መሞትን ፡ ነው ። ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ሁለተኛው ፡ በጠ ላት ፡ እጅ ፡ ከመውደቅ ፡ ቶሎ ፡ ብሎ ፡ ጨክኖ ፡ መሰደድ ፡ ነው ።

በእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ነፃነታችሁም ፡ ቢመለስ ፡ ኢትዮጵ ያን ፡ መልሶ ፡ ለማቋቋም ፡ ጠቃሚ ፡ ትሆናላችሁ ።

ይህም ፡ ባይሆን ፡ እውነትን ፡ ተደግፋችሁ ፡ በባዕድ ፡ አገር ፡ በችጋር ፡ ብትሞቱ ፡ ዋጋ ፡ ያለው ፡ የክብር ፡ ሞት ፡ ነው ፡ አሉኝ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ጦር ፡ ጠቅላዮቼ ፡ ገብቼ ፡ ጀኔራል ፡ ወሂብ ፡ ፓሻ ፡ የነገሩኝን ፡ የቈራጥነት ፡ መንፈስ ፡ ያለበትን ፡ ምክር፡ ከነገርኋቸው ፡ በኋላ ፡ ብዙ ፡ ክርክር ፡ አድርገን ፡ በመጨረሻ ፡ መሰ ደድን ፡ መርጠን ፡ ከግርማዊነታቸው ፡ ጋራ ፡ ለመገናኘት ፡ ወደ ፡ ድሬ ፡ ዳዋ ፡ በካሚዎን ፡ ተጓዝን ።

ነገር ፡ ግን ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ወደ ፡ ጅቡቲ ፡ ስለ ፡ ሄዱ ፡ ለመ ገናኘት ፡ አልቻልንም ፤ ቢሆንም ፡ ጠላት ፡ እየገፋ ፡ አዋሽ ፡ ስለ ፡ ደረሰ ፡ ሁላችንም ፡ ገንዘብ ፡ አዋጥተን ፡ ከጧቱ ፡ በ፩ ፡ ሰዓት ፡ በልዩ ፡ ባቡር ፡ ወደ ፡ ጅቡቲ ፡ ተጓዝን ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከዛፍ ፡ሥር ፡ ተቀምጦ ፡ በዕንባዬ፡ ሰሌዳ ፡ ላይ ፡ ተጽፎ ፡ የሚታየኝ ፡ ይህ ፡ ቤትኽ ፡ አይደለም ፡ ሚስት ኽም ፡ ያንተ ፡ አይደለች ፡ የረገጥኻት ፡ መሬት ፡ እንኳ ፡ የጠላት ፡ ናት ፡ የሚል ፡ ነው ፤ እንግዴህ ፡ ማነኝ ፡ ሻቴ ፡ ተማቹ ፡ አይደለ ሁምን ፡ እያለ ፡ በጽኑ ፡ ኀዘን ፡ እንዳሰበ ፡ ሁሉ ፡ እኛም ፡ የተፈጠርን ባት ፡ ውድ ፡ አገራችን ፡ የጠላት ፡ መሬት ፡ በመሆኗ ፡ በላይዋ ፡ ላይ ፡ ለመቆም ፡ ስለ ፡ ፈራን ፡ ከባቡሩ ፡ ለመውጣት ፡ ስንጣደፍ ፡ ይህ ፡ ጽሑፍ ፡ ትዝ ፡ ብሎኝ ፡ በጣም ፡ አዘንኹ ።

ከአኩል ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ዐሥር ፡ ሰዓት ፡ ላይ ፡ ከድሬ ፡ ዳዋ ፡ ተነሥተን ፡ ግርማዊነታቸውን ፡ ባንድ ፡ አንትርፕራይዝ ፡ «ENTREPRISE» በሚባል ፡ የእንግሊዝ ፡ መንግሥት ፡ የጦር ፡ መርከብ ፡ ላይ ፡ ተገናኘን ።

በዚያ ፡ ሰዓት ፡ ከኢትዮጵያ ፡ ጋራ ፡ የመጨረሻ ፡ ስንብታችን፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በመረረ ፡ ኀዘንና ፡ ለቅሶ ፡ በጥቍር ፡ ደመና ፡ በተሸፈነ ፡ ጊዜ ፡ አሳለፍነው ።

በዚያች ፡ የቀቢጸ ፡ ተስፋ ፡ ጨለማ ፡ በሸፈናት ፡ የኀዘን ፡ ቀን ፡ ውስጥ ፡ ከግርማዊነታቸው ፡ የሰማሁት ፡ ቃል ፡ ከማይረሱኝ ፡ ነገሮች ፡ አንዱ ፡ እሱ ፡ ነው ።

የግርማዊነታቸው ፡ ቃል ፡ ሞትን ፡ ብፈልግ ፡ አጣሁ ፡ ሦስት ፡ ክንድ ፡ መሬት ፡ እንኳ ፡ ካገሬ ፡ ላይ ፡ ለመቃብር ፡ የሚሆን ፡ አላገኘሁም ፡ የሚል ፡ ነው ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ በመከራና ፡ በጦር ፡ ሥቃይ ፡ በወንድሞቻችን ፡ ደም ፡ ስለ ፡ ሰከርን ፡ ደንዝዘን ፡ የረሳነው ፡ ካገር ፡ ላይ ፡ ተነቅለን ፡ በባዕድ ፡ አገር ፡ ላይ ፡ መጣል ፡ በግርማዊነታቸው ፡ የመረረ ፡ ኀዘን፡ ምክንያት ፡ ስለ ፡ ታሰበኝ ፡ እኔም ፡ የመረረ ፡ ለቅሶ ፡ አለቀስሁ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ በ፲፱፻፳፰ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ሚያዝያ፡ ፳፬ ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ ቅድስት ፡ አገር ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተጓዙ ።

እኛም ፡ ከጥቂት ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ በማሳጀሪ ፡ ማሪቲም ፡ መርከብ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ተከተልን ።

እኛ ፡ በገባን ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ ግርማዊነታቸው ፡ የመጡበትን ፡ የፖለቲካ ፡ ጉዳይ ፡ ለመቀጠል ፡ ወደ ፡ ሎንዶን ፡ ጉዞ ፡ አደረጉ።

ሰኔ ፡ ፳፫ ፡ ቀን ፡ ፲፱፻፳፰ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ወደ ፡ ዠኔብ ፡ ለዓለም ፡ መንግሥታት ፡ ማኅበር ፡ የኢትዮጵያን ፡ ግፍ ፡ ለማመልከት ፡ ሄዱ ።

በመሰብሰቢያው ፡ አዳራሽ ፡ ውስጥ ፡ ከመግባት ፡ እንዲከለከሉ ፡ ስንት ፡ መሰናክልና ፡ ወጥመድ ፡ ተዘረጋ ።

ብዙዎችም ፡ መንግሥታት ፡ የግርማዊነታቸው ፡ በዓለም ፡ ጉባኤ ፡ መካከል ፡ መገኘት ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ ይነሣል ፡ ተብሎ ፡ የተፈራውን ፡ ጦርነት ፡ ይቀሰቅሳል ፡ በማለት ፡ ተቃወሙ ።

ነገር ፡ ግን ፡ በብዙ ፡ ድካምና ፡ ባለመመረር ፡ የኢትዮጵያን ፡ ግፍና ፡ መከራ ፡ ለመናገር ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ዋጋ ፡ ያለው ፡ ዕድል ፡ አገኙ ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ግፈኞችና ፡ ባለጌዎች ፡ ፋሺስቶች ፡ በግርማዊነታቸው ፡ አፏጨባቸው ፤ ታሪካዊ ፡ የሆነውን ፡ ቃል ፡ ማኅበሩ ፡ እንዳይሰማ ፡ ውካታ ፡ አበዙ ።

ስለዚህ ፡ የሮማኒ ፡ መንግሥት ፡ ጠቅላይ ፡ ሚኒስትር ፡ ኒኮላ ፡ ቲቱሊስኮ ፡ «NICOLA TITULESCU» የሚባለው ፡ ጎሊናው ፡ አስደፍሮት ፡ ብድግ ፡ ብሎ ፡ እነዚህን ፡ እድፋሞች ፡ ከዚህ ፡ ጠር ጋችሁ ፡ አስወጡ ፡ ብሎ ፡ ጮኸ ፡ ተናገረ ።

ወዲያው ፡ በኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ላይ ፡ የተደረገውን ፡ ግፍና ፡ የጣሊያኖችን ፡ እብሪትና ፡ ብልግና ፡ በማየቱ ፡ ከዚያው ፡ ከማኅበሩ ፡ ውስጥ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ራሱን ፡ በሽጉጥ ፡ ለመግደል ፡ ተኰሰ ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ በመሰብሰብያው ፡ ውስጥ ፡ ያሉ ፡ ሕዝቦችና ፡ መል ክተኞች ፡ ተሸበሩ ። አንዳንዶቹም ፡ ፋሺስቶች ፡ በግርማዊነታቸው ፡ ላይ ፡ የተኰሱባቸው ፡ መስሏቸው ፡ እየወጡ ፡ ሄዱ ።

ግርማዊነታቸው ፡ ግን ፡ በፀጥታ ፡ በደመ ፡ በራድነት ፡ ቀጥ ፡ ብለው ፡ ቆመው ፡ ደማቸው ፡ በፈሰሰ ፡ ጊዜ ፡ በእጃቸው ፡ ከማኅበሩ ፡ ጠረጴዛ ፡ ላይ ፡ ረጭተው ፡ ይህ ፡ ደም ፡ እንደ ፡ አቤል ፡ ደም ፡ ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ይፋረድ ፡ ብለው ፡ ለመውደቅ ፡ ይጠባበቁ ፡ ነበር ።

ከዚያም ፡ በኋላ ፡ ካረፉበት ፡ ሆቴል ፡ በራፍ ፡ ላይ ፡ ለመግደል ፡ እንደ ፡ ተፈረደባቸው ፡ ለማስታወቅ ፡ የሰው ፡ ሀዕም ፡ እየሣሉ ፡ ይሰ ቅሉ ፡ ነበር ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አቶ ፡ ተማቹ ፡ በጄኔቃብ፡ጦር፡ሜዳ ፡ ላይ ፡ ለመከላ ከያ ፡ ምክንያት ፡ እንዳይሆነው ፡ መሣሪያውን ፡ ወርውሮ ፡ የሞት ፡ ጥላ ፡ በጨለመው ፡ የጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ አውሬዎች ፡ እንዲበሉትና ፡ ሉማሌዎች ፡ እንዲገድሉት ፡ በትሩን ፡ ይዞ ፡ የሚጓዘው ፡ ትዝ ፡ አለኝ ።

ግርማዊነታቸውም ፡ አንድም ፡ ሴኩሪቲ ፡ አንድም ፡ ጥንቃቄ ፡ ሳይደረግላቸው ፡ ምርኵዛቸውን ፡ ይዘው ፡ በፋሺስት ፡ መካከል ፡ ያላ ንድ ፡ ፍራት ፡ የመጡበትን ፡ ተግባር ፡ ፈጽመው ፡ ወደ ፡ ሎንዶን ፡ ተመለሱ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ዓለም ፡ በጣም፡እየተበላሸ ፡ ይሄድ፡ገመር።ከፍ ፡ ያሉ ፡ የዓለም ፡ መንግሥታት ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ የሚነሣውን ፡ ጦር ፡ ለማ ስቀረት ፡ ታናናሾችን ፡ መንግሥቶች ፡ ለዲክታተሮች ፡ ማጉረሥ ፡ መልካም ፡ መስሎ ፡ ታያቸው ።

ሙኒክ ፡ ላይ ፡ ሻንበርለ ፡ ቸኮስሎቫኪን ፡ ለሂትለር ፡ አጉርሦ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ የፈረንሳዊና ፡ የእንግሊዝ ፡ ሕዝብ ፡ መጠን፡የሌለው ፡ ደስታ ፡ አደረጉ ። ምክንያቱም ፡ በቃኝ ፡ የማይል ፡ የዲክታተር ፡ መሪ ፡

ሂትለር ፡ ቸኮስሎቫኪን ፡ በመጐረሡ ፡ ጠግቦ ፡ ይተኛል ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ሰላም ፡ ይሆናል ፡ በማለት ፡ ነበር ።



ቻምበርለርና ፡ ሂትለር ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ዓለም ፡ ታውሮ ፡ እያየ ፡ አያስተውልም ፡ ኑሯል ፤ የሚገርመው ፡ የፓሪስ ፡ የማዘጋጃ ፡ ቤት ፡ አማካሪዎች ፡ ሠላሳ ፡ መስከረም ፡ ብለን ፡ ለመንገድ ፡ ስም ፡ እናውጣ ፡ ብለው ፡ አሳብ ፡

አቀረቡ ። እሁሉም ፡ ሳይደርሱ ፡ ጀርመን ፡ ከፕራግ ፡ «PRAGUE» በገባ ፡ ጊዜ ፡ ሻንበርለ ፡ ብርቱ ፡ በሆነ ፡ የፖለቲካ ፡ ጦር ፡ ተዋጋ ። ወዲያው ፡ ጀርመን ፡ በሮፓ ፡ ላይ ፡ የመስፋት ፡ አሳቡ ፡ እንዳልተወሰነ ፡ ታወቀ ። ፖሎኝንም ፡ ለመውጋት ፡ እንደ ፡ ቈረጠ ፡ ተገለጸ ።

የታላላቆች ፡ መንግሥቶች ፡ ሹሞች ፡ አሳብና ፡ ፖለቲካ ፡ ጦርን ፡ እንኳ ፡ ለማስቀረት ፡ ባይቻል ፡ ታናናሾችን ፡ መንግሥቶች ፡ ለናዚስትና ፡ ለፋሺስት ፡ ማጕረስ ፡ ለመዘጋጃ ፡ ቀን ፡ እንደሚገኝ ፡ አምነውበት ፡ ነበር ።

ለማስረጃ ፤ ሚስተር ፡ ቸርቺልና ፡ ምስተር ፡ አንድሬ ፡ ሞርዋ ፡ የተነጋገሩት ፡ በጣም ፡ ገልጦ ፡ ያስረዳል ።

ምስተር ፡ ሞርዋ ፡ ለምስተር ፡ ቸርቺል ፡ ስለ ፡ ምንድነው ፡ እንግሊዝ ፡ በጣሊያን ፡ መቀጫ ፡ በተፈረደበት ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ያፈገፈገችውና ፡ የፈቀደችው ።

ምስተር ፡ ቸርቺል ፡ ወዳጄ ፡ አንድሬ ፡ ሞርዋ ፡ የአርማን ፡ «HOMARD» ልምድ ፡ መከተል ፡ ያስፈልጋል ። ጊዜ ፡ ብታገኝ ፡ ልታጠናውም ፡ ይገባኻል ፡ በጣም ፡ አስፈላጊ ፡ ምሳሌ ፡ ነው ። አማር ፡ «HOMARD» የባሕር ፡ ውስጥ ፡ አውሬ ፡ በሕይወቱ ፡ ውስጥ ፡ ጥቂት ፡ በተለዩ ፡ ጊዜዎች ፡ እንደ ፡ ባልጩት ፡ ድንጋይ ፡ የጠነከሩ ፡ ቅርፊቶቹን ፡ ያጣል ፤ አሸናፊ ፡ አርበኛ ፡ የነበረው ፡ ወዳንዲት ፡ ቋጥኝ ፡ ጕድጓድ ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፡ ጊዜውን ፡ ያሳልፋል ። ከዚያም ፡ አዲስ ፡ ቅርፊት ፡ እስኪያወጣና ፡ ኀይሉን ፡ እስኪለብስ ፡ ድረስ ፡ አዲሱ ፡ መሣሪያ ፡ እንደ ፡ ባልጩት ፡ ድንጋይ ፡ ከጠነከረ ፡ በኋላ ፡ ከጕድጓዱ ፡ ይወጣና ፡ የባሕር ፡ ገዥ ፡ ሆኖ ፡ በአርበኝነት ፡ ይዋጋል ።

እንደዚሁም ፡ እንግሊዝ ፡ በሚኒስትሮቿ ፡ ዝንጉነትና ፡ ልፍስፍስነት ፡ እንደባልጩት ፡ ድንጋይ ፡ የጠነከረ ፡ ኀይሏን ፡ ጣለች ። ስለዚህ ፡ ይገባናል ፡ ከጕሬያችን ፡ ሆነን ፡ ኀይላችንን ፡ እስክናገኝ ፡ መጠባበቅ ፡ የሚል ፡ ንግግር ፡ ተለዋወጡ ።

በውነትም ፡ ስንመለከተው ፡ የእንግሊዝ ፡ መንግሥት ፡ ጀርመን ፡ በጦር ፡ እንደ ፡ ተዘጋጀች ፡ ሲያውቅ ፤ ጦር ፡ ይመጣል ፡ ብዬ ፡ ለወታደርና ፡ ለመሣሪያ ፡ ገንዘብ ፡ ከማጥፋት ፡ ገንዘብ ፡ ካለ ፡ በቶሎው ፡ ይደርሳል ፡ በማለት ፡ ይሆናል ።

ቢሆንም ፡ ቤት'ኽ ፡ ሳይቃጠል ፡ አስቀድመ'ኽ ፡ አሱራንስ ፡ ማኅበር ፡ መግባት ፡ ያስፈልጋል ፡ የተባለውን ፡ አለመርሳት ፡ ይገባ ፡ ነበር ። ባለመጠንቀቅ ፡ የጐደለውን ፡ ቀን ፡ ለማግኘት ፡ ብዙ ፡ የማያስተማምን ፡ የውርደት ፡ ሥራ ፡ ተሠራ ። ወዳጆችም ፡ ለጥቅም ፡ ተሼጡ ፡ ወዳጆች ፡ ለጥቅምና ፡ ጊዜ ፡ ለማግኘት ፡ በተሼጡበት ፡ ጊዜ ፡ ሊዮድ ፡ ጆርጅ ፡ ታሪካዊ ፡ የሆነ ፡ ቃል ፡ ካንድ ፡ ኮንፌራንስ ፡ ላይ ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ ተናገረ ፡ ጦር ፡ አይቀርልንም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ጦርነት ፡ የምናደርገው ፡ ወዳጆቻችንን ፡ ካጣን ፡ በኋላ ፡ ነው ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፤ እንግዴህ ፡ ነገሬን ፡ ላበዛ ፡ አልፈልግም ፡ ባጭሩ ፡ በኢትዮጵያና ፡ በሺን ፡ ላይ ፡ የተነሣው ፡ የሰደድ ፡ እሳት ፡ ዓለምን ፡ ሁሉ ፡ አቃጠለ ። ቢያንስ ፡ ቢያንስ ፡ የዓለም ፡ ሩብ ፡ በሰውም ፡ በገንዘብም ፡ በእሳት ፡ ውስጥ ፡ ተጣለ ። የብዙ ፡ ሕዝብ ፡ ቤት ፡ ተዳፈነ ፡ ብዙ ፡ ወጣቶች ፡ በእሳተ ፡ ገሞራ ፡ ተቃጠሉ ። ብዙ እናቶች ፡ መካን ፡ ሆኑ ፤ ብዙም ፡ ሴቶች ፡ ያለ ባል ፡ ተንከዋተው ፡ ቀሩ ።

ይህ ፡ ሁሉ ፡ የደረሰው ፡ በሦስት ፡ ሰዎች ፡ ዕብደትና ፡ የዓለም ፡ ማኅበር ፡ የገባችውን ፡ ግዴታ ፡ ባለማክበር ፡ ቃሏንም ፡ ባለመጠበቅ ፡ ነው ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሂትለር ፡ በዲስኩር ፡ ማሳመርና ፡ በጉራ ፡ በፉከራ ፡ አንድ ፡ ያደረገውን ፡ የናዚስት ፡ ወታደር ፡ በመካከል ፡ ሮፓ ፡ ላይ ፡ አፈሰሰው ።

ፈረንሳዊም ፡ አስቀድማ ፡ በሹማምቶቿ ፡ ገንዘብ ፡ መውደድና ፡ መንግሥቱን ፡ ዕለት ፡ በዕለት ፡ በመለወጥ ፡ በራፖር ፡ መጻፍና ፡ በኮሚሲዮን ፡ የመንግሥቱን ፡ ገንዘብ ፡ በመጨረስ ፡ እንደ ፡ ነቀርሳ ፡ ያለ ፡ ክፉ ፡ ደዌ ፡ ይዟት ፡ ነበርና ፡ ቆሎ ፡ ብላ ፡ ወደቀች ።

በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ሙሶሎኒ ፡ በማመዛዘን ፡ ላይ ፡ የነበረውን ፡ ፖለቲካ ፡ የፈረንሳዊን ፡ ቆሎ ፡ መውደቅ ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፡ ፍርሃት ፡ አዳፍሮት ፡ አንድ ፡ ወፍ ፡ ዘንዶ ፡ ስታይ ፡ በፍርሃት ፡ ከሰው ፡ ላይ ፡ እንደምትወድቅ ፡ ከጀርመን ፡ ጋራ ፡ አንድ መሆኑንና ፡ በጦሩ ፡ ውስጥ ፡ መግባቱን ፡ ለዓለም ፡ አስታወቀ ።

እኛም ፡ በእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ የእንግሊዝ ፡ መንግሥትና ፡ የኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ ጥቅምና ፡ ጉዳት ፡ የጋራ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሰኔ ፡ ፳፯ ፡ ቀን ፡ ፲፱፻፴፪ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ከሎንዶን ፡ ወደ

ካርቱም ፡ ግርማዊነታቸው ፡ እንዲሄዱና ፡ በጦር ፡ ኀይል ፡ ወዳገ ራቸው ፡ እንዲገቡ ፡ ተደረገ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ያገሬ ፡ ልጅ ፡ በጠላትኽ ፡ ላይ ፡ እጅኽን ፡ አንሣ ፡ ብለው ፡ በወርቅ ፡ ዐዋጃቸው ፡ ቢያስታ ውቁ ፡ ከምሥራቅ ፡ እስከ ፡ ምዕራብ ፡ ከሰሜን ፡ እስከ ፡ ደቡብ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ አንድ ፡ ሆነ ።



ሂትለር ፡ ዲስኩር ፡ ሲናገር ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ በደም ፡ የተነከረ ፡ ፋሷን ፡ ይዛ ፡ ከቋጥኝ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ ወጥታ ፡ ያገሬ ፡ ልጅ ፡ እጅኽን ፡ በጠ ላትኽ ፡ ላይ ፡ አንሣ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ እያለች ፡ የጮኽችው ፡ ትዝ ፡ አለኝና ፡ ተገረምሁ ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክና ፡ ተረት ፡ እውነት ፡ ሆኖ ፡ ማየት ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ዕድል ፡ ነው ።

መከራ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ማጣሪያ ፡ ነው ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ግርማዊነታቸው ፡ በመከራ ፡ ተጣርተው ፡ ስለ ፡ መጡ ፡ ሕዝባቸውን ፡ ባንዲት ፡ ቃል ፡ ቢጠሩት ፡ ከጠረፍ ፡ እስከ ፡ ጠረፍ ፡ ባንድነት ፡ እጁን ፡ በጠላቱ ፡ ላይ ፡ አነሣ ።



በይቅርታ ፡ ጕዳና ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ጥር ፡ ፲፪ ፡ ቀን ፡ ፲፱፻፴፫ ፡ ዓ ፡ ም ፡ በግፈኛው ፡ ፋሺስት ፡ ተነቅላ ፡ ወድቃ ፡ የነበረችውን ፡ ሰንደቅ ፡ ዓላማችንን ፡ ግርማዊነታቸው ፡ አሜደላ ፡ መሬት ፡ ላይ ፡ አቁመው ፡ በይቅርታ ፡ ጐዳና ፡ ወደ ፡ ፍኖተ ፡ ሰላም ፡ ተጓዙን ።

ከአሜድላ ፡ ተነሥተን ፡ እስከ ፡ በላያ ፡ ድረስ ፡ በእግርና ፡ በፈረስ ፡ ብዙ ፡ ችግር ፡ ያለበት ፡ ጕዞ ፡ አደረግን ። በየካቲት ፡ ፳፯ ፡ እኔ ፡ የነበርኩበት ፡ካሚዮን ፡ ከክፉ ፡ ሦፍራ ፡ ላይ ፡ ተገልብጦ በእግዚአብሔር ፡ ቸርነት ፡ ከአደጋ ፡ ዳንሁ ። ምንም ፡ ብዙ ፡ ችግር ፡ በመንገዳችን ፡ ላይ ፡ ቢገጥመን ፡ እንኳ ፡ ያገራችን ፡ ተራሮችና ፡ ወንዞች ፡ በሩቁ ፡ እየሸተቱን ፡ የበረሓው ፡ ሙቀት ፡ ያገሩ ፡ ዐቀበትና ፡ ቍልቍለትነት ፡ ምንም ፡ አይሰማንም ፡ ነበር ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ በበረሓው ፡ ውስጥ ፡ ሰፍረን ፡ የድካም ፡ ጣፋጭ ፡ እንቅልፍ ፡ ሽልብ ባደረገን ፡ ጊዜ ፡ የኢትዮጵያ ፡ አንበሶች ፡ ሲያገሡ ፡ ዕንባችንና ፡ ርስ ፡ በርሳችን ፡ አሽናፊው ፡ የይሁዳ ፡ አንበሳ ፡ ጠላቱን ፡ ሊሰብር ፡ ያገሣል ፡ ይህ ፡ የመንግሥታችን ፡ ኀይል ፡ ምልክት ፡ ነው ፡ እያልን ፡ እንጫወት ፡ ነበር ።

ከበላያ ፡ ከደረስን ፡ በኋላ ፡ ጥቂት ፡ በርከት ፡ ያሉ ፡ ቀኖች ፡ ካንዲት ፡ ወንዝ ፡ አጠገብ ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ሸለቆውን ፡ ይዘን ፡ ሰፈርን ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በመተከል ፡ በኩል ፡ በአስኩና ፡ መካከል ፡ ወደ እንጀባራ ፡ ከተማ ፡ ሄደን ፡ የፋሺስት ፡ ምርኮኞች ፡ ከግርማዊነታቸው ፡ ፊት ፡ ቀርበው ፡ ከታዩ ፡ በኋላ ፡ የሚያስፈልጋቸውን ፡ ምግብና ፡ ልብስ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ አዘውላቸው ፡ ወደ ፡ ቡሬ ፡ ጕዟችንን ፡ ቀጠልን ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ዳንግላም ፡ ቡሬም ፡ ያለው ፡ የፋሺስት ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ እንደ ፡ ሰናክሬም ፡ ጦር ፡ መቶው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ወታደር ፡ ዐሥሩን ፡ ሺሕ ፡ የፋሺስት ፡ ወታደር ፡ እያሳደደው ፡ የቡሬም ፡ በሌላም ሦፍራ ያለው ፡ የጠላት ፡ ጦር ፡ የኢትዮጵያ ፡ ወታደሮች ፡ ብዙውን ፡ በተኵስ ፡ እያስቀሩት ፡ የተረፈው ፡ ተሰብስቦ ፡ ደብረ ፡ ማርቆስ ፡ ከተማ ፡ ገባ ።

ግርማዊነታቸውም ፡ ጥቂት ፡ ቀን ፡ ከቡሬ ፡ ከተማ ፡ ወጣ ፡ ብለው ከሰፈሩ ፡ በኋላ ፡ ጀኔራል ፡ ናዚ ፡ ጦሩንና ፡ የኢትዮጵያን ፡ ሰንደቅ ዓላማ ፡ ለልዑል ፡ ራስ ፡ ኃይሉ ፡ አስረክቦ ፡ ወደ ፡ ጐንደር ፡ ባይሮፕላን ፡ መሸሹን ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ስለ ፡ ሰሙ ፡ ማታውኑ ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ማርቆስ ፡ በጦር ፡ ካሚዎን ፡ ገሠገሡን ። ከእኩለ ፡ ሌሊት ፡ በኋላ ፡ መብራታችንን ፡ አጥፍተን ፡ በብዙ ፡ ችግር ፡ የኢትዮጵያ ፡ አርበኞችና ፡ የእንግሊዝ ፡ መንግሥት ፡ የጦር ፡ ኃይል ፡ ካለበት ፡ ሰፈር ገባን ። በማግሥቱ ፡ ማለዳ ፡ ከግርማዊነታቸው ፡ ድንኳን ፡ ውስጥ ፡ ተሰብስበን ፡ ለልዑል ፡ ራስ ፡ ኃይሉ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ከዚህ ፡ መምጣታቸውን ፡ እንላክባቸውና ፡ የኛ ፡ መሆናቸውንና ፡ አለመሆናቸውን እንወቀው ፡ ተብሎ ፡ በምክር ፡ ተቈረጠ ። ወዲያው ፡ ደጃዝማች ፡

ከበደ ፡ ተሰማ ፡ እንዲላክ ፡ ተደረገ ። ጥቂት ፡ ቄይቶ ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ ኃይሉ ፡ እኔ ፡ የግርማዊነትዎ ፡ ቤት ፡ ጠባቂ ፡ ነኝና ፡ ግርማዊነትዎን ፡ እግዚአብሔር ፡ በደኅና ፡ ከመለሰዎ ፡ ቤትዎን ፡ እንዲረከቡኝ ፡ የሚል ቃልና ፡ አቶሞቢላቸውን ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰንደቅ ፡ ዓላማ ፡ አድር ገው ፡ ላኩ ።

ወዲያውኑ ፡ እኔና ፡ ብሪጋዲዬር ፡ ጀኔራል ፡ ሳንፎርድ ፡ አኳኋኑን ፡ ለማ የትና ፡ ለማረጋገጥ ፡ በልዑል ፡ ራስ ፡ ኃይሉ ፡ አቶሞቢል ፡ ተቀም ጠን ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ማርቆስ ፡ ከተማ ፡ ወጣን ። ግራና ፡ ቀኝ ፡ የተሰ ለፈው ፡ የቢትወደድ ፡ ነጋሽ ፡ ጦር ፡ ግርማዊነታቸው ፡ መስለውት ፡ እየተንበረከከ ፡ መሬት ፡ ይስም ፡ ነበር ። እኛም ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሰን ደቅ ፡ ዓላማችንን ፡ እያውለበለብን ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ቅጥር ፡ ግቢ ገባን ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከልዑል ፡ ራስ ፡ ኃይሉ ፡ ጋራ ፡ ተነጋግረን ፡ ለግርማዊነታቸው ፡ ለማስታወቅ ፡ ተመለስን ። ነገር ፡ ግን ፡ ጥቂት ፡ እን ደሄድን ፡ ግርማዊነታቸው ፡ በጦር ፡ ካሚዎን ፡ ላይ ፡ ሆነው ፡ የጦር ፡ አርበኞቻቸውን ፡ አስከትለው ፡ ሲመጡ ፡ ከመንገድ ፡ ላይ ፡ ተገናኘን ፤ ከአቶሞቢል ፡ ወርደን ፡ ከልዑል ፡ ራስ ፡ ኃይሉ ፡ ጋራ ፡ የተነጋገርነውንና ፡ የኛም ፡ አርበኞች ፡ በየመንገዱ ፡ መሰለፋቸውን ፡ ለግርማዊነታቸው ፡ ካመለከትን ፡ በኋላ ፡ አብረን ፡ ወደ ፡ ከተማው ፡ ተጓዝን ።

ግርማዊነታቸው ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ቅጥር ፡ ግቢ ፡ ሲገቡ ፡ የጐ ዣም ፡ መኳንንትና ፡ ሕዝብ ፡ ከልዑል ፡ ራስ ፡ ኃይሉ ፡ ጋራ ፡ የሰንደቅ ፡ ዓላማውን ፡ መስቀያ ፡ የብረት ፡ ምሰሶ ፡ ከበው ፡ ተሰልፈው ፡ ቆመው ነበርና ፡ ሁሉም ፡ እጅ ፡ ነሥተው ፡ እንኳን ፡ ቸሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ በደ ኅና ፡ ካገርዎ ፡ አገባዎ ፡ ብለው ፡ አጨበጨቡ ።

ግርማዊነታቸው ፡ ወደ ፡ ብረቱ ፡ ምሰሶ ፡ ተጠግተው ፡ እንደዚህ ያለ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡ የሠራላቸውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመስግ ነው ፡ ሰንደቅ ፡ ዓላማቸውን ፡ ሰቀሉ ።

መጋቢት ፡ ፳፯ ፡ ቀን ፡ የኢትዮጵያ ፡ አርበኞችና ፡ የእንግሊዝ ፡ መንግሥት ፡ የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ባንድነት ፡ ተባብረው ፡ አዲስ ፡ አበባን ከጠላት ፡ አስለቀቀው ፡ መግባታቸውን ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ከማታው ፡ በ፫ ፡ ሰዓት ፡ መሳፍንቱንና ፡ መኳንንቱ ፡ የጦር ፡ አለቆቹን ፡ ሰብስበው ፡ አስታወቁ ። የእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ በጠላት ፡ ሻምፓኝ ፡ ተመረቀ ።

ወዲያው ፡ ብፁዕ ፡ አባታችን ፡ አቡነ ፡ በስልዮስ ፡ ተነሥተው ግርማዊ ፡ ሆይ ፡ ባ፲፱፻፳፰ ፡ ዓ ም ፤ መጋቢት ፡ ፳፯ ፡ ቀን ፡ ግርማ ዊነትዎ ፡ ከማይጨው ፡ ጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ አልሄድም ፡ ከዚሁ ፡ እሞ ታለሁ ፡ ብለውን ፡ የተጨነቅንባት ፡ የዛሬ ፡ ቀን ፡ ናት ። ይህች ፡ ቀን፡ የቀቢጸ ፡ ተስፋ ፡ ጨለማ ፡ የሸፈናትና፡ የእግዚአብሔር ፡ ቍጣ ፡ የወ ረደባት ፡ እኛም ፡ አባት ፡ ልጁን ፡ እንደሚቀጣ ፡ በብርቱ ፡ የተመታ ንባት ፡ ቀን ፡ ናት ።

ነገር ፡ ግን ፡ እግዚአብሔር ፡ ዛሬ ፡ በወደቅንባት ፡ ቀን ፡ አን ሥቶ ፡ የቀድሞ ፡ የቸርነቱን ፡ ሥራ ፡ ሠርቶ ፡ መልሶ ፡ በዚሁ ፡ ቀን ፡ ስላቆመን፡ ምን ፡ ልንመልስለት ፡ እንችላለን ፡ ብለው ፡ በሰፊው ፡ በዚያው ፡ የነ በሩትን ፡ የመከራ ፡ ታሪክ ፡ እያሳሰቡ፡ ተናገሩ ።

ግርማዊነታቸውም ፡ ለብፁዕ ፡ አባታችን ፡ ወድቀን ፡ የተነሣንባ ቸውን ፡ ቀኖች ፡ ታሪክ ፡ ጠቅሰው ፡ በተናገሩት ፡ ቃል ፡ አመስግነው፡ ይኸንን ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ሥራ ፡ የሠራላቸውን ፡ እግዚአብሔርን ፡ አመ ሰገኑ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ በሦስተኛው ፡ ቀን ፡ እኔ ፡ የግርማዊነታቸው ፡ እንደራሴ ፡ ሆኜ ፡ ከጥቂት ፡ የጦር ፡ መኰንኖች ፡ ጋራ ፡ ማለዳ ፡ ጎሕ፡ ሲቀድ ፡ ባይሮፕላን ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ በረርን ። ከጧቱ ፡ በሁለት ፡ ሰዓት ፡ ተኩል ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ደረስን ፡ በአየር ፡ ላይ ፡ ሆነን ፡ ከተ ማውን ፡ እንጐበኝ ፡ ዠመር ።

በወንድሞቻችን ፡ የደም ፡ ጐርፍ ፡ የለቀቅናትን ፡ የተወደደች ፡ ከተማችንን ፡ አምራ ፡ አብባ ፡ ከየቤቱ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ቀለም ፡ ጋራ ፡ ዛፉና ፡ አበባውን ፡ በማየት ፡ የደስታና ፡ የናፍቆት ፡ የሰቀቀን ፡ ዕንባ፡ ሳላስበው ፡ ካይኔ ፡ ፈሰሰ ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ከጦሩ ፡ በፊት ፡ ከጐሬ ፡ ስነሣ ፡ ታሞ ፡ መዳን ፡ ወድቆ ፡ መነሣት ፡ እንዳለ ፡ ለማሳሰብ ፡ የተናገርሁት ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ዲስኩር ፡ ትዝ ፡ አለኝ ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ላይ ፡ ከናቴ ፡ ማሕፀን ፡ ወጥቼ፡ በተጣልኩበት ፡ ዘመን ፡ ውስጥ ፡ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ደስ ታን ፡ ስታልፍ ፡ ባይኔ ፡ ያየኋት ፡ ከሁለቱ ፡ አንዲቱ ፡ በልቅሶና ፡ በወንድሞቻችን ፡ የደም ፡ ጐርፍ ፡ ተነቅዬ ፡ በባዕድ ፡ አገር ፡ ተጥዬ፡ የነበርኩ ፡ ሰው ፡ ተመልሼ ፡ ባይሮፕላን ፡ አዲስ ፡ አበባን ፡ መገሥ

መሪያ ፡ ያየሁበት ፡ ቀን ፡ ናት ። የዚችን ፡ ዕለት ፡ የደስታዋን ፡ ትርጉም ፡ የስሜቷን ፡ ምሥጢር ፡ ለመግለጥ ፡ አይቻልም ። ነገር ፡ ግን ፡ የሰው ፡ ደስታው ፡ ቶሎ ፡ ብሎ ፡ በኀዘን ፡ እንዲደፈርስ ፡ የታወቀ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በማግሥቱ ፡ እናቴ ፡ በኔ ፡ ኀዘንና ፡ በፋሺስት ፡ ግፍ ፡ ከስተው ፡ ደክመው ፡ ሳሉ ፡ እኔ ፡ ከግርማዊነታቸው ፡ ጋራ ፡ ከርቱም ፡ መምጣቴ ፡ ስለ ፡ ተወራ ፡ በስውር ፡ በምሥጢር ፡ ለመንገር ፡ ዘመዶቼ ፡ ካዲስ ፡ አበባ ፡ ወደ ፡ በቾ ፡ ጉራንዳ ፡ ስለመጡ ፡ እናቴ ፡ ልጄ ፡ ሞቶ ፡ ሊያረዱኝ ፡ ነው ፡ የመጡት ፡ በማለት ፡ ልብ ፡ የሚያፈርስ ፡ ድንጋጤ ፡ በደከመ ፡ ሰውነታቸው ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ጦር ፡ ስለ ፡ ወጋቸው ፡ ወዲያው ፡ በቅጽበት ፡ ማረፋቸውን ፡ ሰማሁ ።



ከጠላት ፡ በፊት ፡



በጠላት ፡ ጊዜ ፡

ወይዘሮ ፡ አቦነሽ ፡ ተክለ ፡ ማርያም ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ የናቴን ፡ መሞትና ፡ ደግሞ ፡ የናቴን ፡ ሞታ ፡ መነሣት ፡ ባንድ ፡ ቀን ፡ ስላየሁና ፡ ስለሰማሁ ፡ የኔን ፡ እናት ፡ ብቻ ከፍ ፡ ያለውን ፡ ኀዘኔን ፡ ትቼ ፡ የሁላችንም ፡ እናት ፡ ወደሆነችው ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ደስታ ፡ ተመለስሁ ።

ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ አርበኞቻቸውን ፡ ለመቀበል ጥቂት ፡ ቀን ፡ ደብረ ፡ ማርቆስ ፡ ከተቀመጡ ፡ በኋላ ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ በሰላሌ ፡ በኩል ፡ ጕዞ ፡ ዠመሩ ። በዚያው ፡ በኩል ፡ ደብረ ሊባኖስ ፡ ገዳም ፡ ሄደው ፡ የይኩኖ ፡ አምላክን ፡ መንግሥት ፡ በጸሎታቸውና ፡ በድካማቸው ፡ እንዲመለስ ፡ ካደረጉት ፡ ካቡነ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ዐፅም ፡ ላይ ፡ ጸሎት ፡ አድርገው ፡ በፋሺስት ፡ እብሪት ፡

በሰማዕትነት ፡ የሞቱትን ፡ የቅዱሳን ፡ አባቶቻችንንና ፡ ወንድሞቻችንን ፡ ዐፅም ፡ አይተው ፡ ወዳዲስ ፡ አበባ ፡ ጕዟቸውን ፡ ቀጠሉ ።

ግርማዊነታቸው ፡ ከመናገሻ ፡ ከተማቸው ፡ ለመግባት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ሲቀረው ፡ ሹማምንቶቹ ፡ ተሰብስበን ፡ ፕሮግራሙ ፡ እንደዚህ፡ ባለ ፡ አኳኋን ፡ ተቈረጠ ።

፩ኛ ፤ ከንጦጦ ፡ በታች ፡ ዝምሮ ፡ እስከ ፡ ትልቁ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ድረስ ፡ ሕዝቡ ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ እንዲሰለፍ ።

፪ኛ ፤ ከቡር ፡ ራስ ፡ አበበ ፡ አረጋይ ፡ ካርበኞቹ ፡ ጋራ ፡ ግርማዊነታቸውን ፡ ተቀብሎ ፡ እንዲያጅብ ።

፫ኛ ፤ እኔ ፡ ከኢትዮጵያ ፡ መንግሥት ፡ መኳንንቶችና ፡ ከእንግሊዝ ፡ መንግሥት ፡ የጦር ፡ መኰንኖች ፡ ጋራ ፡ ከትልቁ ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ አጠገብ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ሲገቡ ፡ እንድቀበል ፡ ተወሰነ ።

ከዚህ፡ በኋላ ፡ ያገር ፡ መኳንንቶችና ፡ የእንግሊዝ ፡ መንግሥት፡ መኰንኖች ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ተሰልፈው ፡ ቆሙ ። በቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ግንባር ፡ የሱዳን ፡ ወታደሮች ፡ ተሰልፈው ፡ ሰላምታ ፡ ለመስጠት ፡ ይጠባበቁ ፡ ነበር ። ካዲስ ፡ አበባ ፡ እንጦጦ ፡ ከተራራው ፡ እግር ፡ ድረስ ፡ እየተመላለሰ ፡ የካሚዎን ፡ ሆርፓለር ፡ ማንም ፡ የጠላት ፡ ሕዝብ ፡ ወታደርም ፡ ነጋዴም ፡ ቢሆን ፡ ይህ ፡ በዓል ፡ እስካለቀ ፡ ድረስ ፡ ከቤቱ ፡ እንዳይወጣ ፡ እያለ ፡ ይለፍ ፡ ነበር ። በዚህ ፡ ዐዋጅ ፡ ምክንያት ፡ ካርበኞችና ፡ ካገር ፡ ተወላጆች ፡ በቀር በውጭ ፡ የጠላት ፡ ሕዝብ ፡ አይታይም ፡ ነበር ። ከጥቂት ፡ ጊዜ ፡ በኋላ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ ከንጦጦ ፡ ቅድስት ፡ ማርያም ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ገብተው ፡ ይህን ፡ ታምራት ፡ ለሠራላቸው ፡ እግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ ሰጥተው ፡ ብቅ ፡ ብለው ፡ አዲስ ፡ አበባን ፡ አይተው ፡ ይኸንን ፡ ለሠራልን ፡ አምላክ ፡ ምን ፡ እንመልስለት ፡ ይሆን ፡ በማለት ፡ የደስታና ፡ የናፍቆት ፡ ዕንባ ፡ እየተናነቃቸው ፡ በመለከት ፡ ፍርድ ፡ እየተገረሙ ፡ ድል ፡ ሆነው ፡ በወረዱበት ፡ ቍልቍለት ፡ ድል ፡ አድርገው ፡ በሰልፍ፡ ወረዱበት ።

ካዲስ ፡ አበባ ፡ ከተማ ፡ ወሰን ፡ ሲደርሱ ፡ የካሚዎኑ ፡ ሆርፓለር ፡ ግርማዊ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ መጡ ፡ እያለ ፡ እየለፈለፈ ፡ ወደ ፡ ቤተ፡ መንግሥቱ ፡ ሲወርድ ፡ ወዲያው ፡ በአርበኞች፡ ታጅበው ፡ ከትንሹ ፡

ቤተ ፡ መንግሥት ፡ በደረሱ ፡ ጊዜ ፡ የሕዝቡ ፡ እልልታና ፡ ጭብ ጨባ ፡ ተዠመረ ።

በዚያ ፡ ጊዜ ፡ አንዳንዱም ፡ በደስታና ፡ በሰቀቀን ፡ ምክንያት ፡ ያለቅስ ፡ ነበር ። ይልቁንም ፡ በጣም ፡ የሚያስገርመው ፡ የኢትዮጵያ ፡ ተወላጆች ፡ ሁሉ ፡ በፋሺስት ፡ ጊዜ ፡ በገዛ ፡ መሬታቸው ፡ ላይ ፡ እየ ፈሩ ፡ እየተገላመጡ ፡ በመንገድ ፡ ለመሄድ ፡ ይጨነቁ ፡ የነበረውን ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍርድ ፡ ቀኑን ፡ አለዋውጦት ፡ የፋሺስት ፡ የጦር ፡ አለቆችና ፡ የከተማ ፡ ነዋሪዎች ፡ ሁሉ ፡ ከቤታቸው ፡ እንዳይወጡ ፡ በሆርፓለር ፡ ስለ ፡ ተነገሩ ፡ በቤታቸው ፡ እስረኞች ፡ ሆነው ፡ መቀመ ጣቸው ፡ ነው ።

የኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ያለፍራት ፡ በነፃነት ፡ እያጨበጨበ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱን ፡ ሲቀበል ፡ በእውነት ፡ በፈረዳችሁበት ፡ ፍርድ ፡ ይፈረድባችኋል ፡ ያለውን ፡ መለኮታዊ ፡ ቃል ፡ ያሳስብ ፡ ነበር ።

ግርማዊነታቸው ፡ ከቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ደረጃ ፡ አጠገብ ፤ ደር ሰው ፡ ከአቶሞቢል ፡ ሲወርዱ ፡ መኳንንቱም ፡ ሕዝቡም ፡ አጨበጨቡ ። ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ግርማዊነታቸው ፡ በሙዚቃ ፡ የሱዳንን ፡ ወታደሮች ፡ እየዞሩ ፡ ከጐበኙ ፡ ወዲያ ፡ የቤተ ፡ መንግሥቱን ፡ ደረጃ ፡ ወጥ ተው ፡ በግፈኛው ፡ ፋሺስት ፡ ተነቅላ ፡ የወደቀችውን ፡ የኢትዮጵ ያን ፡ ሰንደቅ ፡ ዐላማ ፡ ከሥፍራዋ ፡ መልሰው ፡ ሰቀሉ ። ወዲያው ፡ ወደ ፡ ተሰበሰበው ፡ ሕዝብ ፡ ብቅ ፡ ብለው ፡ «የሰማይ ፡ መላእክት ፡ የምድር ፡ ሠራዊት ፡ ሊያስቡትና ፡ ሊያውቁት ፡ ይቻላቸው ፡ ባል ነበረ ፡ በዚህ ፡ በዛሬ ፡ ቀን ፡ ቸሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ በመካከላችሁ ፡ ለመገኘት ፡ ስላበቃኝ ፡ በሰው ፡ አፍ ፡ የሚነገር ፡ ምስጋና ፡ የሚበቃ ፡ አይደለም» ፡ ብለው ፡ በተናገሩ ፡ ጊዜ ፡ የሕዝቡን ፡ ደስ ታና ፡ የናፍቆት ፡ ሰቀቀን ፡ ያየ ፡ በጣም ፡ ያስገርማል ።

በውነት ፡ ለተመለከተው ፡ ሰው ፡ ባዲስ ፡ አበባና ፡ በሌላ ውም ፡ አገር ፡ በግፍ ፡ የተደበደቡና ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ የወ ደቁ ፡ አርበኞች ፡ ወንድሞቻችን ፡ ሁሉ ፡ ይኸንን ፡ በዓል ፡ ለማ ክበር ፡ ከወደቁበት ፡ ተነሥተው ፡ የመጡ ፡ ይመስል ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በውነት ፡ ባዲስ ፡ አበባ ፡ ብቻ ፡ ከሞት ፡ የተረፉ ፡ ሕዝ ቦች ፡ አይመስሉም ፡ ነበር ።

በዚያ ፡ ጊዜ አቶ ፡ ተማቹ ፡ ከጃንጋብ ፡ የጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ሞት ፡ ተፍቶት ፡ እጅና ፡ እግሩ ፡ ቈስሎ ፡ ፊቱ ፡ በቦምብ ፡ ተቃጥሎ ፡ ምርኵዙን ፡ ይዞ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ የውስጡ ፡ ወደላይ ፡ ተገልብጦ ፡ የከተማ ፡ ነዋሪው ፡ ሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ በየቤቱ ፡ እስረኛ ፡ ሆኖ ፡ የሞት ፡ ጥላ ፡ ወድቆበት ፡ ሲጨነቅ ፡ በማየቱ ፡ እያለቀሰ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ቢገባ ፡ የነፃነታችን ፡



መቱ ፡ ላይ ፡ የመትረየስ ፡ ተኵስ ።

ምልክት ፡ ሰንደቅ ፡ ዐላማችን ፡ ተነቅሎ ፡ የጠላት ፡ ባንዲራ ፡ ሲውለበለብበት ፡ አይቶ ፡ የመረረ ፡ ልቅሶ ፡ እያለቀሰ ፡ ያገሬ ፡ ክብር ፡ የነፃነቴ ፡ ምልክት ፡ ወዴት ፡ አውርደው ፡ ጣሉሽ ፡ በፋሺስት ፡ እግር ፡ ተረገጥሽን ፡ ይኸንን ፡ ውርደት ፡ ሳያይ ፡ የሞተ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ዕድለኛ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ የተናገረው ፡ ትዝ ፡ አለኝ ፡ በፈረዱብንም ፡ ፍርድ ፡ ሲፈረድባቸው ፡ አየን ።

አንባቢ ፡ ሆይ ፡ ያቶ ፡ ተማቹን ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ አልሮ ፡ አልፎ ፡ በውጋዴን ፡ በማይ ፡ ጨው ፡ ታሪክ ፡ ውስጥ ፡ የማስታውሰው ፡ ይህ ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ ባ፲፱፻፳፰ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ጥቅምት ፡ ፳ ፡ ቀን ፡ ከይሉባቦር ፡ የጦር ፡ ሠራዊቱን ፡ እስከ

ትቹ ፡ ስነሣ ፡ የጦሩን ፡ ምግባር ፡ ለማበረታታት ፡ ባንድ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ የቈሰለና ፡ ፊቱ ፡ ሁሉ ፡ በመርዝ ፡ የጠቈረ ፡ የጦር ፡ አለቃና ፡ አንዲት ፡ የሱ ፡ ሚስት ፡ የሆነች ፡ ሴት ፡ ጠላት ፡ አግብታ ፡ እንደ ፡ ቈየችውና ፡ ይኸንን ፡ ታምር ፡ የሆነ ነገር ፡ በማየቱ ፡ ታንቆ ፡ እንደ ፡ ሞተና ፡ ሚስቱም ፡ የተሰቀለው ፡ ባሏ ፡ መሆኑን ፡ ስላወቀች ፡ የባሏንና ፡ ያገሯን ፡ ጠላት ፡ በፋስ ፡ አን ገቱን ፡ ቈርጣ ፡ ከትልቅ ፡ ቋጥኝ ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ ወጥታ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ ኡ ፡ የጕበዝ ፡ ያለኸ ፡ በጠላትኸ ፡ ላይ ፡ እጅኸን ፡ አንሣ ፡ እያለች ፡ በመጮኋ ፡ እሷም ፡ እንደ ፡ ተገደለች ፡ በነዚህ ፡ በሁ ለቱ ፡ የቈራጥነት ፡ መንፈስና ፡ የሚገርም ፡ ነገር ፡ ምክንያት ፡ አገር ፡ አንድ ፡ ብሎ ፡ ተነሥቶ ፡ ነፃነቱን ፡ አስመለሰ ።

ስለዚህ ፡ ታሞ ፡ መዳን ፡ ወድቆ ፡ መነሣት ፡ አለና ፡ ጠላት ፡ ቢያሸንፈን ፡ እንኳ ፡ እንደ ፡ ተኛን ፡ እንደ ፡ ወደቅን ፡ እንዳን ቀር ፡ የሚል ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ዲስኩር ፡ በረዥሙ ፡ ተናግሬ ፡ ነበርና ፤ ይህ ፡ ዲስኩር ፡ ዘወትር ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ላይም ፡ ሆነ ፡ በስደትም ፡ ዋና ፡ አስታዋሽ ፡ ጓደኛዬ ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ በብዙ ሥፍራ ፡ ላይ ፡ ጠቅሼዋለሁ ።

እውነተኛ ፡ ታሪክ ፡ ሲቈይ ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክና ፡ ተረት ፡ ይሆናል ፡ እንጂ ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ያልተደረገ ፡ ነገር ፡ የለም ። ከ፲፱፻፳፰ ፡ ዓ. ም. አንሥቶ ፡ እስከ ፡ ፲፱፻፴፫ ፡ ዓ. ም. ሚያዝያ ፡ ፳፯ ፡ ቀን ፡ ድረስ ፡ የተሠሩት ፡ ተአምራቶች ፡ በጊዜ ፡ ብዛት ፡ እንደ ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ ታሪክ ፡ ለሚመጣው ፡ ትውልድ ፡ እንደሚያስደንቁ ፡ የታወቀ ፡ ነው ። አንባቢ ፡ ሆይ ፡ እንግዴህ ፡ ነገሬን ፡ ሳሳጥር ፡ ታሞ ፡ የተነሣ ፡ እግዜርን ፡ ረሳ ፡ የተባለው ፡ እንዳይደርስብን ፡ የተደረገልንን ፡ ስፊ ፡ ችሮታ ፡ መታሰቢያ ፡ ዘወትር ፡ ካጠገባችን ፡ አንለየው ።

